# ወልታ ጽድቅ

ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከየአንዳሩ የሚያነጻጽር ፣
ጥንተ አብሶን ከነንዙ የሚተነትን፣ ቁንጾላዎችን የሚወድር

2ኛ ዕትም



በአማን ነጸረ

የመጀመሪያ ዕትም ታኅሳስ 2009 ዓ.ም.
ሁለተኛ ዕትም መጋቢት 2009 ዓ.ም.
አዲስ አበባ፣ ኢትዮጵያ

**የጸሐፊው አድራሻ**

ኢ-ጦማር:- beamannetsere@gmail.com
መጽሐፌ ገጽ (Facebook):- በአማን ነጸረ

**ዋና አከፋፋይ**

0912 074 575

**የሽፋን ሥዕል**

ዘሪሁን ገብረ ወልድ

**የሽፋን ሥዕል መግለጫ**

መጽሐፉ ሽፋን ጋሻ ይታያል:: በጋሻው ላይ የተወደረ መጾር መስቀል፣ ቃለ እግዚአብሔርና፣ እመቤታችን ከተወዳጅ ልጇ ጋር ይታያሉ:: ይህም በቤታ ታምነን፣ መስቀል ተመርጉዘን፣ የእመቤታችንን አማላጅነት ተስፋ አድርገን፣ በእነርሱ (በተለይም በእመቤታችን) ክብር ላይ ቂናጽላን የሚሰነዝሩትን የጥርጣሬ ትምህርት በቃለ እግዚአብሔር/ በእውነኛው ቃል/ ጋሻነት ፀንተን በመቆም ለመመከት ያለንን መንፈሳዊ የውጊያ ትጥቅ የሚወክል ነው::

**አኅጽሮት**

- የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ.= የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን
- እ.ኤ.አ. = እንደ ኤሮፓውያን አቈጣጠር
- አ/አዩ. = አዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ
- የኢ/ቃ/ሕ/ቤ/ክ. = የኢትዮጵያ ቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን
- መ/ብ. = መልአከ ብርሃን ወይም መጋቤ ብሉይ
- መ/ሐ. = መጋቤ ሐዲስ
- ሊ/ብ. = ሊቀ ብርሃናት
- ፕ/ር. = ፕሮፌሰር
- ገ. = ገጽ

# ማውጫ

# ምስጋና

ከፈጣሪ በታች...

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን በእምነት፣ በትውፊትና በጥበብ በዓለም የክርስትና ካርታ የራሷ የሆነ የተዋበ ልዩ ቀለም እንዳላት የሚያስረዱ ወጥና የትርጓሜ መጻሕፍትን በራሳችን አገራዊ ዘይቤና ቋንቋ ጽፈውና ደጉሰው ያኖሩልንን ቀደምት አበው ባሰብኩ ቁጥር ከምስጋና ይልቅ ኩራት እየቀደመኝ እቸገራለሁ። ምስጋና ለእነርሱ! በረከታቸውን ለእኛ!

ጽሑፉ ዘመን በወለዳቸው የተለያዩ የመገናኛ ዘዴዎች በእኔና በእኔ ትውልድ እየተነሡ ምንታዌ ላይ የሚጥሉ አሳቦችን በመጠኑ የሚዳስስ ነው። በመሆኑም በማኅበራዊ የመረጃ መረብ የተዛመድኋቸው ጓደኞቼ ያቀጡትን አሳብ አልዘነጋውም። በግብዐትነት ተጠቅሜበታለሁ! ክብር ለፍቁራን ጓደኞቼ!

በጽሑፉ ትርጉማቸውንና አሳባቸውን ለተዋስኳቸው ሁሉ እጅ እነሳለሁ፤ በተለይ ግለሰብ ሳይሆን ተቋም ሆነው ለሚታዩኝ ፕሮፌሰር ጌታቸው ኃይሌ።

የወንድሜ ገብረ እግዚአብሔር ኪዳ ቅን ልቡና፣ ትሑት ሰብእና ባይኖር፥ ይዘቱ ተቃንቶ፣ ጽሑፉ ታርሞ፣ በኮምፒዩተር ተለቅሞ፣ የጎዳግ ማስታወሻውና የቃላት እሰካኩ በተቻለ መጠን ተስተካክሎ (ያልተስተካከለ ካለም የእኔን የስንፍና መጠን ያሳያል እንጂ የእርሱን ትጋትና ቅንነት አያጎድለውም!)፣ ግዘፍ ነስቶ ወደ አንባብያን መድረሱን እንጃ! ባለቤቱ ስንፍናዬን አይቶ እርሱን ላከልኝ!

የዲያቆን ኄኖክ ኃይሌ ስስት አልባ ማበረታቻና በረቂቁ ላይ የሰጠኝ ቀጥተኛ አስተያየት በራሴ ትውልድ ቀናነት እንድኮራ ሳያደርገኝ አልቀረም! 'አዲሱ ትውልድ ካለፈው በተሻለ በቀናነት መደጋገፍን የታደለ ነው' ለሚል እምነቴ ማስረጃዬ ነው - ኄኖክ!

ሲፈርድብኝ ረቂቁን ለዲያቆን ብርሃኑ አድማስ አሳየሁ። እግዚአብሔር ይደለት! አኮሰሰኝ! አሳነሰኝ! ስክንቱ፣ ዝርዝር እይታው፣ ነገሮችን የሚያስተውልበትና የሚገልጽበት እንጻር፣ የንባብ አድማሱ፣ የሚጠቁመኝ መጻሕፍት ዝርዝር ሰውየውን አገዘፉብኝና አነስኩ። እርሱ ትልቅ ሰው ነው!

በአጠቃላይ፡- ለቀደምቶቹ አበው፣ በማኅበራዊ ሚዲያ ላሉ ጓደኞቼ፣ የዚህን ጽሑፍ ረቂቅ በማንበብ ሁለንተናዊ አስተያየትና እገዛ ለሰጡኝ፡- ለገብሬ፣ ለኄኖክና ለብርሃኑ ያለኝ የውዴታ መግለጫ አንድ ነው!

"የኔ ባትሆኑ ይቆጨኝ ነበር!"

# መቅድም

ወልታ "ወልተወ - መከተ፣ ከለለ፣ ጋረደ" ከሚለው ግስ የወጣ ቃል ... "ወልታ - ጋሻ፣ መከታ"። ጽድቅ የሚለው ቃል አወጣጡ "ጸድቀ - እውነት ሆነ፤" ከሚለው ግስ ሲሆን "ጽድቅ - እውነት" ማለት ነው። በተገናኘ ... ጽድቅ - የእውነት ጋሻ።" ይህ ቃላዊ ትርጓሜው ነው፤ በዘይቤ ረገድ ... ሰብቻው ብዙ ትርጓሜ አለው።

ነቢዩ ዳዊት፦ እግዚአብሔርን "ከመ ወልታ ሥሙር ከለልከነ እግዚአ ... እንደ ጋሻ በሞገስ ከለልኸን" ይለዋል (መዝ.5፡12)። ቅዱስ ጳውሎስ ... ሃይማኖትን ወልታ ይለዋል። "ወበእንተዝ ንሥኡ ወልታ እግዚአብሔር ከመ ትክሀሉ ተቃውሞታ ለዕለት እኪት - በክፉው ቀን ለመቃወም ኹሉን ፈጽማችኹ ለመቆም እንድትችሉ የእግዚአብሔርን ዕቃ ጦር ኹሉ አንሡ (ኤፌ.6፡13)።[1] ቅዱስ ያሬድ የጳውሎስን ቃል ለመስቀል ሰጥቶ "ወልታ ጽድቅ ዘአምየማን፣ ወዘአምጸጋም መስቀል ብርሃን - ከቀኝና ከግራ የሚሆን እውነተኛ ጋሻ(ችን) መስቀል ነው" ይላል።[2] አባ ጊዮርጊስ ዘጋሥጫ የእመቤታችንን ጸሎትና በረከት "ይክድነነ ከመ ወልታ ጸሎታ ወበረከታ ጸሎቷና በረከቷ እንደ ጋሻ ይጋርደን" ይላል።[3]

ከላይ የተጠቀሱት ሁሉም እንደ ዘይቤው አገባብ ወልታ ተብለው በተጠቀሱበት አንጻር ሁሉ ወልታነታቸው የእውነት ነው - ወልታ ጽድቅ የእውነት ጋሻ! የጋሻ ጥቅም ጠላት ከወረወረው ጦር፣ ከጣለው ጠጠር ... ሙሉ ለሙሉ መጋረድ፤ ያም ባይሆን ጦርና ጠጠሩ በጋሻው መከታ ... በርዶ ጉዳት እንዳያደርስ ማድረግ ነው። ይህች የእነሱን ክብር የምታነሣ መጽሐፍም ውጥኗ እንደሱ ነው - እንደ ጋሻ። በደቂቀ እስጢፋኖስና በ... አብሶ ዙሪያ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ሊቃውንት መካከል ያሉ መጠነኛ የአተራረክ የአተያይ ልዩነቶችን ተጠቅመው ጦር ከሳሉ በኋላ መልሰው ወደ ራሳቸው የሚወረውሩ ወደረኞቻችንን ለመወደር ትውተረተራለች - ወልታ ጽድቅ!

---

[1] ቅዱስ ጳውሎስ ንባቡና ትርጓሜው፡ገ.292

[2] ድጓ ዘመስቀል፡ ገ.33



በደቂቀ እስጢፋኖስ እንቅስቃሴ ትረካ በብዙኃን የቤተ ክርስቲያኗ ሰዎች ዘንድ እንቅስቃሴውን ምንጊዜም ከውግዘቱ ጋር ብቻ አያይዞ የማየት ዝንባሌ አለ። ከአባ እስጢፋኖስ ህልፈት በኋላ በአፄ ናዖድ ዘመን ስለ ተፈታው ግዝትና ስለ ተፈጸመው እርቅ እምብዛም አይነሣም። በዚህ ላይ ለእንቅስቃሴው የተገኘውን ያክፋልናል ተብሎ የሚታሰብ ስም ሁሉ የማውጣትና ታሪኩን በቸልተኝነት ለሌሎች የመተው ዝንባሌ ይስተዋላል።

ደቂቀ እስጢፋኖስን በማድነቅ መሪዎቹ እንደ ኦርቶዶክሳውያን ቅዱሳን እንዲታዩ በሚፈልጉ የተወሰኑ ጸሐፍትና በእስጢፋኖሳውያን በተመሠረቱ ውስጥ ገዳማት ዘንድ ደግሞ እንቅስቃሴው ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ ህፀፅ እንዳልነበረበትና ቅጣቱ የመነጨውም ከአፄ ዘርዓ ያዕቆብ አምባገነንነት የተነሣ ብቻ ሆኖ እንዲታይ የመፈለግ አዝማሚያ አለ።

ለዘመናት የመንግሥትን ሥልጣን የሚገራ ተቋምና አሠራር ስላላዳበርን አገራችን የጠንካራ መሪዎችና የደካማ ዜጎች አገር ናት። በመሆኑም ከነገሥታቱ ጋር ፊት ለፊት የተላተመ ሰው ሲገኝ በማኅበረሰቡ ውስጥ ያሉት ሕዝባውያን ምሁራን የታሪኩን ፖለቲካዊ ትርጓሜ ያስፋታል፤ ያገንኑታል። ብሒላችንም "አኮ መንክር ለእመ ሞዖ ኃያል ለድኩም፤ መንክርሰ ለእመ ሞዖ ድኩም ለኃያል - ኃይለኛው ደካማውን ቢያሸንፍ አይደንቅም፤ የሚደንቀውስ ደካማው ኃያሉን ካሸነፈው ነው፤" ይላል። የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ በዓለማዊ ምሁራን አካባቢ እንዲህ ዐይነት (የርኅራኄ/ Sympathy?) እይታ ያገኘ ይመስለኛል። ምክንያቱም በተለምዷችን ገዢዎችን መገዳደር ዐላማው ምንም ይሁን ድል ባያስገኝ እንኳ ዝናና "እንዲያ ነው እንጂ! አይ ቆራጥነት! ልክ ልኩን ነገረው!" የሚል ውዳሴ አያሳጣም።

የላይኞቹን አመለካከቶች በ"እንዲህም አለ?!" ስሜት በማለስማማበት ተዐቅቦ እያደረግሁ መቀበል አልከበደኝም። የከበደኝ በእነዚህ አመለካከቶች መካከል ሰርጎ ገብቶ አሳቦችን በመቆንጸል የደቂቀ እስጢፋኖስን ታሪክ የይሁዲ/ የተሐድሶ/ የፕሮቴስታንት ገጽታ የሚያላብስ ትረካ ማየት ነው። እንዲህ ዐይነት አመለካከቶችን ደሞ እንዳላዩ ማለፍ አይሆንልኝምና አሳቡን ለመመከት ያለቺኝን የንባብ መከላከያ አነግባለሁ - ወልታ ጽድቅ!

ጥንተ አብሶን በሚመለከት በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. እንደ ካቶሊካውያንና ምሥራቃውያን ኦርቶዶክሶች ወይም የኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን ጥንቅቅ ብሎ በርእስነት ለብቻው የተብራራ ነባር ጽሑፍ ማግኘት አስቸጋሪ ነው። በቅዱሳት ትውፊታችን ጽንሰ አሳቡ በተለያየ መንገድ ቢገለጽም ለብቻው የተፍታታና የተቀናጀ "ፎርሙላ" ያለው አይመስልም።

ከዚህ የተነሣ መንፈሳውያን ኮሌጆች እየተከፈቱ ምሁራን ለከፍተኛ የሥነ መለኮት ጥናት ወደ ውጭ ሲወጡ በተሳኩበት አገር ያሉ ብሒሎችን ይዘው ይመጡና እዚህ (ለብቻው ባይቀናጅም) በየመጻሕፍቱ ተካትቶና ፀንቶ ከኖረው ብሒል ጋር ለማገጣጠም ሲጣጣሩ ብሒላቸው ከነባሩ ትውፊትና ትርጓሜ ጋር መግጠም ይሣነዋል። ብሒላቸው አልገጥም ሲል ውጭ የተማሩት ከአብነቶቹ ምሁራን ጋር በቃላት እርስ በርስ ጦርነት ይጋጠማሉ። አንዳንድ ጊዜም የቃላት ጦርነቱ ከአሳብ ወደ ስብእና ሲሻገር ይታያል።

እንዲያም ሆኖ በምሁራን ቤተ ክርስቲያን መካከል በጥንተ አብሶ ዙሪያ ያለው የተወሰነ ልዩነት ሁለቱም ክፍሎች ለኦርቶዶክሳዊው ትውፊት ቀናእያን ስለ ሆኑ በቅንነት መነጋገሩ ቢኖር በአንድ ብሒል የመስማማቱ እድል ከብዶ አይታየኝም። ከብዶ የሚታየኝ መፈራረጁና በዚህ ንግግር መካከል የሚነሡ ቃላትን ለግል ዐላማ ቆንጽሎ፣ የአንደኛው ደጋፊ በመምሰል መላውን የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ትውፊት ለማነወር የሚደረግ ውጫዊ መፋጠን ነው። እንዲያ ሲሆን እንማለሁ - ወልታ ጽድቅ!

የወልታ ጽድቅ ዐላማ፦ ወዲህ የተሰነዘሩ፣ ከውስጥም የተነሡ ልብ ከፋይ አሳቦችን ከተቻለ መክቶ፣ ያም ባይሆን አርግቦ በነባሩ ኦርቶዶክሳዊ እምነትና ሥርዓት ተቃኝቶ ከተቻለ ልብን ለማጽናት ነው! እሱ ካልተሳካም ሊቃውንት አርእስቱን እንዳለየ ከማለፍ ትኩረት ሰጥተው እይታቸውን እንዲያጋሩን ለመቀስቀስ ያህል ነው እንጂ አሳብን ከግለሰብ ደባልቆ ለማጥቃት ወይም ነጥብ ለማስቆጠር አይደለም። አይደለም! እንዲያ አለመሆኑን ደጋግሜ በአትሕቶ ርእስ አገልጻለሁ። በዚህ ረገድ ባለማወቅ፣ እንዲያው በ"ዳህፀ ብዕር" (slip of pen) ቃል ካለፈብኝ አስቀድሜ ይቅርታ እጠይቃለሁ።

መልካም ንባብ!

ንሥኡ ወልታ ጽድቅ፤ ከመ ትክሀሉ ተቃውሞታ ለ...

# ክፍል ፩

## ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ አቋም - እናነጻጽር፤ አራቱን እንጻር

"ለማርያም ዘምሩ፣
ለማርያም ዘምሩ፣
መስቀሉ ለወልዳ እንዘ ትጸውሩ።
(ዘምሩ ለማርያም ፣
ዘምሩ ለማርያም ፣
የልጇን መስቀል በመሸከም።)"

መጽሐፈ ዚቅ (1986 ዓ.ም.)፣ ዘታኅሳስ በዓታ፡ገጽ 83

## የደቂቀ እስጢፋኖስና የዘመነኞቻቸው ቁልፍ ሰዎች የታሪክ ሂደቶች

•እ.ኤ.አ 1394 ዓ.ም. (1387 ዓ.ም.) አባ እስጢፋኖስ ተወለደ።

•1391 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1499) አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ተወለደ።

•ከ1406 — 1421 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ.1414-1429) አፄ ይስሐቅ ነገሡ።

•እ.ኤ.አ. 1428 ዓ.ም. (1421 ዓ.ም.) አባ እስጢፋኖስ ከደብረ ቁየጻ ገዳም ተገለሉ።

•ከ1426- 1460 (እ.ኤ.አ. 1434-1468) አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ነገሡ።

•1429 ዓ.ም. በ1391 ዓ.ም የመጡት ግብጻዊው አቡነ በርተሎሜዎስ ዐረፉ።

•እ.ኤ.አ. በ1434 ዓ.ም. (ጥቅምት 5 ቀን 1427 ዓ.ም.) አባ እስጢፋኖስ ለመጀመሪያ ጊዜ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ አደባባይ ቀረበ። ሰንበትን ባለ ማክበሩና ንጉሡን በማቃለሉ ኅዳር 18 ቀን 1427 ዓ.ም. 46 ጊዜ ተገርፎ የካቲት 29 ቀን 1427 ዓ.ም. ወደ በሩ (ጉንዳጉንዶ/ ደብረ ገሪዛን) ተመለሰ።

•እ.ኤ.አ. 1437 ዓ.ም. (1429 ዓ.ም) አባ እስጢፋኖስ በዘርዓ ያዕቆብ አደባባይ ለመጨረሻ ጊዜ ተከራክሮ ሊመለስ ባለመቻሉ ዕጉዕ ግርፋት ተገረፈ።

•1431 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1439) አባ ሚካኤልና አባ ገብርኤል ከግብጽ መጡ።

•1433 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. በ1441) በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን (አፄ ዳዊት በ1392 ዓ.ም. ካጻፈው ወዲህ) ከነ መቅድሙ የተጻፈው ተአምረ ማርያም ተጠናቀቀ። እሑድ ጠዋት ከቅዳሴ ውጭ ተአምረ ማርያም ማንበብ ተጀመረ።

•እ.ኤ.አ. 1444 ዓ.ም. (ታኅሣስ 18 ቀን 1437 ዓ.ም) አባ እስጢፋኖስ ግንቦት 18 ቀን 1436 ዓ.ም. 70 ጊዜ ተገርፎ ኅትር በተጋዘ በስድስተኛው ወር ዐረፈ።

•1442 ዓ.ም (እ.ኤ.አ. 1450 ) የዘመነ ዘርዓ ያዕቆብ ክርክሮች በደብረ ምጥማቅ ጉባኤ ተዘጉ፤ ሁለቱ ሰንበታት እኩል እንዲከበሩ ተወሰነ።

•የካቲት 2 ቀን 1446 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1454) ደቂቀ እስጢፋኖስ ለመስቀልና ለእመቤታችን የጸጋ ስግደት ስላልሰገዱ እፍንጫቸው ተፎነነ፤ምላሳቸው ተቆረጠ።

•ጳጉሜ 3 ቀን 1460 ዓ.ም. አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዐረፈ።

•1460-1471 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ.1468-1478) አፄ በዕደ ማርያም ነገሡ።

•1471-1487 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ.1478 - 1494)አፄ እስክንድር ነገሡ።

•1468 ዓ.ም (እ.ኤ.አ. 1475 ) የደቂቀ እስጢፋኖስ ልዑክ በአባ ዕዝራ እየተመራ ክህነት ለመቀበል ኢየሩሳሌም ሄደ።

•ግንቦት 29 ቀን 1469 ዓ.ም (እ.ኤ.አ. 1476) አባ አበክረዙን ዐረፈ።

•1460-1471 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1468-1478) ገድለ አበው ወአኃው ተጻፈ።

•1474 ዓ.ም. አቡነ ይስሐቅ (በ1501 ዓ.ም. ያረፉት) እና አሳቸውን ተከትለው ጵጵስናውን ይዘው ቆይተው በ1522 ዓ.ም. ያረፉት አቡነ ማርቆስ መጡ።

•1488-1500 (እ.ኤ.አ. 1494-1508) አፄ ናዖድ ነገሡ።

•ጥር 21 ቀን 1492 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1499 ) አባ ዕዝራ ለመስቀልና ለእመቤታችን ሰግዶ ግዝት አስፈታ፤ በአፄ ናዖድ ቤተ መንግሥት ለዘጠኝ ዓመታት ቆየ።

•ነሐሴ 7 ቀን 1500 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1508) አፄ ናዖድ ዐረፈ።

•1501-1532 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1508-1540) አፄ ልብነ ድንግል ነገሡ።

•እ.ኤ.አ. 1520 ዓ.ም. (ነሐሴ 11 ቀን 1512 ዓ.ም.) አባ ዕዝራ ዐረፈ።

•እ.ኤ.አ 1522 ዓ.ም. (መስከረም 3 ቀን 1515 ዓ.ም.) አባ ገብረ መሲሕ ዐረፈ።

•የካቲት 18 ቀን 1519 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ.1527) የግራኝ ጦርነት ተጀመረ። የእስጢፋኖሳውያን እንቅስቃሴም በዚሁ እየከሰመና ከነባሩ ብሒል እየተዋሐደ ሄደ።

# መግቢያ

ዘወትር የሕሊናዬን ሚዛን ኾርቋኹርቆ ከትተው ከሚያንገላቱት አርእስተ ጉዳዮች አንዱ ነው፤ የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ። ታሪካቸው ለሁሉ የተመቸ ሆነ። እናም ሁሉም እንደ መሰኖ ውኃ እየጠለፈ ወደ ራሱ ሁዳድ ሊያስተኛው ይጥራል። እየቦጨቀ በቁንጽላ ይወስድለታል። ማን አለ ያልወሰደለት?! የኢትዮጵያ ፖለቲካ እና ሥልጣኔ ተንታኞች፣ የኢትዮጵያ ታሪክ ጸሐፊዎች፣ የቤተ እስራኤል ጉዳይ አይሁዳውያን ጸሐፍት፣ ከአገር ውስጥ እስከ ዓለም አቀፍ ያሉ ፕሮቴስታንቶች፣ ወዘተ... እንደየራሳቸው አስተሳሰብ እየቆነጸሉ ታሪኩን ለዓለም ናኝተውታል።

ታሪኩ በልዩ ልዩ ጸሐፍት ግላዊ ትርጓሜ አገልግሎት ላይ ሲውል ማየት አታከተኝ። በማኅበራዊ ሚዲያው ዕድል ባገኘሁ ቍጥር ለሕሊናዬ የሚሰማኝን ብናገርም አልወጣልኝም። የመተርጐማት ጽንፍ እና ጽንፍ ረግጦ እንደ ተመች ታሪኩን መቀልመም ደጋግሞ አእምሮዬን አሟታው። ስለዚህ የራሴን አቋም በግልጽ ማንጸባረቂን ሳልዘነጋ ከትረካቸውና ከተራኪዎቹ አቋም በመነሣት የደቂቀ እስጢፋኖስን ታሪክ አረዳድ በዐራት አርእስት ከፍዬ ገፋ አድርጌ ለመዳሰስ እሞክራለሁ። ዐራቱ አንጻር የምላቸው፦

1. መፍቀሬ ዘርዓ ያዕቆብ የሆነው እይታ፣

2. መፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ የሆነው አቋም/ መላምት፣

3. ጉዳዩን ከሃይማኖት ይልቅ ከንጉሣዊ ሥርዓት ፖለቲካ ጋር የሚያዛምደው አቋም/ መላምት፣

4. አይሁዳዊው እና ፕሮቴስታንታዊው እይታ ናቸው - ዐራቱ አንጻሮቼ።

አንዲት (ስርዋጽ) ወሸመጥም ትኖረኛለች፤ መደምደሚያም እንዲሁ።

ከላይ የተገለጹትን አቋሞች ከራሴ አቋም ጋር እያስተሳሰርኩና ንባቤ የፈቀደልኝን ያህል እጄ ላይ ባለው ማስረጃ እያስደገፍኩ ገልጫለሁ። ያም ሆኖ ሐሳቤን በኮምፒዩተር መትቼ ስጨርስ ብዙ ጊዜዬንና ጉልበቴን የነ ፕ/ር ጌታቸው ኃይሌ አቋም ያልኩትን መፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ አቀራረብ በመሞገት ሳላሳልፍ እንዳልቀረሁ ተሰምቶኛል። ምናልባት አሁን አሁን

ለታሪኩ ትርጉሜ መብዛት የእሳቸው ድርሻ ስላየለብኝ ይሆናል።ከዚያ በፊት ግን ስለ መሪ ባለታሪኩቹ ማጠንኛ መረጃ ልስጥ።

## ሀ. ስለ አባ እስጢፋኖስና አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ማንነት አጭር መግለጫ

አባ እስጢፋኖስ በትግራይ ከአክሱም በስተምሥራቅ ስቡሐ በተባለ አካባቢ በግምት እ.ኤ.አ በ1394 ዓ.ም. ከአባቱ ብርሃን መስቀል፣ ከእናቱ ሌሊ ተወለደ። ዓለማዊ ስሙ "ጎድገ እንበሳ"[4] ተባለ። አባቱ ገና በማኅፀን ሳለ ስለ ሞተ[5] ጥቂት ጊዜ እናቱን በእረኛነት ሲያገለግል ቆይቶ ትምህርት ቤት ገባ። በ19 ዓመቱ መነኩሰ። በአባ ሳሙኤል ዘቈየፃ ገዳም ቅዱሳት መጻሕፍትን የመገልበጥና ወጣቶችን የማስተማር ሥራ ተሰጥቶት እሱን ለዓመታት ሲያከናውን ቆይቶ ከግብጻዊው አቡነ በርተሎሜዎስ ቅስና ተቀበለ። ቅስና ተቀበለ በኋላ ባራመደው አቋም የተነሣ ከገዳም እበ ምኔቶች እስከ ነገሥታት ድረስ እየተከራከረ ቅጣት ሲቀበል ቆይቶ ታሕሣሥ 18 ቀን 1444 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ.) በእረማውያን ግዛት ውስጥ ተግዞ ሳለ ዐረፈ፤ ታሕሣሥ 24 ተቀበረ። ባረፈ ጊዜ ዕድሜው 50 ዓመት ይሆናል።[6] የተረፈ ታሪኩ በጽሑፉ ይዳሰሳል።

ከአባ እስጢፋኖስ ጋር እያይዘን በዚህ ጽሑፍ የምናነሣው ዘርዓ ያዕቆብ በ1391 ዓ.ም.[7] ከአባቱ ንጉሥ ዳዊት፣ ከእናቱ እግዚእ ክብራ፣ በፈጠጋር (የዛሬው ምንጃር፣ ሸንኮራና አድዐ አካባቢ[8]) ልዩ ስሙ ጥልቅ በተባለ ቦታ ተወለደ።[9] በአምባ ግሽን በደብረ ዐባይ መንፈሳዊ ትምህርት እየተማረ[10] አደገ። ከአባቱ አፄ ዳዊት ሞት በኋላ ሥልጣን መንግሥቱ በዐራት ወራሾች መካከል ተፈራርቆ በስተመጨረሻ በ1426 ዓ.ም. እርሱ ከአምባ ግሸን ወርዶ[11] ነገሠ። 34 ዓመታት ገዝቶ ጳጉሜ 3 ቀን 1460 ዓ.ም. ዐረፈ።[12] ደብረ ነጕድጓድ[13] ተቀበረ። በኋላ፣ በአፄ ናዖድ ዘመን[14] ራሱ ወደ አሳደሰው ዳጋ (ጣና) እስጢፋኖስ ፈለሰ። ባረፈ ጊዜ ዕድሜው 69 ዓመት ይገመታል። ንጉሡ በመካከለኛው ዘመን ከተነሡ ነገሥታት ሁሉ እጅግ ምሁሩ፣ ዝነኛውና ኃያሉ ሳይሆን አይቀርም። በእምነት ደረጃ ከሙስሊሞች፣ ከደስክ[15]፣ ታፋንት[16]፣ ማቅዋዝ[17]፣ ጉዳሌ[18]ና ዲና[19] የባዕድ አምልኮ ተከታዮች፣

---

[4] ጎድገ እንበሳ=የአንበሳ ቅሪት፣ የአንበሳ ደቦል፣ (አባቱ) 'ብርሃን መስቀል መቼ ሞተ? ይኼው አለ' የሚያሰኝ ተባለ። (አቡነ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዶ፣ ዘአኀተም መምህር ወማህበ ዘጉንዳጕንዶ ደብረ ገሪዛን ገዳም፣ 1996 ዓ.ም.፡ገ.12)

[5] ይህ በአባት ኅልፈት ምክንያት ዕጓለ ማውታ የመሆን አጋጣሚ በገበኞቹ ደቂቀ እስጢፋኖሳውያን አባ አበከረዙንና አባ ዕዝራም ላይ የመከሰቱ ግጥምጥሞሽ ይገርማል!

[6] Taddesse Tamrat, "Some Notes on the Fifteenth Century Stephenite 'Heresy' in the Ethiopian Church,", 22(1966), Addis Ababa University, IES Library p.104 የአፍሪካ ክርስቲያኖች መዝገበ ቃላት - Dictionary of African Christian Biography http://www.dacb.org/stories/ethiopia/estifanos_.html በተሰኘ ድረ ገጽ ያለተጠቀሰ ምንጭ በፕሮቴስታንቶች የተለጠፈ መረጃ የአባ እስጢፋኖስን ልደት በ1380 ዓ.ም.፣ ሀልፈቱን በ1450 ዓ.ም. አድርጎ ዕድሜውን 70 ዓመት ያደርሰዋል።

[7] በዓመተ ምሕረት አጠቃቀስ ረገድ የምጠቀመው ኢትዮጵያዊ አቈጣጠር እንጂ የአውሮፓውያኑ ሲሆን እ.ኤ.አ የሚል ምኅጻር አስቀድማለሁ።

[8] ዳንኤል ክብረት (ዲያቆን)፣ "እሬቱ ኃያላን"፣ 2006፣ አግዮስ ኅትመት፡ገ.228

[9] ዓለሙ ኃይሌ፣ የዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል፣ 2007 ዓ.ም.፡ገ.34

[10] ዮስጢኖስ ለተባለ የደብረ ቢዘን መነኩሴ በእናቱ አማካይነት አደራ ተሰጥቶ፣ አምባ ግሸን ለእስር ሳይገባ በየገዳማቱ እየተዘዋወረ መንፈሳዊ ትምህርት ሲቀስም መኖሩን የሚገልጹም አሉ። (ሥርግው ሀብተ ሥላሴ (ዶ/ር)፣ አማርኛ የቤ/ክ መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 9፣ ገ.158።)

[11] Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, 2014, p.147.

[12] ፐሮፌሰር ጌታቸው፣ ባሕረ ሐሳብ፣ 1993 ዓ.ም.፡ገ.237

[13] ደብረ ነጎድጓድ በግራኝ መሐመድ ከመጥፋቱ በፊት በዛሬው ወሎ /ዶ.ር.ማ/ ወይም ከሐይቅ እስጢፋኖስ በስተምሥራቅ ወደ አውሳ መሄጃ የሚገኝ ዝነኛ የቤማ ማዕከልና ገኛና ደብር ነበር። በ1874 ዓ.ም፣ በአፄ ዮሐንስ ዘመን ተቆፍሮ በከፊል ወጥቶአል። ምናልባት አፄ ዮሐንስ (ያስቆፈሩት አፄ ምኒልክ ናቸው ቢባልም ዘመኑ የአፄ ዮሐንስ ነውና) ከእስልምና አንጻር ወሎ ላይ በተከተሉት ፖሊሲ ይህን እይታት የግራኝ ጥፋቶች ቅሪትን ማየት ያደረገው አስተዋጽኦ ሳይኖር አይቀርም። ደብሩን አሳድሶ (መስርቶ የሚሉም አሉ) ያጸናው አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ነበር። (ገሞሐንስ ገማርያም፣ የኢትዮጵያ እርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ፣ በ16ኛው ክፍለ ዘመን"፣ 1992 ዓ.ም.፡ገ.37-39። የድጓ መቅድም፡ገ.2። የአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫና አባ በጸሎተ ሚካኤል ገድል፣ 2004 ዓ.ም.፡ገ.12።) መጽሐፈ ጤፉት ግን ደብረ ነጎድጓድ የቀድሞ የግሸን ደብረ ከርቤ ሥም መሆኑን ይናገራል። (መጽሐፈ ጤፉት፣ 2006 ዓ.ም.፣ ገ.61 የሚገኝ የኅዳግ ማስታወሻና ገጽ 74።)

[14] Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, p.148.

[15] "ደስክ" ወይም "ደስት" በደስታ ተክለ ወልድ መዝገበ ቃላት ገጽ 394 "ጋኔን፣ ደባት፣ የእንቅልፍ ጋኔን" ተብሎ ተተርጉሟል። ኪዳ ወልድ ክፍሌም በመዝገበ ቃላት መጽሐፋቸው በተለምዶ "ደራሞ ጸራሞ" ከምንለው የእንቅልፍ (የዱከክ፣ የሚጫጫን) ጋኔን ጋር በማዛመድ በገጽ 363 ተመሳሳይ ትርጉም ሰጥተውታል።

[16] በተአምረ ማርያም "ታፋንት"፣ በገድለ አቡው ወአኃው ገጽ "ጠፋንጿ"፣ በ Encyclopedia Aethiopica, Volume 2 ገጽ 131 "ጠፈንት" ተብሎ ቀርቧል። ከጥንቆላ፣ ከዛርና ከቡዳ ጋር የተያያዘ አምልኮ ባእድ ይመስላል። (ደቂቀ እስጢፋኖስ ገ.221፣ ኅዳግ ቁ.417)

[17] ዝኒ ከማሁ።

[18] "ጉዳሌ" የሥርግው ሀብተ ሥላሴ የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት በቅጽ 12፣ ገጽ 183 የዛር አይነት ይለዋል። ፕ/ር ጌታቸው በገጽ 145፣ ኅዳግ ቁ.97 "ኩዳ" ማለት ነው ብለዋል። ይህ ቃል (ጉዳሌ) በነሻም አገው (አዊ) አነጋገር ዛሬ ድረስ "ኩዳ" የሚለውን ቃል ለመግለጽ ጥቅም ላይ ስለሚውልና የገድለ አቡው ወአኃው ጸሐፊው አባ ገብረ ክርስቶስ ትውልዱ ዘእምነገደ ዛግ መሆኑን ገድሉ ስለሚናገር የፕ/ር ግምት ትክክል ይመስላል።

ከአይሁዳውያንና ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር የተያያዘ ኃይል የተቀላቀለበት ታሪክ አለው።[20] በአባ እስጢፋኖስና በዘርዓ ያዕቆብ መካከል የተጀመረውና በወራሾቻቸው መካከልም ከሰባ[21]፣[22] ዓመታት በላይ[23] የቀጠለው ግጭት በዋናነት ለመስቀል፣ ለእመቤታችንና ለንጉሥ መደረግ ስላለበት ስግደት በተነሣ አለመግባባት ዙሪያ ያተኩራል። አለመግባባቱ በሁለቱም ወገኖች አልተካደም። ያለመግባባቱ ምንጭና አተረጓጎም ግን በሁለቱም የተለያየ ምክንያት ይሰጠዋል። ፈተናችን እርሱ ነው፤ ከሁለቱ ተገዳዳሪ ጽሑፎች መካከል እውነትን እንጥሮ ማውጣት! የአንዱ ወገን ብቻ ደጋፊ ሆኖ "የታባቱ፤ ድሮስ...!" እያሉ መቀጠልን ለሚሻ ግን ታሪኩ የተመቻቸ ነው፤ መድከም አያስፈልግም። መርጦ መሰለፍ ብቻ! ወይም ለራስ ሃይማኖታዊ ወይም ፖለቲካዊ፤ አለፍ ካለም ለብሔረሰባዊ አጀንዳ ጠምዝዞ መተርጎም! እንዲያ ባይሆን ግን ምኞቱ ነው። እኔማሴም ታሪኩን በተረዳሁበት መንገድ እነጸጽር

[19] "ዲኖ"= የባር ስም፣ ዋናና ምንዝር (አገልጋይ/ የበታች) አለው።ወደዚህ እምልኮ የሚገባ ሰው (ምዕመን) እግዚአብሔርን መካድ አለበት። ቄስ ከሆነ ቅስናውን፣ መነኩሴ ከሆነ ምንኩስናውን እፍርሶ ዲና ስተባለው ዛር የተሰዋውን ተረፈ መሥዋዕት ተመግቦ አባል ይሆናል። (ሥርግው ሀብተ ሥላሴ፣ የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 11፣ ገ.28።) ከዛ ወልደ ክፍሌ ጅን/ ጂኒ፣ የባሕር ጉሽ፣ የጋኔን በሬ፣ ከባሕር እየወጣ ሳር ይበላል፣ ከየብስ እንስሳትም ይወልዳል ይሉታል። (መጽሐፈ ሰዋስው ወግስ፡ገ.347።)
[20] ተእምረ ማርያም፣ ተስፋ ገብረ ሥላሴ ዘብሔረ ቡልጋ፣1987 ዓ.ም.፣ ገ.11፣ 891
[21] T/C ታደሰ ታምራት ግጭቱ የተካሄደባቸውን ዘመናት 81 ዓመታት ናቸው ይላሉ፤ እንቅስቃሴው ተጀመረ ከተባለበት እ.ኢ.አ. ከ1428 የአፄ ናዖድ ህልፈት (1508 ዓ.ም.) ድረስ በመቁጠር። (Taddessee Tamrat, p.106።) ይሁን እንጂ አባ ዕዝራ ዕርቅ ፈጥሮ አፄ ናዖድ ደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ (ገጽ 310) ስለሚገልጽ እንዚህ ዘጠኝ ዓመታት ከቀደመው መረር የግጭት ዘመን ጋር መደመር ያለባቸው አይመስለኝም። ዘመኑ እ.ኢ.አ. ከ1428-1499 ነው፤
[22] መጀመሪያ አባ ዕዝራን ወደ አፄ ናዖድ፣ በኋላም አባ ይስሐቅን (ዘከስዋ?) ወደ አፄ ልብነ ድንግል በመላክ ዕርቅ የፈጠሩት እስጢፋኖሳዊው አቡነ ገብረ መሲሕ ገድል ከዕርቁ በኋላ ያለውን ሁኔታ "ይበሉሙ ለደቂቁ 'ተፈጸመ ቃለ ነቢይ ዘይቤ እምድኅረ ፹ ዓመት ይገብእ እግዚአብሔር ለጢሮስ' - ልጆቹንም አላቸው 'ከሰባ ዓመትም በኋላ እግዚአብሔር ጢሮስን ይጎበኛታል' ያለው የነቢዩ (ኢሳ.23:17) ቃል ተፈጸመ" ስለሚለው እንቅስቃሴው በዘለቀው ግለት ከሰባ ዓመት እምብዛም የተሻገረ አይመስለኝም። (UNTSC Library Digital Scholarship Unit, Life of our Father Gabre Masih, p.44 digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3A5453#page/40/mode/2up : Visited on Nov.8, 2016)
[23] ከመቶ አስከ መቶ ኀምሳ የሚሉም አሉ። (ጌታቸው ኃይሌ፣ ደቂቀ እስጢፋኖስ፣ 2ኛ ዕትም፣ 2007 ዓ.ም.፣ ቀዳሚ ቃል፣ በሺፈራው በቀለ፡ገ.16።) ሆኖም ከአፄ ናዖድ ሕልፈት በኋላ ብዙም ሳይዘገይ የግራኝ ጥቃት ስለ ተነሣ እንቅስቃሴው በነበረው ግለት የዚህን ያህል ጊዜ ቀይቷል ለማለት የሚቻል አይመስለኝም።



"እውነት ነው" ብዬ ያመንኩበትን መጻፍ ነው። ቀጠልኩ...። ከመቀጠሌ በፊት[24] ግን ተከታዩን መረጃ ላካፍል።

### ሀ. ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላት የተጠቃለለ አጭር መግለጫ

**ገድል የተጻፈላቸው እስጢፋኖሳውያን ዝርዝር፦** UNTSC Library Digital Scholarship Unit በተሰኘ ድረ ገጽ አማካይነት በደቂቀ እስጢፋኖስ ዙሪያ የተጻፉ 18 ገድላትን፣ መልክ መልኮችንና ተአምራትን የማየት እድል አግኝቻለሁ። እነሱም፦ (1) የአባ እስጢፋኖስ ገድል፣ ዜና ሞቱ ለእስጢፋኖስ፣ ተአምረ እስጢፋኖስና መልክዐ እስጢፋኖስ፣ (2) የአባ ይስሐቅ ዘከስዋ፣ (3) የአባ አበከረዙን፣ (4) የአባ ገብረ መሲሕ ቀዳማዊ፣ (5) የአባ ዕዝራ፣ (6) የአባ ሀብተ ሥላሴ ዘከስዋ፣ (7) የአባ ተክለ ነቢያት፣ (8) የአባ ኢሳይያስ፣ (9) የአባ ገብረ ክርስቶስ፣ (10) የአባ ሳሙኤል ዘከስዋ፣ (11) የአባ ተወልደ መድኅን (12) የአባ ኢዮሳብዕ፣ (13) የአባ መዝገበ ሥላሴ በአጠቃላይ የ13ቱም ገድላትና መልኮች፣ (14) ገድለ አባ ሃብተ ሥላሴ ዘደዋር፣ (15) ገድለ ዳግማዊ ገብረ መሲህ፣ (16) ክፉል ገድለ ይስሐቅ ዘዴስእና (17) T/C ጌታቸው የተረጐሙት ገድለ አበው ወእኀው (18) T/C ጌታቸው ከተረጐሙት የቀጠለና የእስጢፋኖሳዊው አባ በርተሎሜዎስ ተጋድሎ ጎላ ብሎ የሚነገርበት ተጨማሪ ገድለ አበው ወእኀው[25] ናቸው።

**የገድላቱ ይዘት፦** (1) ለእመቤታችንና ለመስቀል መስገዱን ባይናገሩም የአባ እስጢፋኖስ ክብር በሁሉም ገድላት ይወሳል። (2) የባለ ገድሎቹን የትውልድ ሐረግና ሥፍራ፣ የወላጅ ሥም፣ የወላጅ የመደብ ጀርባ፣ የትምህርት ቦታ፣ የምንኩስና ገዳምና አባት፣ የክህነት (በብዛት በ12 ዓመት ዲቁና፣ በ15 ዓመት ምንኩስናና ቅስና ይቀበላሉ፤ ሕጻናትን ማመንኰስ ከሚከሰሱባቸው ጉዳዮች አንዱ ነው[26]) አባት ይጠቅሳሉ። (3) የእናቶቻቸው ስም ብዙ ጊዜ ከእመቤታችን ጋር ይያያዛል (ከ16ቱ ነጠላ ባለ ገድሎች የ8ቱ የእናቶቻቸው ስም ማርያም የሚል ዘርፍ ያለው ሲሆን ከዚህ ውስጥም የ4ቱ ወላጅ እናቶች ስም "ንግሥተ ማርያም" ነው።) (4) አባ እስጢፋኖስ፣ ይስሐቅ ዘከስዋ፣ ዕዝራ፣ ኢሳይያስና ተወልደ መድኅን፣ ከአጋሜ/ አጋምያ/ እም ሥዩማን ሰቡሐ ናቸው። ይስሐቅ ዘዴስአ ስሙ አካባቢውን ይገልጻል። አባ አበከረዙን

[24] "ስለ ዲቀቀ እስጢፋኖስ ገድላት" የሚለው ክፍል በመጀመሪያው ዕትም የኅዳግ ማስታወሻ ነበር፤ አሁን በተጨማሪ መረጃ በመጠኑ ተሻሽሎ የዋናው ጽሁፍ አካል ተደርጓል።
[25] "ክፍል ራብዕ፡እመጽሐፈ ገድሎሙ ወስምዖሙ ለአበዊነ ወእኀዊነ ቅዱሳን ለባስያነ መስቀል"
[26] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.199

አክሱም ነው። አቡነ ገብረ መሲሕ፣ መዝገበ ሥላሴ፣ ሀብተ ሥላሴ፣ ሳሙኤል ዘከስዋ፣ ዳግማዊ ገብረ መሲህ ከኢሮብ / እሮብ/ ሕዝበ ሰርክዮ ናቸው። አባ ገብረ ክርስቶስ ዘእምነገደ ዛን (አገው)፣ ልዩ ስሙ ለከማ[28] ነው። አባ ኢዮሳብ ከእምሐራ (እንትት/ የጁ) ነው። የተክለ ነቢያትን አላወቅሁም፤ ቤተሰቡ የንጉሥ የእጋዘን እደን (ንጓወ ደስከን) ባለሥልጣናት ካህናት መሆናቸውና ትውልዱ "መጋዳ"[29] መሆኑ ብቻ ተገልጸዋል። ሃብተ ሥላሴ ዘደዋሮ አለያየሙ የመጣበትን አካባቢ የሚገልጽ ይመስላል። ደዋሮ እርሲ ናት ይባላል። እሱ የተወለደባት ልዩ ቦታ "ዓንጥዩስ" ትሰኛለች። (5) በገድላቱ በየዘመኑ የተነሡ ሃይማኖታዊ ክርክሮች ተመዝግበዋል። በእጌ ሱስንዮስ ዘመን የተነሣውን ክርክር የሳሙኤል ዘከስዋና የዳግማዊ ገብረ መሲህ ገድላት ጠቅሰውታል። እስጢፋኖሳውያን ከተዋሕዶው ወገን ስለነበሩ እያሌ ተዋሕዶዎችን በገዳሞቻቸው ሰውረው ከሱስንዮስ ሰይፍ አትርፈዋል። በዚህ የተነሣ በፋሲል ዘመን ሞገስ አግኝተዋል። ዳግማዊ ገብረ መሲህ ለፋሲል መስቀል ያለበት በትረ መንግሥት መላኩና ንጉሡም ገብረ መሲህ ሲያርፍ በቤተ መንግሥቱ ኃዘን መቀመጡ፣ በየእድባራቱና ገዳማቱ ማለትም በኢሮብ፣...መንበርታ(ዲቦ)፣...ዴስአ፣...እምሐራ ያሉ ካህናትና ደባትር በዳግማዊ ገ/መሲህ ሞት ማልቀሳቸው ተጽፏል። (6) ስለ ፈላሾች (የቀዳማዊ ገብረ መሲሕ[30] እና የይስሐቅ ዘከስዋ ገድላት)፣ ስለ ግራኝና የኦሮሞ እንቅስቃሴ (የአባ ሃ/ሥላሴ ዘደዋሮ፣ የኢሳይያስና የተክለ ነቢያት ገድላት) ያነሳሉ። የኦሮሞ እንቅስቃሴ በገዳሙ ያደረሰው ጫና፣ የወቅቱ ተንቀሳቃሽ ኦሮሞዎች ኢግዙር (ያልተገዘሩ) እና ማዕተብ አልባ መሆን በተጠቀሱት ገድላት ተወስቷል። በግራኝ ዘመን መናንያኑ ገዳማቸውን ለመከላከል ጸሎት ብቻ ሳይሆን ኃይል ጥምር መጠቀማቸውን የሚያሳዩ ምንባባት አሉ። (7) እመቤታችንን በተደጋጋሚ "አክሊለ ምክሕነ" ይሏታል። ገድላቸውን የሚዘጉትም "ጸሎታ ለማርያም..." እያሉ ነው። (8) መዝሙረ ዳዊትን

---

[27] ዘራቸው "እብነ ሮም" ከሚባል ንጉሥ ሲሆን ከሮም መጥተው "ሰሮ'ሸ ሰብ" በተባለ አካባቢ እንደ ሰፈሩ፤ የእብነ ሮም የልጅ ልጅ የሆነ ኢዮባን "ቦሬ" በምትባል ቦታ (1)ሐዘ፣ (2)ኃሪዛ፣ (3)ሰርኩሳ፣ (4)ሬዘ፣ (5)ጎረፍቴ (ገርዓልታ)፣ (6)ተሩዓ፣ (7)ዋኪታ (ደኸናውያን የተባሉ 7 ልጆችን እንደ ወለደ ገድለ አባ መዝገበ ሥላሴ ይናገራል፤ ኢሮብ የሚለውን ቃል ከሮም/ ሮማዊነት ጋር ያይዘዋል።

[28] ምናልባት "ለኮማ ይሆን? አዊ ዞን ውስጥ ለኮማ የሚባል ቦታ ዛሬም አለ።

[29] ቦረና (ኦሮሚያ) አዶላ አካባቢ በዚህ ስም (መጋዳ) ተብሎ የሚጠራ ቦታ አለ።

[30] አባ ገብረ መሲህ ቀዳማዊ ከሰባት እስጢፋኖሳውያን ጋር ተከዜን ተሻግሮ ሰድስቱ በረሀ ሲያልቁ እሱ በአንድ ፈለሳዊ (ፈላሻ) የተረፈበትን ታሪክ የሚገልጸውን ክፍል ስቴቨን ካፕላን በጥናት መጽሔት አውጥቶታል። Steven Kaplan "The Falasha and the Stephanite: An Episode from 'Gadla Gabra Masih'", Bulletin the School of Oriental and African Studies, University of London, Vol.48, No.2 (1985),pp.278-282.



በብዛት ይጠቅሳሉ። በተጨማሪም ሰማንያ አሐዱን፣ መጽሐፈ መነኮሳትን፣ መዝሙራተ ያሬድን፣ መጽሐፈ ፈላስፋን[31]፣ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫን ይጠቅሳሉ። (9) ከአባ እስጢፋኖስ በቀር ቀሪዎቹ ረጅም ዘመን (አባ ገብረ መሲሕ 103፣ ገብረ ክርስቶስ 101፣ ተክለ ነቢያት 93፣ ኢሳይያስ 87፣ አበከረዙን 81፣ መዝገበ ሥላሴ 115 ዓመት/ ዕድሜ) እየኖሩ ነው ያለፉ። (10) ባለ ገድላቱ የዕለተ ሞታቸውን መቃረብ ያውቃሉ። በዚህም መሠረት የሞቱበትን ቀን በቀኑ ከዋለው ዓመታዊ ወይም ወርኃዊ በዓል አቆራኝተው ከነ ሰዓቱ ይመዘግባሉ። ፕ/ር ጌታቸው በአባ ዕዝራ ገድል ገጽ 313፣ ኅዳግ ቁ.172 እስጢፋኖሳውያን በፍልሰታ ለማርያም መሳይዳቸውን አስመልክቶ የእመቤታችን ስም መነሳቱ የሚታሙበትን ለማስተባበል በደራሲው የገባ ማስመሰላቸው በየገድላተ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከሚታየው እመቤታችንን የሚያወድስ ምንባብ የሚስማማ አይመስለኝም። በፍልሰታ በሚቆመው ሰዓታት ውስጥ "ርጉመ ይኩን ዘይረግመኪ ... ፀረኪ ንረግም በምክረ ቃል አሐቲ.." የመሳሰሉ ዜማዎች መኖራቸውና እስጢፋኖሳውያን ፀረ ማርያም መሰኘታቸው ሲታይ በፍልሰታ መሳይዳቸው የሚጠበቅ ነው። የአባ ገብረ መሲህ ገድል ጸሐፊ እንዲያውም በፍልሰታ አፄ ልብነ ድንግል ደርሶላቸው ከማስቆሙ በፊት ገዳማቸው (አፄ ናዖድ ዐልፎ ልብነ ድንግል ሲተካ በነበረው አጭር ጊዜ) ዘርዐ ሠናይ በተባለ መኰንን ትግራይ ሲመዘበርና ሲቃጠል መሳይዳቸው ያሳደረበትን ትካዜ "ወአመ ፲፮ ለነሐሴ ዝ ውእቱ በዓለ ፍልሰታ ለማርያም እንዘ ይብሉ በአፉሆሙ 'ንህነ ፍቁራኒሃ [ለማርያም]' ወኢያከብሩ በዓላ ወይውዕሉ እንዘ ይገብሩ ፈቃዶሙ፤ 'ወእሉሰ ደቂቀ እስጢፋኖስ ኢያከብርዋ' ይብሉ፤ በከመ ባህለ ነቢይ ወንህነሰ ንብል 'እስመ ውእቱ የአምር ኅቡዐተ ልብነ' - በነሐሴ 16[32] ይኸውም የማርያም ስጋ በፈለሰበት (ቀን) በአፋቸው 'የእሷ ወዳጆች ነን' እያሉ ፈቃዳቸውን ሲፈጽሙ ይውላሉ እንጂ በዓሏን አያከብሩም፤ [እንዲያም ሆኖ ደግሞ] 'እኒህ የእስጢፋኖስ ልጆች ግን አያከብሯትም' ይላሉ፤ እኛስ ነቢዩ[33] 'እርሱ ልብ የሰወረውን ያውቃልና' ያለውን እንላለን/ እንጠቅሳለን/።" ይህን በዓለ ፍልሰታን መነሻ ያደረገ ንባብ ለማሳየት ጠቀስኩ እንጂ በገድላቱ በአጠቃላይ ቀናትን በተለዋጭነት በሚውሉባቸው በዐላት መጥራት የእነሱም ልማድ ነው - የሁላችንም ትውፊት! 19 ለማለት "በበዓለ ገብርኤል"፣ 21 ለማለት "በበዓለ ማርያም"፣

---

[31] ለምሳሌ፦ አባ ሳሙኤል ዘከስዋ መጽሐፈ ፈላስፋን ጠቅሶ "አብዝሆ እርምሞ ያለብስ ግርማ - እርምሞን ማዘውተር ግርማን ያላብሳል"፤ "ኢትትቀነዩ ለከርስ ዘእንበለ ለነፍስ - ለነፍስ እንጂ ለከርስ አትገዙ" ይላል። አባ ተወልደ መድኅንም "በከመ ይቤ መጽሐፈ ፈላስፋ 'እስመ ከልብ ይኄይስ እምሰብእ - መጽሐፈ ፈላስፋ እንዳለው፦ ከሰው ውሻ ይሻላል" ይላል።

[32] 1487/8 ዓ.ም.

[33] መዝ.43፡21

24 ለማለት "በበዓለ ተክለ ሃይማኖት"፣...የሚሉባቸው አያሌ ምንባባት አሉ። (11) በስሜኑ ክፍል እሁን ድረስ ከሀናው የልቅሶ ወግ እጅግ በሚመሳሰል መልኩ መሪር ልቅሶና ሙሾ፣ ጸሎተ ፍትሐት፣ ለሙታን በተከታታይ 40 ቀናት ቁርባን ማስቀረብና ተዝካር ማውጣት በእስጢፋኖሳውያን የተለመደ ነው። አባ ምኔት ከሞተ 40 ቀን ካለቀሱለት በኋላ ነው ተተኪውን የሚመርጡት። (12) አባ አበከረዙን፣ አባ ዕዝራ፣ አባ ተወልደ መድኅን፣ ዳግማዊ ገብረ መሲህ በመጻሕፍት ዕውቀታቸው (በሥነ መለኮት) የላቁ ሲሆኑ በእንጻሩ አበው ወእኃው የተባሉት ክፍሎች ዳዊት እየደገሙ በቁፋሮ ከመናር ባለፈ ያን ያህል በመጻሕፍት የሚራቀቁ አይመስሉም።[34] (13) በቦታና ብሔር ረገድ ትግራይ፣ ጸለምት፣ መንበርታ (ዲጠ)፣ ተንቤን፣ ድሙሉ፣ ቀወት፣ ደበአ፣ አምሐራ፣ ጎዣም (ጎግም/ ጎጃም)፣ ሲሬ (ሽሬ)፣ ሲዋ (ሸዋ)፣ አክሱም፣ ሰራዌ/የ (ኤርትራ ውስጥ)፣ ሀገረ ጸው (አፋር)፣ አደል፣ ደዋር፣ ጎትር፣ እሮሞ፣ አገው (ነገደ ዛን)፣ ኢሮብ/ም፣ ቂሰ፣ ቀትት፣ ዶብዐ፣ መጋዳ፣ ወግራት፣ ሰበል (ሸበል)ና በረንታ (ጎጃም)...ተጠቅሰዋል።

የእስጢፋኖሳውያን ባለገድላት የዕረፍት (የሞት) ቀናት፡- እስጢፋኖስ ታኅሣሥ 18፣ ይስሐቅ ዘከስዋ ግንቦት 19፣ ይስሐቅ ዘዴብስ ኅዳር 24፣ ገብረ መሲህ ቀዳማዊ መስከረም 3፣ አበከረዙን ሐምሌ 29፣ ዕዝራ ነሐሴ 11፣ መግዳሊ ሥላሴ ጥቅምት 7፣ ኢሳይያስ መስከረም 17፣ ገብረ ክርስቶስ ዘነገደ የ... መጋቢት 18፣ ሃብተ ሥላሴ ዘደዋሮ ሚያዝያ 17፣ ሃብተ ሥላሴ ዘከስዋ ግንቦት 5፣ ተክለ ኢየሱስ ነሐሴ 23፣ ሳሙኤል ዘከስዋ የካቲት 6፣ ኢዮሳስ ዘአምሐራ ሐምሌ 22፣ ተወልደ መድኅን ግንቦት 23፣ ዳግማዊ ገብረ መሲህ መስከረም 10 በደብረ ገርዜን (ገሪዛን) ጕንዳጕንዶ (ከስዋ) ማርያም ይታሰባሉ።

[34] T/C ጌታቸው ኃይሌ በደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፋቸው ባያትቱትም ቀደም ሲል ያሰ... ሰቀመጡ ነበር። - "The [E]stifanosites were not Theologians. Their writings, except perhaps for the Gadla-Ezra, do not indicate that they were composed by sophisticated scholars. - እስጢፋኖሳውያን የነገረ መለኮት ሊቃውንት አልነበሩም... ምናልባትም ከገድለ ዕዝራ በቀር ጽሑፎቻቸው በረቂቃን ምሁራን መጻፋቸውን አያመለክቱም... Getachew Haile, "The Cause of [E]stifanosites: A Fundamentalist Sect in the Church of Ethiopia", Paideuma, Bd 29(1983),pp.107.

# ምዕራፍ አንድ

## መፍቀሬ ዘርዓ ያዕቆብ የሆነው እይታ

በእኔ ጠባብ ንባብ መሠረት ይህ እይታ በተአምረ ማርያም፣ በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል እና በማኅሌተ ጽጌ ከሰፈሩ ታሪኮችና አገላለጾች ይነግል። የቅርብ ዘመን የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊዎችም ይህንኑ ፈለግ ሲከተሉ ይታያሉ። ከሞላ ጎደል ሁሉም በኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፍያን አበው የተጻፉ ተጠቃሽ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ መጻሕፍት በእጌ ናዖድ አደባባይ ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር የተደረገውን ዕርቅ ወደ ጎን ብለው ቀደም ሲል በተማሉበት ሥዕለ ኅሊና (perception) ብቻ ያቀርቧቸዋል። ያለመግባባቱን መነሻ ከየእንጻሩ አንጻጽረው በስፋት ሳይነግሩን የጥያቄውን ባለቤቶች "አይሁዳውያን፣ ፕሮቴስታንቶች" በማለት በባዕድነት ለመፈረጅ መቻኮል በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመንም ሆነ ከእርሱ በኋላ በተነሡ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊዎች ዘንድ ይስተዋላል። ያለ መግባባቱ በዘርዓ ያዕቆብ ዘመን በተጻፉና በብዙኃን የቅርብ ዘመን የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊዎች የቀረበበትን መንገድ በመጠኑ እንይ።

### 1.1 ያለመግባባቱ መነሻ በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን በተጻፉ መጻሕፍት ሲብራራ

(1.1.1)[35] በተአምረ ማርያም ደቂቀ እስጢፋ[ኖስ] ለእመቤታችንና ለመስቀል መስገድን እምቢ ያሉ "አይሁዳውያን" በመሆናቸው ለክርክር ንጉሡና ሊቃውንቱ ፊት ቀርበው በጉባኤ እንደ ተረቱ፣ በንጉሡና በተሰበሰበው ምእመን ሞት ተፈርዶባቸው በሥልጣነ ክህነት ተወግዘው ከተለዩ በኋላ በድንጋይ ተወግረው እንደ ተገደሉ ተጽፏል።[36] ከዚሁ ጋር ተያይዞ በማኅሌተ ጽጌ ውስጥም "ዘለ ይብል አፈቅረኪ ወኢያፈቅር ተአምረኪ ክርስቲናዊ፣ ኢ

[35] ከእንቀጽ ይልቅ ቁጥር የተጠቀምኩት በሥነ ጽሑፋዊ ምክንያት ሳይሆን ሙያዊ ሕግ በመሆኑ በዚሁ ልማድ ነው። በተጨማሪም የሐንስ እድማሱ የቀኝ ጌታ የፍታሒን ግለ ታሪክ ሲጽፍ ተመሳሳይ አካሄድ ሲከተል ስላየሁት አካሄዴን አልቀየርኩትም።
[36] ተአምረ ማርያም በጌታቸው ኃይሌ (T/C)፣ "ደቂቀ እስጢፋኖስ በሕግ አምላክ"፣ 1996፣ ኮሊጅ ቪል ሚኒሶታ፣ አ.አ.ዩ.ፕሬስ እንደተጠቀሰው ገጽ 53፣ ወሕላይ ዝእግዚአብሔር፣ "ምንኩስና በኢትዮጵያ ዛሬና ትናንትና"፣ 2000 ዓ.ም.፣ ማኅቤቀ ያልተገለጸ፣ ገጽ 47

ክርስቶስን ውእቱ (ዲሎመ) እይሁዳዊ፣ ወስርፀ እስጢፋ ሐሳዊ፣... - እንቺን እወዳለሁ እያለ ተአምርሽን ግን የማይወድ ክርስቲያን፣ ክርስቲያን አይደለም፣ አይሁዳዊና የውሸተኛ እስጢፋ[ኖስ] ተቀጽላ እንጂ..." የሚል ማጎሊታዊ ድርሰት ያለ ሲሆን በዘመነ ጾጌ አሉዶች[37] ድርሰቱ በዜማ ይደረሳል።

አፄ ዳዊትና አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ግማደ መስቀሉን ግሸን ስላስገቡበት ሒደት የሚናገረው መጽሐፈ ጤፉት በገጽ 65 የደቂቀ እስጢፋኖስንና የአፄ ዘርዓ ያዕቆብን ግጭት በሚጠቁም መልኩ "የእመቤታችን የድንግል ማርያምን ክብር የሚቃወሙትንም ከሀገር አስወጡአቸው። ከዚህም በሚገባ የፈረዱባቸው አሉ" ይላል። አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በደረሰው መጽሐፈ ብርሃንም እስጢፋኖሳውያንን ለእመቤታችንና ለመስቀል አንሰግድም ስለ ማለታቸውና ቃላቸውም በሐዋርያት ቃል ስለ መረታቱ "And the evil Stephanites who say 'We do not worship[38] Mary, the twofold virgin and the Holy Cross' say so in the words of their lie....The Aposteles destroy the words of these rebels, the Stephanites ... - እናም ክፉዎች እስጢፋኖሳውያንም በሁለት ወገን ድንግል ለምትሆን ለማርያምና ለቅዱስ መስቀል አንሰግድም ብለው በሐሰተኛ ቃላቸው ተናገሩ። ... ሐዋርያት የኒህን አማጽያን የእስጢፋኖሳውያንን ቃል አፈረሱት (ረቱት)" ተብሎ መጽሐፉን ባጠኑት ምሁራን ተገልጹዋል።[39]

(1.1.2) በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል ይህንኑ ታሪክ እናገኘዋለን። "ከጥቂት ወራት በኋላም ለእመቤታችን ማርያምና ለልጅዋ መስቀል አንሰግድም የሚሉ ደቂቀ እስጢፋ(ኖስ) ተነሡ። በዚህም ምክንያት በንጉሡ ፊት አቀሙአቸው። ንጉሡም የተናገሩበትን ምክንያት ጠየቃቸው።

[37] ከመስከረም 26 - ኅዳር 6 ባሉ ሰድስት፣ አንዳንድ ጊዜም አምስት በሚሆኑ እሑዶች
[38] "Worship of Latreia - የአምልኮ ስግደት" እና "Worship of veneration - የአክብሮት/ የጸጋ/ ስግደት" የተለያዩ ናቸው። ይህኛው "Worship of veneration - የአክብሮት/ የጸጋ/ ስግደት" ነው። አባ እስጢፋኖስ የጸጋ ስግደትን በሥዕሉ ላይ "ርባዔ" እንደ ማድረግ ስለሚቆጥር ሁለቱንም አንድ አድርጎ የሚመለከት ይመስላል። "ርባዔ" ቃሉ በምስጢረ ሥላሴ የታወቀ ነው። አግዚአብሔርን "በአንድነቱ ምንታዌ/ ሁለትነት/፣ በሦስትነቱ 'ርባዔ/ በራትነት/ የሌለበት" ይሉታል የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ መተርጉማን። ስለ ሰጊድ አይነት፣ የቀደሙ አበውን እዮ፣ የአንጾኪያ አብያተ ክርስቲያናት አመለካከት በምዕራፍ ሁለት ተራ ቁጥር 2.4 ስር ተመልከት።
[39] Ephraim Issac, A New Text-Critical Introduction to Mashafa Berhān with a Translation of Book I. Leiden: E. J. Brill, 1973, Netherland, p.70



ከሊቃውንቱም ጋር በመሆን ተከራከራቸው፣ አሸነፋቸውም፣ አሳፈራቸውም። በዚህም ከክፋታቸው አልተመለሱም። ንጉሡ ያን ጊዜ በእነርሱ ላይ ፍርድ ይሰጡ ዘንድ የክርስቲያን ወገኖችን ሁሉ ሰበሰበ። ከኢየሩሳሌም የመጡትንም ክርስቲያን እንግዶች (ነጋዴዎች) ጨምሮ እንዲፈርዱ አዘዘ። እነርሱም በእነርሱ ላይ እስከ ሞት በሚደርሱ በተለያዩ ቅጣቶች እንዲቀጡ ፈረዱባቸው። ከዚያ በኋላ አፍንጫቸውን ፎነኗቸው፣ ምላሶቻቸውንም ቆረጡአቸው፣ በድንጋይም ወገሩአቸው። ይህ የሆነው የካቲት ሁለት ቀን ነው።[40] ከወገሯቸው ከሠላሳ ስምንት ቀን በኋላ መጋቢት ዐሥር ቀን በበዓለ መስቀል ብርሃን[41] ወረደ፣[42] በየሀገሩም ሁሉ እየታየ ብዙ ቀን ቆየ። በዚህም ምክንያት ያችን ቦታ ሁሉ ወደዳት፣ ስሟንም ደብረ ብርሃን[43] አላት።"[44]

[40] የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮች ቅጣቱ የተፈጸመባቸው የካቲት 2 ቀን 1446 ዓ.ም. እንደ ሆነ የሚያሣይ ተጨማሪ መረጃ አለ። (የአማራ ብሔራዊ ክልል፣ ባህል፣ ቱሪዝምና ማስታወቂያ ቢሮ፣ የአማራ ክልል የቱሪስት መስህብ ሃብቶች (አጭር ቅኝት)፣ 1991 ዓ.ም. አርቲስቲክ ማተሚያ ድርጅት።) አባ ትባል የነበረችው ደ/ብርሃን በዚህ ጊዜ የዛሬ ስሟን እንደምትታወቅ አገኘች። አሁን ደብረ ሕገ በደ/ብርሃን የአንድ የከተማዋ ክፍል መጠሪያ ነው።
[41] ስለዚህ ብርሃን ሦስት መላ ምቶች አሉ። (1) በዘርዓ ያዕቆብ በኩል ያሉት መዛግብት የመስቀልንና የእመቤታችንን ክብር ለመግለጽ በተደጋጋሚ የወረዱ ናቸው ይላሉ። (2) እስጢፋኖሳውያን ብርሃኑ እሳትነት ያለው የእግዚአብሔር ቁጣ ነው ይላሉ። (ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.172።) (3) ዘመናውያን ሊቃውንት የሀሌይ ኮሜት (Halley's Comet) ታይታ ሊሆን ይችላል ይላሉ። (Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, p.148.)
[42] በ1987 ዓ.ም. በተስፋ ገብረ ሥላሴ የታተመው ተአምረ ማርያም በተአምር ተራ ቁጥር 298፣ ገጽ 890 ለእመቤታችንና ለመስቀል አልሰግድም የሚል ጽንዕ ክሒደ የሚመሩቸው ከዳተኞች ተነሥተው በተሰበሰበው ሕዝብና በግብጻውያን መልእክተኞች ፊት ቀርበው ስገዱ ቢባሉም ፈቃደኛ ባለመሆናቸው አምላክ ስለ መስቀሉና ስለ እመቤታችን ክብር ኃይሉን እንዲገልጽ ሰባት ቀን ሱባኤ ተገብቶ በሰባተኛው ቀን መጋቢት 10 ቀን ብርሃን መውረዱን ይገልጻል። በዚህኛው ንባብ ብርሃኑ የወረደው አፍና አፍንጫቸው በመፎነን ሳይሆን በተገባው ሱባኤ መሆኑ ተገልጦዋል። አባ እስጢፋኖስ ጾማቸውን "ጾመ ኢልዛቤል" ሲል ቢያስተሐቅረውም እሱን ለመከራከር የቆመ መንክሳት ከሱባኤ በፊት መጾማቸው የተለመደ ይመስላል። (ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.91።)
[43] መስከረም 24 ቀን 2008 ዓ.ም. ደብረ ብርሃን ሥላሴ ለመሳለም ገብቼ (ከዚያ በኋላ በተደጋጋሚ ገብቼዋለሁ) ይህ ብርሃን ወረደበት ተብሎ በትውፊት የሚታወቅ ቦታ በመቅደሱ እና በቤተ ልሔሙ መካከል በተደበቀ ምሥራቅ አቅጣጫ ከ1978 ዓ.ም. ጀምሮ ለማዘክሪያ የሚሆን ምልክት እንደ ተደረገለት አስተውያለሁ። በላዩ ላይም "ይህች ቦታ በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመነ መንግሥት ከኢ.ኦ 424 - ኢ.ኦ 460 ዓ.ም. ባለው ጊዜ ውስጥ መጋቢት 10 ቀን ብርሃን የወረደባት ታሪካዊ ቦታ መሆኗ ይነገርላታል!" የሚል ጽሑፍ በሰሌዳ ተጽፏል። የዕብኑ ሰሌዳ ጽሑፍ የዓመተ ምሕረት መዛባት ያለበት ይመስላል። ዘርዓ ያዕቆብ የነገሡበት ዓመት በእኛ አቆጣጠር ከ1426-1460 ዓ.ም. ሲሆን እ.ኤ.አ ደግሞ ከ1434-1468 ዓ.ም. ስለመሆኑ በብዙ ምንጮች ተጠቅሷል።
[44] ዓለሙ ኃይሌ፣ የንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል ፣2007 ዓ.ም.ሲራክ አሳታሚ፡ገ.35-36

(1.1.3) ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ አማንያን ሦስት የሰጊድ ዐይነቶችን እንዲጠብቁ ስለ ማዘዙ ዜና መዋዕሉ እንደሚከተለው ይተርካል፦ "ዳግመኛም ንጉሣችን እንዲህ ሲል አዘዘ፦ ሁላችሁም የክርስቲያን ወገን የሆናችሁ ሁሉ የእግዚአብሔር ስም በምትጠሩበት ጊዜ በመጀመሪያ 'በገናና መንግሥቱ ፊት እሰግዳለሁ' በሉ፤ ከዚህ በኋላ የእግዚአብሔርን ስም ጥሩ። ሁለተኛም የእመቤታችን የቅድስት ድንግል ማርያምን ስም ለመጥራት በምትፈልጉበት ጊዜ 'ለድንግልናዋ ስግደት ይገባል' በሉ ከዚያ በኋላ ስሟን ጥሩ። ሦስተኛ የእኛን ቃል በሰማችሁ ጊዜ፥ በፊታችን ዘወትር ስትቀርቡ 'ለአብ ለወልድ ለመንፈስ ቅዱስ እንሰግዳለን! ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብን ስለ እንገሠልን' በሉ።"[45]

ድንጋጌው በደቂቀ እስጢፋኖሳውያን ዘንድ የነበረው አሉታዊ አቀባበል በገድለ አበው ወአኃው የሰፈረውን መሪር ንጉሣዊ ቅጣት እንደ ወለደ መገመት ይቻላል። የትእዛዙን መጽሐፋዊነት እናቆየውና ወደ መፍቀርያነ ዘርዓ ያዕቆብ ጸሐፍት እንመለስ።

## 1.2 የዘርዓ ያዕቆብና የደቂቀ እስጢፋ(ኖስ) አለመግባባት በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ታሪክ ጸሐፊዎች እይታ

(1.2.1) በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ዙሪያ ለሚጸፉ ጽሑፎች ሁሉ ቀዳሚ ተጠቃሽ በሆነው የአቡነ ጎርጎርዮስ ካልዕ "የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ" መጽሐፍ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ በነገሠበት [ኢ.ኢ.አ] ከ1434-1468 ዓ.ም. "ደቂቀ እስጢፋ የሚባሉ ለእመቤታችንና ለቅዱስ መስቀል ስግደት አይገባም የሚሉ መናፍቃን እንደተነሡ" ሰፍሯል።[46] ሊቀ ካህናት ክንፈ ገብርኤል አልታዬ በበኩላቸው፦ "ደቂቀ እስጢፋ (የእስጢፋ ተከታዮች) በአለቃቸውና በመምህራቸው በሠርፀ እስጢፋ[47] መሪነት ይሰጡት በነበረው ትምህርት በኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ከፍተኛ ክርክር ተነሥቶ

[45] ዓሰሙ ኃይሉ፥ገ.54

[46] ብፁዕ አቡነ ጎርጎርዮስ (M.A)፤ "የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ"፤1986 ዓ.ም.፤ 2ኛ እትም፤ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት፥ ገ.45

[47] ሊቀ ካህናት "ሠርፀ እስጢፋ" የሚለውን መጠሪያ የወሰዱት ከማኅሌተ ፅጌ ይመስለኛል፡ ሆኖም አጠራሩ ደቂቀ እስጢፋኖስን እንደ ቡድን የሚገልጽ እንጂ የአንድ ሰው ወይም የመሪው መጠሪያ አይደለም። የመሪው ስም አባ እስጢፋኖስ ነውና።



መለያየት ተፈጥሮ ነበር" በማለት በለዘብታ እንሥተውታል።[48] የቤተ ክርስቲያን ታሪክ በመጻፍና በማስተማር በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. በተለይም በቅድስት ሥላሴ መንፈሳዊ ኮሌጅ የክብር[49] ቦታ ያላቸው ሉሌ መላኩ፦ "ደቂቀ እስጢፋ (የእስጢፋኖስ ተከታዮች፡ ልጆች) የተባሉት ለእመቤታችን ለቅድስት ድንግል ማርያም፤ ለቅዱሳንና ለጌታ መስቀል መስገድ አይገባም ብለው የክሕደት ትምህርት ስላስተማሩ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት ተወግዘዋል። በአፄ ዘርዓ ያዕቆብም ትእዛዝ የሞት ቅጣት ተፈጽሞባቸዋል። የእነዚህ ሰዎች ትምህርት ዘግየት ብለው በ16ኛው መቶ ክፍለ ዘመን አውሮፓ ውስጥ ከተነሡት ፕሮቴስታንቶች እምነት ይመሳሰላል። ይኸው ትምህርታቸው የአይሁድ እምንትም ጠባይ አለው" ይላሉ።[50] ሉሌ መላኩ ባነሧቸው የመጨረሻዎቹ ሁለት ዐረፍተ ነገሮች ላይ ተዐቅቦ ይኖረኛል። ኋላ ልመለስበት!

(1.2.2) ከዚሁ ከቅድስት ሥላሴ መንፈሳዊ ኮሌጅ ሳንወጣ መምህር እንዱዓለም ዳግማዊ "ነገረ ድኅነት" በተሰኘ መጽሐፋቸው ፕሮፌሰር ታደሰ ታምራትን ምንጭ አድርገው ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ያሰፈሩትን እንጥቀስ። እሳቸው እንዲህ ይላሉ፦ "በታሪክ እንደምንረዳው [ኢ.ኢ.አ] በ1428 ዓ.ም. የተጀመረው ይህ የእስጢፋኖሳውያን እንቅስቃሴ በብዙዎች ክርስቲያኖች ዘንድ 'ፀረ ማርያም' እና 'ፀረ መስቀል' እንቅስቃሴ በመባል ይታወቅ ነበር። ይልቁንም የእስጢፋኖሳውያን አባት የሆነው አባ እስጢፋኖስ ለዘመናት የቆየውን የቤተ ክርስቲያኒቱን ትውፊታዊ ውርስ እንዲሁም አገር በቀል የሆኑትን ሃይማኖታዊ ጣዕምና ለዛ ያላቸውን ባህልና ልማዶች ይቃወምና ያጣጥል ስለነበር በዘመኑ የነበረችውን የኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያንን አንድነትና ጽናት በእጅጉ ይፈታተን ነበር። ይሁን እንጂ ኦርቶዶክሳዊው ንጉሥ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በወቅቱ ያደረገው ከፍተኛና ያላሰለሰ ጥረት የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያንን ለማዳከምና ብሎም አንድነቷን

[48] አቡነ ገሪማና ሌሎች፤ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን ከልደተ ክርስቶስ እስከ ፳፻ (2000 ዓ.ም.)"፤ 2000 ዓ.ም.፤ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት፥ ገ.22

[49] ነፍስ ኄር ሉሌ መላኩ በኢ/ኦ/ተ/ቤ/ክ. የሥነ መለኮት (ቲዎሎጂ) ኮሌጆች ታሪክ በአቡነ ጳውሎስ ሰኔ 21 ቀን 2000 ዓ.ም. የመጀመሪያው ረዳት ፕሮፌሰርነት መዓርግ የተሰጣቸው ታላቅ፤ ትሁትና ትጉህ መምህር ናቸው (ይህ መጽሐፍ ለ2ኛ ጊዜ ሲታተም ዐርፈዋል)።

[50] ሉሌ መላኩ (ሪ/T/C)፤ "የቤተክርስቲያን ታሪክ"፤ 1986 ዓ.ም.፥ ገ.32

ለመከፋፈል ምቹ ሁኔታን ይፈጥር የነበረውን ይህን ችግር ለመግታት ችሏል፡፡ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በደቂቀ እስጢ(ፋኖስ) ምክንያት የተከሰተውን ይህንን ችግር ለማስወገድና ለመፍታት ካደረጋቸው ብርቱ ጥረቶች መካከል አንዱና ዋነኛው [እ.ኤ.አ][51] በ1450 ዓ.ም.[52] በደብረ ምጥማቅ ያደረገው ሃይማኖታዊ ጉባኤ እንደ ነበር ይነገርለታል፡፡"[53]

(1.2.3) ከኢትዮጵያ ታሪክ ጸሐፊዎች አንዱ የሆነው አለቃ ተክለ ኢየሱስ ዋቅጂራ በመጽሐፉ "... በዚያን ጊዜ [በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን] የሃይማኖት ነገር [ክርክር] ተነሣ፡፡ ሕዝቡም እርስ በእርሱ ተከፋፈለ፡፡ 'የእንግሊዝ ሃይማኖት'[54] ያን ጊዜ ተጀመረ፡፡ የሃይማኖት ጉባኤ በደብረ ብርሃን ሆነ፤" ይላል፡፡[55] ሆኖም የተክሌን መጽሐፍ አርትዖት ሠርተው ያሳተሙት የቆሜ ድንግና ቅኔ ዐዋቂው ዶ/ር ሥርግው ገላው በዚሁ ገጽ ኅዳግ ቍጥር 31 ተክሌ "[የእንግሊዝ ሃይማኖት ያለው] የደቂቀ እስጢፋ ትምህርትን ይመስላል፡፡ የደቂቀ እስጢፋን ትምህርት የፕሮቴስታንት ትምህርት ነው ብሎ ይሁንና ለመደምደም ያስቸግራል፡፡ ደቂቀ እስጢፋ ፕሮቴስታንትነት አልሰበኩም" ሲሉ ተክሌን በኅዳግ "ኀድግ!" ሲሉ ይሞግቱታል፡፡

(1.2.4) እስከ ቅርብ ጊዜ ባለው የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ታሪክ አጻጻፍ ሒደት ዘርዓ ያዕቆብ ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር ባለው ግንኙነት እና በወሰደው ቅጣት፣ እንዲሁም በዘመኑ ስላካሔዳቸው መሪር ቅጣቶች በወቀሳ የጻፈበት ሰው ብዙም አይገኝም፡፡ በዜና መዋዕሉ "ንጉሣችን ዘርዓ ያዕቆብ በደብረ ብርሃን ተቀምጦ ሥርዓተ መንግሥቱን ሁሉ አፀና፤ በዚያም ብዙ ሰዎችን ገደለ፡፡ በእምልኮተ እግዚአብሔር ላይና እግዚአብሔር ቀብቶ ባነገሠው በእርሱ ላይ በደል ባደረሱ ጊዜ የተቀጡ አሉ፡፡ በሞት የተቀጡም አሉ፡፡ ዳግመኛም...

(የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፤ ቅጽ 9፡ገ.160፡፡)

[51] በአፄ 1442 ዓ.ም፡፡ (የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፤ ቅጽ 9፡ገ.160፡፡) ጠቅሰው አባ

[52] ለT/C ጌታቸው ትርጉም ቀዳሚ ቃል የጻፉት T/C ሺፈራው ምንጭ ጠቅሰው አባ እስጢፋኖስ በችሎት የቀረበበትን ጊዜ እ.ኤ.አ. በ1437 ዓ.ም. ስለሚያደርጉትና ሀልፈቱንም እ.ኤ.አ. በ1444 ዓ.ም. መሆኑ ስለሚታወቅ ይህኛው የ1450 ዓ.ም. የደብረ ምጥማቅ ጉባኤ በአባ እስጢፋኖስ ደቀ መዛሙርት (አበው ወአኃው) ላይ የተላለፈውን ፍርድና ዕቀባ ብቻ የሚመለከት ነው፡፡ (ደቂቀ እስጢፋኖስ፤ ቀዳሚ ቃል፡ገ.15፤16-3፡፡ Taddessee Tamrat, 111.፡፡) ሁለቱ ሰንበታት (ቅዳሜና እሁድ) እኩል እንዲከበሩ የተወሰነውም በዚሁ ጊዜ ነው፡፡ ... 1998 ዓ.ም.፡ገ.23

[53] አንዱ ዓለም ዳግማዊ (መምህር)፤ ወላዲተ አምላክ በስንገ ድንግት፤ 1998 ዓ.ም.፡ገ.23

[54] የእንግሊዝ ሃይማኖት=ፕሮቴስታንት፡፡

[55] አለቃ ተክለ ኢየሱስ፡ገ.35



በእግዚአብሔር ፈቃድ የሚኖሩትን፣ የንጉሡንም ትእዛዝ አክብረው የሚኖሩትን ንጉሡ አክብሮና ከፍ አድርጎ የሚያኖራቸው ብዙ ሰዎች አሉ፤"[56] እየተባለ ድርጊቶቹ በፍትሐዊነታቸው ሳይተቹ ታልፈውለታል፡፡ ከዛ ይልቅ የንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን ሥነ ጽሑፍ በማነቃቃት፣ ሥርዓት በመደንገግ፣ "ደስክ" እና "ዲኖ" የተባሉትን የአምልኮ ባዕድ መንገዶች በማጥፋት፣ ጸሎተ ሃይማኖት፣ ዐራቱ ወንጌላት፣ ዐሥርቱ ቃላት፣ ስድስቱ ቃላተ ወንጌል፣ ወልድ ቅድመ ዓለም ያለ እናት መወለዱንና ድኅረ ዓለም ያለ አባት መወለዱን በዐዋጅ መልኩ እንዲሰበክ ማዘዙን፣ እማጺ ሙስሊሞችን በመውጋት፣ አብያተ ክርስቲያናትን በማሳነጽና በማደስ[57]፣ የኢየሩሳሌም ገዳማትን ይዞታ በማጠናከር፣ እ.ኤ.አ. በ1440-1441[58] በፍሎሬንስ ከተማ በተካሔደ የክርስቲያኖች ጉባኤ ወኪል ከኢየሩሳሌም ገዳም አባ ኒቆዲሞስ የተባሉ ኢትዮጵያዊ ስለ መላኩ፣ የግብጻውያን ክርስቲያኖችና የኢየሩሳሌም ተሳላሚ ኢትዮጵያውያን ደኅንነትን ለማረጋገጥ ስለ መድከሙ የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ታሪክ ላይ በጻፉ ሰዎች ሁሉ ተጠቅሶለታል፡፡ በአቡነ ጳውሎስ ጥናት፣ በዜና መዋዕሉ፣ በመቅድመ ተአምረ ማርያም፣ በገ/ዮሐንስ ገ/ማርያም፣ በረዳት ፕ/ር ሉሌ መላኩና በአቡነ ጎርጎርዮስ መጻሕፍት፣ በሥርግው የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት ይኸው ሰፍሯል፡፡ ከግብጻውያን የኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን አባቶች ዘመናዊ ጸሐፍት መካከል የሆኑት አባ ታድሮስ "ቅድስት ማርያም በኦርቶዶክሳዊ ኀሊና - St.Mary in Orthodox Concept" በተሰኘ መጽሐፋቸው ገጽ 115 ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ለክብረ ድንግል ያለውን ቀናኢነት በአድናቆት ዘክረውታል፡፡

(1.2.5) ያም ሆኖ በተሐድሶዎች መጻሕፍትና በፕሮቴስታንት ጸሐፊዎች[59] የነገር ጫፍ በመያዝ ከመወራቱ በቀር ንጉሡ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. በክብር

[56] ዓለሙ ኃይሌ፡ገ.37

[57] ለምሳሌ፡- በጋሞ ጎፋ ጨንቻ ያለችው ብርብር ማርያም፣ ደብረ ሊባኖስ፣ ደብረ ብርሃን ሥላሴ፣ የጎጃሟ ደብረ ወርቅ ማርያምና የባሕር ዳሩ ቅዱስ ጊዮርጊስ፣ ጸድቃኔ ማርያም፣ ግሸን ማርያም፣ አክሱም ጽዮን መጠኑ ቢለያየም ከንጉሡ ጋር የተያያዘ ታሪክ አላቸው (የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 9፡ገ.161)

[58] በአፄ 1433 ዓ.ም፡፡

[59] በ2000 ዓ.ም. በተሐድሶዎች የታተመው "መቅደስ የገቡ መናፍቃን" የተሰኘ መጽሐፍ በመቅድሙ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. እንደ ቅዱስ እንደሚታይና ጽላትም እንደ ተቀረጸለት ያትታል፡፡ ፕሮቴስታንቱ ጸጋአብ በቀለ በ2006 ዓ.ም. ባሳተመው "ተሐድሶ፤ ቅኝ ተገዥዋ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን" የተሰኘ ነቀፋና ትምክሕት የተካነበት መጽሐፉ ፤፤ ላይ ታድግ ያረጀች የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን

ከመነሣት ውጭ የቅድስና መዓርግ የተሰጠው ስለ መሆኑ የጸፈ እርቶዶክሳዊ የለም። ስንክሳሩ በጳጉሜ ሦስት ዕረፍቱን ይጠቅሳል፤ ሆኖም "ቅዱስ" አይለውም። በዚህ ዙሪያ ዲ/ን ዳንኤል ክብረት "ዐራቱ ኃያላን" በተሰኘ የትርጉምና ሐተታ ሥራው በኅዳግ ማስታወሻ መልኩ ሲጽፍ "አንዳንድ ሰዎች ቤተ ክርስቲያን አፄ ዘርዓ ያዕቆብን ቅዱስ እንዳለችው ይገልጣሉ።[60] እኔ እስካሁን ባለኝ መረጃ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ የክብር እንጂ የቅድስና መዓርግ በቤተ ክርስቲያን አልተሰጣቸውም።[61] አብዝቶ በሚከበሩበት በደብረ ብርሃን ሥላሴ ያረፉበት ጳጉሜን 3 በቅዳሴ ይታሰባል እንጂ የዘርዓ ያዕቆብ በዓል ተብሎ አይከበርም። ገድል አልተጻፈላቸውም፤ ጽላት አልተቀረጸላቸውም።

---

ገጽ 117 ተሐድሶዎቹ ያሉትን ጠቅሶ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. በቅድስና ጽላት ተቀርጾለትና ሕንጻ ቤተ ክርስቲያን ታንጾለት እንደሚዘከር አስመስሎ ጽፏል።

የሁለቱ ተመጋጋቢ አስተምህሮ አራማጆች ("ተሐድሶ" ፕሮቴስታንቶች ስለ ኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ነቀፋ መጻፍ ሲፈልጉ የሚጠቀሙበት ጥብዕር ስም") የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ዘርዓ ያዕቆብንም አባ እስጢፋኖስንም ቅዱስ በማለት ተጻራሪ አቋም ታስኬዳለች ለማለት እንዲመቻቸው ነው ዘርዓ ያዕቆብ ቅዱስ ተብሏል የሚሉት። እውነታው ግን፦ (1) በማዕከል ደረጃ ሁለቱም በቅድስና አይታወቁም፤ (2) ለአባ እስጢፋኖስ ጽላት ቀርጸው ቅዱስ ነው የሚሉት ተከታዮቹ በመሠረቷቸው ገዳማት ያሉ ሰዎች ናቸው፤ (3) እነርሱም ቢሆኑ እስከ አሁን በእርሱ ስም የሚጠራ ራሱን የቻለ ቤተ ክርስቲያን አላቋቋሙም፤ ቤተ ክርስቲያኖቻቸው በእመቤታችን ስም ናቸው፤ (4) እስጢፋኖስን እንደ ቅዱስ የሚመለከቱ ገዳማውያን በተግባር ለመስቀልና ለምስለ ፍቁር ወልዳ ሥዕል ስለሚሰግዱ የእርሱን አስተምህሮ በዝርር ሽረዉታል፤ (5) በማዕከላዊው ቤተ ክህነት እንዲልታየ የሚታሰቡትም ለዚህ ነው፤ (6) የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮች ብቻ ሳይሆኑ የተወሰኑ የቅብዐትና የጸጋ ተከታዮችም ሌላውን እስከልተጋፉ ድረስ የማሳደድ አካሄድ ስለሌለ የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮችን ውስን እንቅስቃሴ፤ ከማዕከላዊው ቤተ ክህነት ያልተቋረጠ ግንኙነትና የክህነት መቀበል ሥርዓት በዚህ አንጻር መረዳት ይገባል።

[60] በ1987 ዓ.ም. ተስፋ ገብረ ሥላሴ ባሳተሙት ተአምረ ማርያም መቅድም፤ በ1992 ዓ.ም. መምህር ኪዳነ ማርያም ጌታሁን በጻፉት "ጸረ-ማርያሞች አታወናብዱ" የተሰኘ መጽሐፍ በገጽ 9 እና 11 እንዲሁም ጸ.ት. ገ/ሥላሴ በታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ መጽሐፋቸው (2008 ዓ.ም እትም) ገጽ 20 "ጻድቁ ንጉሠ ነገሥት" የሚል አጠራር ይጠቀማሉ። ሆኖም አጠራሩ የግለሰቦቹ የውዴታ መግለጫ እንጂ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ በይፋ ቅድስና ተሰጥቶት በየወሩ የሚዘከርና ታቦት የተቀረፀለት ቅዱስ ነው ማለት አይደለም።

የክብርና

[61] እንደ ዳንኤል ክብረት ገለጻ ሁለት አይነት የዕውቅና አሰጣጥ መንገድ አለ፤ ክብሩ የቅድስና። የክብር ዕውቅና አንድ ግለሰብ ባበረከተው አስተዋጽኦ የሚሰጥ ሲሆን ክብሩ የሚገኘው በታላላቅ አድባራት በሚገኙ የነገሥታት ተሹዋሚዎች ነው። የክብሩ መገለጫ በመጻሕፍት ኅዳጎችና በሥዕላት ግርጌ ስሙን ሆነ አስተዋጽኦውን በማስፈር ነው። ቅድስና ሲሆን ግን ቅዱሱ ካረፈ በኋላ በሚታይ ራዕይና በሚደረግ ተአምር ከነገሥታት ተጽዕኖ በራቀ ገዳማውያን የሚሰጥ ነው። (አራቱ ኃያላን፡ገ.56።)። ተመሳሳይ አካሄድ (አክብሮትን ለመግለጽ ሥዕል መሳል) በእስጢፋኖሳውያንም ዘንድ እንዳለ በአባ መዝገበ ሥላሴ ገድል መግቢያ በሰገድሉች ጎላ ያሉ ሥዕላት ስር በትንሹ የተሣሉ የግለሰብ ሥዕሎች ይጠቀማሉ። ስለ ቅድስና አሰጣጥ የውጪውንና ያገራችንን ትውፊት በተራ ቁጥር 2.7.5 ተመልከት።



ነገር ግን ባበረከቱት አስተዋጽኦ የክብር ቦታ አላቸው" ይላል።[62] ዲ/ን ዳንኤል እንደ ታዘበው በሦስት መቶ ሠላሳ ሦስት ዓመታት ቆይታ ዐራት ቅዱሳን ነገሥታትና አንዲት ቅድስት ንግሥት ካበረከተው የዛጉዌ ስርወ መንግሥት ጋር ሲነጻጸር በሰምንት መቶ ዓመታት ቆይታው ውስጥ ሁለት ቅዱሳን ነገሥታት (ቀዳማዊ አፄ ቴዎድሮስ እና አፄ ገላውዴዎስን) ብቻ የተገኙበት ሰሎሞናዊ ስርወ መንግሥት በምግባር ረገድ ደካማ የነበረ በመሆኑ እንደ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ያሉ ቀናዒ ሃይማኖተኞች ሳይቀሩ ዕቁባት በማበጀት[63] ለቅድስና ሳይበቁ ቀርተዋል።[64] በቅድስና ረገድ ቀዳማውያን ነገሥታት ይሻላሉ።[65]

(1.2.6) የወቅቱ ሰሎሞናዊ ነገሥታት የምግባር ሕጸጽ እና ቅጥ ያጣ ኢክርስቲያናዊ ቅጣት ሃይማኖታዊ መመዘኛን የማይሻገር[66] መሆኑ እንዳለ ሆኖ ከአንድ በላይ ሚስት የማበጀት ሒደት[67] ከተራ ዝሙት ባለፈ ፖለቲካዊ ትርጉም እንደ ነበረውም ማስተዋል ይገባል። ለምሳሌ፦ የዘርዓ ያዕቆብ እና የገራድ መሐመድ ልጅ የነበረችው ንግሥት እሌኒ ጋብቻ መንሥኤ ከዘርዓ ያዕቆብ ሴሰኝነት ይልቅ ጋብቻው ካነገበው በሙስሊም ግዛቶች የቱርክን ተጽዕኖ በመግታት ሰላም የመግዛት ተልእኮ አንጻርም ሊታይ ይችላል። አንዳንድ ጸሐፊዎች በዚያ መልኩ ተርጉመው ጽፈውታል።[68] ይኼም ሆኖ የደቂቀ እስጢፋኖስ ሰቆቃ "ሃይማኖታዊ ልዩነትን የተመረኮዘ በመሆኑ..." ብለን በአመክንዮ ብናልፈው እንኳ ንጉሡ በሃይማኖት ሕጸጽ የማይታሙትን እንደ አባ ተክለ ሐዋርያት ዓይነት ቅዱስ "ለምን በፈረስ ጉግስ ድኻ ገድልክ ብለው ገሠጹኝ"[69] ሲል በማስገረፍ እግዞ ለጎልፈት በመዳረጉ በሙት ዓመቱ ከመዘከር በቀር ቅድስና ሊያገኝበት የሚችል ዕድል ያለ አይመስልም።

---

[62] አራቱ ኃያላን፡ገ.55

[63] አፄ ዘርዓ ያዕቆብ "ዕሌኒ፤ ፍሬ ማርያምና ጽዮን ሞገሳ" የተሰኙ ሦስት ሚስቶች እንደ ነበሩት መዛግብት ይጠቁማሉ። (Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, 2014, p.149.)

[64] አራቱ ኃያላን፡ ገ.80 እና 238

[65] በዘመነ አክሱም ከአራተኛው እስከ ስድስኛው ክፍለ ዘመን ዐራት ነገሥታትን በቅድስና ተመዝግበዋል። (1) አብርሃ፤ (2) አጽብሓ፤ (3) ካሌብ እና (4)ገብረ መስቀል።

[66] መጽሐፈ ሲኖዶስ ትእዛዝ 25 "ሁለት ከመ ኢመፍትው ያስተጋብኦ ብእሲ ክልኤ አንስቲ ኅቡረ - ሰው (ጎልማሳ) ሁለት ሚስቶችን አንድ ላይ ያኖር ዘንድ እንደማይገባ" በሚል ርእስ ዝርዝር ክልከላ አለው።

[67] በአንድ ፀንቶ ያለፈውን አፄ ልብነ ድንግልን አይጨምርም።

[68] አለባቸው ኪዳሚሶ እና ሳሙኤል ሀንዳሞ፡ የሀዲያ ሕዝብ ታሪክና ባህል ገ.23-31፤ ገብረ የሐንስ ገብረ ማርያም፤ ክርስትና በኢትዮጵያ፡ በ16ኛው ክፍለዘመን፤ 1992 ዓ.ም.፡ገ.18።

[69] ገድለ አቡነ ተክለ ሐዋርያት፤ እጋት መድኃኔዓለም አንድነት ገዳም፡ገ.76

# ምዕራፍ ሁለት

## የመፍቀርያን ደቂቀ እስጢፋኖስ ጸሐፊዎች እይታ

በዚህ ጎራ ውስጥ የመደብኳቸው የገድሉን ተርጓሚ ፕ/ር ጌታቸው ኃይሌ እና በትርጉሙ ተንተርሰው ስለ ኢትዮጵያ የምንኩስና ሥርዓት አስተየ መጽሐፍ የጻፉትን መምህር ካሕሳይ ገብረ እግዚአብሔርን ነው።[1] እስቀድሞ ሁለቱንም እንጋፋ ጸሐፍት ማመስገን የተገባ ነው። በተለይ ብቻቸውን የተቋም ያህል የሚገዘፉት ፕ/ር ጌታቸው ኃይሌ ለተዋጣ ትርጉማቸው፣ ምራቅ ለሚያስውጥ ውብ ቋንቋቸው፣ ሕጸጽ ለሌለበት ጥንቁቅ እርትዖታቸው፣ የገድሉን በስድ የቀረቡ ጥቅሶች ከየምንጮቻቸው የማቆራኘት ግሩም ሥራቸው፣ በቁርኘቱም "ገድል" ማለት በቅጡ ያልተረዱት እንደሚሉት "የመበለት ተረት" ሳይሆን በቅዱስ መጽሐፍ ቃል ያሸበረቀ ጥዑም መዓዛ የሞላበት ሕይወት መተረኪያና የምእመናን ዘሊቋሚ መማማሪያ፣ የታሪክ ማጣቀሻ መሆኑን በማሳየታቸው፣ በመግቢያቸውና በአንዳንድ የኅዳግ ማስታወሻዎቻቸው ላይ ያለኝ መማረር እንዳለ ሆኖ ለጥልቅ ንባባቸውና ለጥንታዊ መዛግብት ስሱነታቸው ያለኝ ክብር ከንብዝ በማውረድ ብቻ ሳይሆን እንደ ግብረ ሕማማት አንባቢ አደግድጎ እጅ በመንሳት የሚገለጽ ነው። ክብር አለኝ፤ ያስንብታቸው። ይህን ካልኩ በኋላ ወደ ቅሬታ ያዘነበለውን፣ በእይታቸው ላይ ያለኝን የልዩነት አሳብ ላንጸባርቅ።

### 2.1. ገለልተኛ ተርጓሚነትና ጸሐፊነት የታለች?!

ፕ/ር ጌታቸው በመግቢያቸው እንዲሁም መምህር ካሕሳይ በመጽሐፋቸው የደቂቀ እስጢፋኖስን እንቅስቃሴ በታላቅ አድናቆት ዘክረውታል። ፕ/ር "ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ 'በሕግ አምላክ'" በተሰኘ ትርጉማቸው ገጽ 23 ገድሉን የማሳተም ዓላማቸው እንቅስቃሴውን "ላላዩ ለማሳየት ነው እንጂ እንቅስቃሴውን ለመደገፍ ወይም ለመቃወም ወይም እንደነሱ የንጉሥ ግርማ የማይፈሩ

[1] በደቂቀ እስጢፋኖስ የተመሠረቱ ገዳማት የሚያንፀባርቁት አቋም መፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ መሆኑ ከመጀመሪያም የሚጠበቅ ነውና እነርሱን እዚህ ማምጣቱ ስላልታየኝ ትቻቸዋለሁ።



መንፈሳዊ አባቶች አልነበሩም ለማለት" እንዳልተረጎሙት ይናገራሉ። ሆኖም ደቂቀ እስጢፋኖስን "የዛሬና የሚራገፍ ነገር ተመልካቾች" ወይም እርጌ ሥርዓት አዳሾች[2] አድርገው በማቅረብ የእንቅስቃሴውን አስመሳክትም "አበባቸውን አረገፉት፤ የእንቅስቃሴውን ነበልባል ውኃ ቸልሰውበት ሳይቀጣጠል ቀረ" እያሉ ገለልተኝነቱን ረስተው ጸጸት ሲበላቸው እናገኛቸዋለን።[3] ክሽፈቱን ከኢዮስጣቴዎሳውያን የቀዳሚት ሰንበትን የማስከበር የተሳካ ተጋድሎ ጋር በማነጻጸር ለመስቀልና ለእመቤታችን ስጊድ መደረግ የለበትም የሚለው እንቅስቃሴ "በድርድር መፈታት ይገባው ነበር፤ ወይም እንዳላየ መታለፍ ነበረበት" የሚል ይዘት ባለው ቃና "ያመለጠ ዕድል" ሲሉ ይቆጫሉ።[4] ያልተስማማኝ አተያያቸው ነው፤ ገለልተኛነታቸውን ጥያቄ ውስጥ የሚከት! ለነገሩ ለንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ያላቸው አመለካከት ትችት ያየለበት ይመስላል። በእርሱ በኩል ያሉትን ምንጮች ሚዛናዊነት ገሸሽ ለማድረግ ከመፋጠናቸውም በላይ "ታሪኩን የሚያንብ ክርስቲያን በዘመኑ ባለ

[2] ከዚህ የፕ/ር ጌታቸው ትርጉም በኋላ ስለ ተሐድሶ የጻፉ ፕሮቴስታንቶችም ሆኑ ተሐድሶዎች "እሕይዎና ተሐድሶ (Revival and Renewal or Reformation) ተደላድሎና ተመቻችቶ በተቀመጠው ሥርዓት (Establishment) ውስጥ የዛሬና የሚራገፍ ነገር የሚያይ የአእምሮ ችሎታና የተፈጥሮ ተሰጥዎ ካላቸው ታላላቅ ሰዎች ዘንድ የሚመጡ እሳቦች ናቸው" የሚለውን በትርጉሙ ገጽ 23 የሰፈረ መግቢያ እጅግ አጨብጨው ራሳቸውን "ፕጊሳቀጅ" የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. "አዘማኞች" አድርገው ያቀርባሉ። እንደ እውነቱ ፕ/ር ጌታቸው በመግቢያቸው የቃሉን አንባብ በዓለማዊነት የተዋጠ ገዳማዊ ሕይወትን ወደ ነበረበት ከመመለስ እንቅስቃሴ ጋር ቢያይዙትም፣ ንጽጽር ሲሠሩ ደቂቀ እስጢፋኖስን ከምንኩስና-አስተሀቃሪው ማርቲን ሉተር አንግስ ማገናኘታቸው ቀዳዮያን እንዲያወናብዱ የሰጠው ዕድል ቀላል አይደለም። ከትርጉማቸው መታተም በኋላ ከገድሉ በላይ የእነርሱ መግቢያ የገነነው፤ ቤተ ክርስቲያኗን የሚዘልፉ፤ ቅስሟና ቅየጣ የሞላባቸው በደቂቀ እስጢፋኖስ ዙሪያ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ የተጻፉ እያሌ የተሐድሶ/ፕሮቴስታንት ጽሑፎች እንዝበዝል።
ግለ ታሪካቸውን በጻፉበት መጽሐፍ ገጽ 58 ከዘውትር ጸሎቶቻቸው አንዱ የመልከአ እየሱስ ግለ መርዋ የሆነው "እምከሉ ይጌይስ በሥላሴክ ተአምኖ፤ ወበወላዲትከ ተማኀፅኖ - በሥላሴህ መታመን፤ በእናትህ (እማጸኛነት) መማጸን ከሁሉም ይበልጣል" የሚል መሆኑን ስለሚገልጹ፤ የአባ ባሕርይን ድርሰት በተረጎሙበት መግቢያ ገጽ 20 እንዲሁ እመቤታችንን "ቅድስት፤ ድንግል፤ ባለ ምሕረት ኪዳኗ" እያሉ በኦርቶዶክሳዊ ቃና ስለሚጠሯት በፕ/ር ጌታቸው የጸና ኦርቶዶክሳዊነትና ልባዊ ተቆርቋሪነት ቅንነት ጥርጣሬ የለኝም። ሆኖም ለእነዚህ ቀናኢን የተሰጠ ትርጉሜ ምንም ምላሽ ማረሚያ አለመስጠታቸው ቅር ያሰኛል። ፕ/ር በተጠቀሰው ግለ ታሪካቸው መግቢያ ገጽ 15 "ስለ ሃይማኖት ብዙ...የሃይማኖት አስተማሪ ሆኜ አይደለም። የምጽፈው ከተጠቀሰ ለታሪክ እንጂ ለሃይማኖት ማስረጃ መሆን የለበትም።" ይላሉ። የደቂቀ እስጢፋኖስ ትርጉማቸው መግቢያና ኅዳግ ግን ከታሪክ ያለፈ ሃይማኖታዊ ብይን ያለው ሆኖ ይታያል።

[3] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.24

[4] ዝኒ ከማሁ፡ገ.35

መኖሩ እግዚአብሔርን ያመሰግናል!" ሲሉ ፍጹም ጸረ ክርስቲያን አስመስለው ያቀረቡበት አጋጣሚም አለ።[5]

መምህር ካሕሳይ በበኩላቸው ንጉሡን በአምላ ገንንትና ስግደት ፈላጊነት፣ በዝሙት፣ በሃይማኖታዊ ህፀፅ፣... ይከስሱታል፤ ጠንካራ ጎኑን ግን ለመናገር ዳተኛ ይሆናሉ።[6] ደቂቀ እስጢፋኖስን ለመከላከል ግን የአንድ ወገን መረጃ ብቻ በመያዝ እስከ ጥግ ይሄዳሉ። እንቅስቃሴው ሲጀመር ስርዓትን እንደማይቀበል በቂ ፍንጮች እያሉ የጅማሬውን የነ አባ እስጢፋኖስ አምልኮ በኋለኞቹ የነ አባ ዕዝራ አሺታ (ስጊድ) ሽፍነው ለማሳለፍ ብርቱ ጥረት ያደርጋሉ። ቅድመ ሥዕል መስገድ የፀና ኦርቶዶክሳዊ ትውፊት መሆኑ እየታወቀ እስጢፋኖሳውያን "ወቅድመ ሥዕላ ስግዱ" ማለትን ያልተቀበሉት በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ የመጣ አዲስ ብሒል ስለሆነ ብቻ አስመስሎ ማለፍ እንደ ኦርቶዶክሳዊ ተገቢ ሆኖ አይታየኝም። መምህር ካሕሳይ እንዲያ የማድረግ አዝማሚያ ይታይባቸዋል።[7]

በአጠቃላይ የሁለቱን ታላላቅ ሰዎች እይታ በአንድ ርእስ ስር ለማጠቃለል ብሞክርም በእይታቸው ያለኝ ግንዛቤ መጠኛ ልዩነት እንዳለው መግለጽ እፈልጋለሁ። T/C ለደቂቀ እስጢፋኖስ ያላቸው ውዴታ ለነጻ አስተሳሰብ (በእሳቸው አነጋገር "የአእምሮ እንቅስቃሴ") ከመጓጓት ነው። በዚህ የተነሣ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ላይ እንደሚያደርጉት በእነርሱ አስተምህሮ ላይ ምንም ትችት ሳያቀርቡ የእንቅስቃሴውን ጅማሮ (መነሻ) ለማጉላት ብዙ ርቀት ይሄዳሉ። በአንጻሩ መምህር ካሕሳይ ደቂቀ እስጢፋኖስን ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ ባለ እንቅስቃሴያቸው እንከን አልባ "ቅዱሳን" ያደርጉና አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ላይ ሉሉ የሚሏቸውን ድክመቶች ከርእሱ የማይያያዘውን ሳይቀር ያገዝፏቸዋል።[8] ያን ጊዜ ጎሊናችን 'ገለልተኛ ተርጓሚነትና ፀሐፊነት የታለች?' የሚል ጥያቄ ያመላልሳል።

---

[5] ጌታቸው ኃይሌ፣ባሕረ ሐሳብ፣ገ.236

[6] ካሕሳይ፣ገ.65-67

[7] ዝኒ ከማሁ፣ ገ.53

[8] T/C ሺፈራው እንደሚገልጹት አለቃ ግርማ ኢልያስ፣ መምህር ካሕሳይ የዘ... እግዚአብሔርና በደቂቀ እስጢፋኖስ የተመሠረቱ ገዳማት ነዋሪ አባቶች የደብረ ... ጉንዳጉንደን ክብርና ሞገስ ከማስጠበቅ [ምናልባት የአካባቢያዊነት - regionalism - መንፈስ...



## 2.2. ሉተርና አባ እስጢፋኖስ ምንና ምን ናቸው?!

የT/C ጌታቸው ለቀንጸላ በር የሚከፍት ንባብ በገጽ 24 ላይ "ደቂቀ እስጢፋኖስ የተነሡት በዐጼ ይስሐቅ (1406-1421 ዓ.ም.) ዘመን ሲሆን ማርቲን ሉተር ጀርመን ላይ 'ተመሳሳይ አሳብ' ይዞ ከመነሣቱ ከሠላሳ ዓመት ገደም በፊት ነው" በሚል ሰፍሯል። የደቂቀ እስጢፋኖስንና የማርቲን ሉተርን አሳብ "ተመሳሳይ" ብለው በመግቢያቸው ካወጁ በኋላ በጎዳግ ማስታወሻዎቻቸው የደቂቀ እስጢፋኖሳውያንን ሐሳቦች እየለጠጡ ከሉተር ሐሳቦች ጋር ለማዛመድ በእያሌው የጣሩ መስሎ ይሰማኛል። የሉተር "Sola fide - faith alone - መዳን በእምነት ብቻ" የሚል የፕሮቴስታንት መሰያ መርሕ ከደቂቀ እስጢፋኖሳውያን ገዳማዊ ጾምና የታከለበት ጥብቅ የምግባር ሥርዓት ጋር ያለው ተቃርኖ፣ የሉተር "Sola scriptura - Scripture alone - 66ቱ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል መፈክር ለማገያ አሉሱን ብቻ ሳይሆን ልዩ ልዩ አዋልድ መጻሕፍትንና መንፈሳዊ ትውፊቶችን ሲቀበሉ ከምናያቸው ደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር እንደማይስማማ፣ "All believers are priests - አማኝ ሁሉ ካህን ነው" በሚል ዓመፃ ከገዳም እምፆ የወጣው "መነኩሴ" (ሉተር) ክህነት ለመቀበል የሲናን በረሃ አቋርጠው እስከ ግብጽና ኢየሩሳሌም ድረስ ሲንከራተቱ ከነበሩት ከደቂቀ እስጢፋኖሳውያኑ እነ አባ ዕዝራ ጋር በT/C ጌታቸው ትርጉም ሲነጻጸር ማየት ለኦርቶዶክሳዊ ኅሊና ይከብዳል። ይህ የተለጠጠ የT/C 'መላምታዊ' አቀራረብ ከላይ ካቀረብኳቸው የመፍቀርያነ ዘርዓ ያዕቆብ ያለ እግባብ ደቂቀ እስጢፋኖስን በይሁዲነትና በፕሮቴስታንትነት የመፈረጅ አካሔድ ጋር ተዳምሮ ታሪኩን ሳልተገባ ቀንጸላ ዳርጎታል ብዬም አምናለሁ። በቤተ እስራኤላውያን (ይሁዲዎች/ ፈላሾች) እና በፕሮቴስታንት ፀሐፊዎች እይታ ላይ ሰብቻ እንመለሳለን። ከዚያ በፊት ደቂቀ እስጢፋኖስ በመነሻቸው ባራመዱት አቋም ተወግዘው ነበር ወይስ አልተወገዙም? የሚለውን ጭብጥ ለማጥራት መሞከር የተገባ ነው።

## 2.3. እውን ደቂቀ እስጢፋኖስ ተወግዘው እያውቁም?!

---

አንጻር አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቹ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ቅዱሳን ተርታ እንዲታዩ መጣራቸው ሊያስገርመን አይገባም። ደቂቀ እስጢፋኖስ፣ ቀዋሚ ቃል፣ ገ.16-5።

ፕ/ር ጌታቸው በገጽ 25፣ መ/ር ካሕሳይ በገጽ 52 ደቂቀ እስጢፋኖስ መንፈሳዊ ሥልጣን ባላቸው ጳጳሳት እንዳልተወገዙና "ተወግዘዋል" የሚለው ዘርዓ ያዕቆብ ያስጻፈው (ያስተረጎመው) ተአምረ ማርያም ብቻ መሆኑን ያመለክታሉ። የውግዘቱ ታሪክ ተአምረ ማርያም ላይ ሲሆን "በተአምረ የዘርዓ ያዕቆብ እጅ ስላለበት ተአማኒነት የለውም፣ እነርሱ የጻፉት ግን በተአማኒነቱ ጥያቄ ሊነሣበት አይገባም" ይመስላል አቀራረባቸው። ፕ/ር በመግቢያቸው ገጽ 29 በዘርዓ ያዕቆብ በኩል ያለውን መረጃ "እሱ ስላልሰገዱልኝ ተጣልቷቸው ብሎ ይጽፋል ተብሎ አይገመትም፣ አይጠበቅምም" ብለው ያሳንሱታል። ሆኖም በተመሳይ ሚዛን ሲታይ እነሱም "ለእመቤታችንና ለመስቀል ስላልሰገድን የተወግዝን፣ ውጉዛን ነበርን" ሊሉ እንደማይችሉ 'ሳይገምቱና ሳይጠብቁ' ይቀራሉ። እዚህ ላይ መፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ መሆን የሚዛናዊ ዓይን እይታ ሳትጋርድ አልቀረችም ብዬ እጠራጠራለሁ። እኔ "ውግዘት ነበረ" ባይ ነኝ። መከራከሪያዬን ላስመዝግብ፦

(2.3.1) ገድሎቻቸውን ያነበበ ሁሉ ደቂቀ እስጢፋኖስ ለእመቤታችን ያላቸውን ፍቅርና አክብሮት እንዲሁም በአማላጅነቷ ማመናቸውን ለማረጋገጥ አይቸግረውም። ለእመቤታችንና ለመስቀል የጸጋ ስግደት ማድረግን በሚመለከት ግን መጀመሪያ አካባቢ በራሳቸው ተነሣሽነት ሲያከናውኑት ማግኘት ከባድ ሲሆን በተለይ በገድለ እስጢፋኖስ ውስጥ አንድም ቦታ ለእመቤታችንና ለመስቀል ሲሰግዱ አናገኛቸውም።[10] ስለ መስገዳቸው ማስረጃ

---

[9] በገድሉ ገጽ 102 እንደተመለከተው ጸሐፊው አባ ገብረ ክርስቶስ የተባለ ደቂቀ እስጢፋኖሳዊ መነኮስ ነው።

[10] እዚህ ላይ ተጋኖ እንደሚነገረው "የአባ እስጢፋኖስ አስተምህሮ ከዛሬ ዘመን ፕሮቴስታንቶችና ከይሁዲዎች ጋር ይመሳሰል ነበር" ለማለት ባይቻልም፣ ከነባሩና ከዛሬው ኦርቶዶክሳዊ አስተምህሮ ጋር በምልዐት ይጣጣማል ማለት ግን አይደለም። በገድለ አበው ወአኃውና በገድለ ዕዝራ እንደምናነበው በሰጊድ ረገድ አስተምህሮው ከራሱ ልጆች አቋም ጋር አይገጥምም። ምክንያቱም፦ (1) በገድሉ ውስጥ በአንድም ቦታ ለእመቤታችንና ለመስቀል ሲሰግድ አይታይም። እንቅስቃሴው ሲጀመር በተጻፉ ቀዳሚ መዛግብት ያሉ ጽሑፎች ለእመቤታችን መስገዳቸውን አያሳዩም። (Taddesse Tamrat, p.111, foot note.1.) (2) ጓደኛ እነ አባ ዕዝራ በአደባባይ "ለመስቀልና ለማርያም መምህራኖቻችንም ይሰግዳሉ" ቢሉም ሁለ በአልሰግድም ባይነቱ የሚታማውን፣ የእርሱን ስም ለይተው "አባ እስጢፋኖስ ይሰግድ ነበር" ለማለት አይደፍሩም። በጉንዳጉንዴ ገዳም የታተመው ገድልም በመግቢያውና በመቅድሙ አባ እስጢፋኖስ ለመስቀልና ለእመቤታችን ስላለመስገዱ የሚቀርበውን ወቀሳ አላስተባበለም፤ ጥያቄውን ሳያነሣ የአፄ ዘርዓ ያዕቆብን ቅጣት መሪርነት በማጉላት ብቻ ሸፍኖ ነው ያለፈው። (3) በንጉሡም ሆነ በሊቃውንቱ ዘንድ "መምህራችሁን ስደቡ" (በሌላ አነጋገር አውግዙ)



ከሌለ ስለ መወገዛቸው የሐሰና ግምት ለመውሰድ የሕግ መርሕ ይፈቅድልናል። ምክንያቱም የጊዜው ትውፊትና ሕግ ለማርያምና ለመስቀል አለመስገድን ኃጢአትም ወንጀልም ስለሚያደርግ!

(2.3.2) በገጽ 146 ለቅድስት ማርያም ስገዱ ሲባሉ "ለልጇ ስንሰግድ እዚያው እናገኛታለን" የሚል ከቅን ልቡና የራቀ የሚመስል መልስ ሲሰጡ እና በገጽ

---

የሚለው እስጥ አገባ እስከ መጨረሻው ተጥጧል፤ እንዲሰደብ የሚፈለገው ደግሞ አባ እስጢፋኖስ ብቻ ተለይቶ ነው። (4) እነ አባ ዕዝራ ወደ ነገሩ ብሔል የተቀላቀሉ የቀደመው የአባ እስጢፋኖስ አቋም በተግባር በተደረገ ሰጊድ ተንቅፎ ነው። (5) ግጭቱ ሲጀምር የተነሣው ተደጋግሞ እንደሚነገረው ከካህናተ ደብተራ ሳይሆን ከገዳማውያን ጋር - እዚያው ገዳም ውስጥ - ነበር። (6) በአፄ ይስሐቅ አደባባይ ስላለመወገዙ ተደጋግሞ ይነገራል፤ ይሁን እንጂ በይስሐቅ አደባባይ ከቀረቡበት ክሶች አንዱ ግልቡ ውስጥ የተደበቀች ሌላ ክሕደት አለች። አብረውት አርገመው መኖር ላዘወተሩ ለጥቂቶች ካልሆነ በቀር እንዲያውቃት ለማንም አይገልጣም የሚል ነበር። ይህቺ ክሕደት ምናልባት "ለማርያምና ለመስቀል አንሰግድም" ማለት ሳትሆን እንደማትቀር በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ጉባኤ የታየው ሁኔታ ያመላክታል። በአፄ ይስሐቅ ጊዜ አባ እስጢፋኖስ ያልተወገዘው ይህቺን ክሕደት ገና ስላልገለጸት ይመስላል። (7) በሌሎች የአገራችን ቅዱሳን በስፋት ከሚስተዋለው በተለየ በተገዳዳሪነት ተነሥተውብኛል የሚሏቸውን ገዳማውያን፣ ካህናተ ደብተራና መሳፍንት ስነቡ ወደራሱ ለመሳብ ከሚያደርገው ጥረት ይልቅ እነርሱን በመንቀፍ የእርሱን ቅድስና ለማጉላት የሚመስል የተርእዮ አካሄድ ይታይበታል። ለምሳሌ፦ በገድሉ ገጽ 72 ከቅስናው በኋላ የሚያሳየው የተነጣይነት ባሕርይ፣ በገጽ 74 ገዳማውያኑን በምንኩስና ስማቸው ከመጥራት ይልቅ "ሰብአ ደብር - የደብሩ ሰዎች" በሚል የለበጣ አጠራር መጥራቱ፣ በተደጋጋሚ በገጽ 93 እና 95 ተከራካሪዎቹን የገዳም መነኮሳት "ጋኔን፣ የሰይጣን ሠራዊት፣ የአጋንንት ማኅበር" በሚል ስያሜ እየጠራ እነርሱን ከመሳብ ይልቅ በትምክህት የማጥጣል አነጋገር መከተሉ ራሱን በማመጻደቅ እንድንጠረጥረው ያደርገናል። ልጆቹም በገድላቸው ገጽ 151 (የሌላውን አገር ምግባር ያን ያህል ዘሪው ያዩ ይመስል!) በድፍን ኢትዮጵያ ላይ የባዕድ አምልኮ፣ የስንበት ሻሪነት፣ የሐሰት መሃላ፣ የዝሙት፣ የንፍስ ገዳይነትና የሐዋርያትን ሥርዓት ጥሰት ክስ በግብጻዊው ጳጳስ ፊት ይዘረዝራሉ። የሚገርመው ጳጳሱ ግብጻዊው አቡነ ገብርኤል ራሱ ቀዳሚት ሰንበትን በማክበር ረገድ እነሱ እንደሚሉት ሳይሆን ከኢትዮጵያውያን የተለየ ያለ ማክበር አቋም ነበረው። (Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, p.147.) ደቂቀ እስጢፋኖስ ግን ጳጳሱ እነሱ በኢትዮጵያውያን ላይ የሚሰነዝሩትንና እሱ ማይቀበለውን ሰንበት ከብር መሻር የተቀበሉቸው አድርገው ራስን ለማጽደቅ በሚመስል መልኩ ይጽፋሉ። እውነት ለመናገር መጀመሪያ ላይ ደቂቀ እስጢፋኖስ ለራሳቸው የሚሰጡት ግምት ግትትና መመጻደቅ ያለበት ይመስላል። ራሳቸውን ገና በቀማቸው "ቅዱሳን" እያሉ መጥራታቸው ከኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. የአትሁቶ ርእስ ትውፊት ያፈነገጠ ነበር። ለዚህ ሳይሆን አይቀርም አባ ዕጓ ብርሃን/ ዕጓ ድንግል "ብፁዐን ትጉሃን እለ ተአምረኪ ተወከሉ፣ እም ሳይሆን አይቀርም ... 'ጻድቅ' እስጢፋ ዘይትሜካሕ በጸማ ገድሉ - 'ጻድቅ' ነኝ ብሎ ከሚመጻደቅ እስጢፋ(ኖስ) ይልቅ ተአምርሽን ተስፋ ያደረጉ ኃጥአን የተመሰገኑ ናቸው..." የሚል ድርሰት በእስጢፋኖስ ላይ የደረሰበት። (8) ፕ/ር ታደሰ ታምራት በጥናታቸው ገጽ 105 ከወጣትነቱ ጀምሮ በምንኩስና ተጠምዶ መጽሐፍ መገልበጥንና ወጣቶችን እያስተማረ በእነርሱ መታጀብን ማዘውተሩን ስለሚገልጹ መሪያቸው አባ እስጢፋኖስም ቅስና ከተቀበለ በኋላ የትዝህርት (ትዕቢት) ጸር የተፈታተነው ይመስላል።

155 ስለ እመቤታችን ሥዕል ሲጠየቁ "ጥሩ ነው፤ ግን የእጅ ሥራ ነው፤ ብቻ በልብህ ሳላት" የሚል ወደ መገዳደር ያጋደለ ምላሽ መስጠታቸውን ስናነብ በመነሻ አቋማቸው ላይ ጥርጣሬ ያድርብናል። በአንድ አጋጣሚ ጳጳሱ ፊት ለውግዘት ቀርበው ሳለም "ከአሁን በፊት ለአብ ለወልድ ለመንፈስ ቅዱስ እሰግዳለሁ ሲባል እንጂ ለማርያም እሰግዳለሁ ሲባል አልሰማንም" የሚል የእምነት ክሕደት ቃላቸውን ከሰጡ በኋላ ጳጳሱ "ለማርያም ባትሰግዱ ስሕተት አይሆንባችሁም፤ ብትሰግዱም ኃጢአት አይሆንባችሁም"[11] የሚል ማግባቢያ ቃል ነገሯቸው "አንተ አባታችን ነህ፤ በመንፈስ ስትነግረን መልካም ነው። አባት ሆይ! በፊትም ለማርያም እንሰግድም ያልነው አቃልለን አይደለም" ብለው እምነው ከጳጳሱ ጋር ለእመቤታችን እንደ ሰገዱ በገድለ አበው ወአኃው ተጠቅሷል።[12] ይህን የደቂቀ እስጢፋኖስ ድርጊትና ክርክራቸውን ስናጤን ከዚያ ቀን በፊት በነበረ ሕይወታቸው "ለማርያም መስገድ አይገባም" በሚል አስተምህሮ ይጓዙ እንደ ነበር መታዘብ አይከብድም። እንዲያ ከተጓዙ ደግሞ እነርሱ ለእመቤታችን እጅ እንዲነሡ ለማግባባት ሲጥሩ የምናያቸው ጳጳስ በቁርጡ ሰዓት መስቀላቸውን ለውግዘት ማንሣታቸው አይቀሬ ነው ብለን መላ እንመታለን። ይህን መላ ምን የሚያጠናክር ንባብ እንይ!

(2.3.3) ቅሉይ ከተጠቀሰው ገጽ ወረድ ብለን ስናነብ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከአቡነ ገብርኤል ውግዘት ያመለጡበት አጋጣሚ ጳጳሱ "እነዚህን ቅዱሳን የማወግዝበት ምክንያት አላገኘሁባቸውም። ሃይማኖታቸው የቀናች ሥርዓታቸውም መልካም ነው። ማርያምን ያምናሉ፤ ይሰግዱላታልም" የሚል ምላሽ ለዘርዓ ያዕቆብ በመስጠቱ ነው።[13] ይህ ከሆነ ለእመቤታችን ባይሰግዱ ኖሮ ይወገዙ ነበር፤ እነርሱ ባይነግሩንም እንሰግድም ባሉባቸው የቀደሙ ጊዜያት ውጉዛን የመሆን ዕድላቸው ሰፊ ነው። አሁንም ዝቅ እንበል!

(2.3.4) ደቂቀ እስጢፋኖስ ውግዘት እንደ ተላለፈባቸው ይጠቁሙኝ አውጋዦቻቸው ግን ጳጳሱ ሳይሆን ደብረ ወርቅ የተባለ የጳጳሱ ሎሌ (ምን አልባት አስተርጓሚው?) የጳጳሱን እጅ ይዞ ወደ ላይ በማንሣት "እነዚህን

[11] በማመን ይከብዳል። እውን አንድ ኦርቶዶክሳዊ አባት "ብትሰግዱም ባትሰግዱም" ይላል?
[12] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.149
[13] ዝኒ ከማሁ፡ገ.151



መነኮሲዎች ክህነታቸውንም፣ ምንኩስናቸውንም አገደናል። በእንጀራም በውኃም አትቀበሏቸው፤ የሚቀበላቸው የተወገዘ ይሁን" ስለ ማለቱ ይገልጻሉ። ሆኖም የጳጳሱ ሎሌ ደብረ ወርቅ እንጂ ጳጳሱ "እኔ እንደዚህ አላልኩም፤ አላወገዝኩም" እንዳለ በመግለጽ መከላከያ ያበጃሉ።[14] መቼም እነርሱ በገድላቸው ቃል በቃል "ተሳስተን ተወግዘን ነበር" እንዲሉ አንጠብቅም። ያሉትን ፍንጮች ተከትለን ማሰላችንን ግን እንቀጥል!

(2.3.5) የደቂቀ እስጢፋኖስ ተከታይ የሆነው ብልሁና ጠቢቡ አባ ዕዝራ የማኅበረ እስጢፋኖስ ተሳላሚዎችን እየመራ ቅድስት አገር ኢየሩሳሌምን ለመሳለም ሔዶ ነበር። በኢየሩሳሌም የነበሩ (ተሳላሚ) ኢትዮጵያውያን መነኰሳት ደቂቀ እስጢፋኖስ ኢየሩሳሌም ሲደርሱ ክስ ያቀርቡባቸዋል። የክሶቹ ይዘት፡-

"(1) በሥላሴ አያምኑም፤
(2) ለማርያም አይሰግዱም፤
(3) ለመስቀል አይሰግዱም፤
(4) ታቦት የላቸውም፤
(5) ቁርባን አይቆርቡም፤
(6) አቡነ ዘበሰማያትና ጸሎተ ሃይማኖት አይደግሙም፤
(7) የኢትዮጵያ ንጉሥ ይገድላቸዋል፤
(8) ጳጳሱ ያወግዛቸዋል፤
(9) ሕጋቸው እንደ ሕጋችን አይደለም፤
(10) አረማውያን ናቸው፤" የሚሉ በጥቅሉ ስንቄጥራቸው ዐሥር የክስ አርእስት ናቸው።[15] አባ ዕዝራ ለእነዚህ ክሶች አንድ በአንድ መከላከያውን ዘርዝሮ ደቂቀ እስጢፋኖሳውያን በክሱ እንደ ተገለጸው እንዳልሆኑ ሞግቷል። "ጳጳሱ ያወግዛቸዋል" ለሚለው ክስ ግን ምላሽ አልሰጠም። አለፈው። በሕግ ቋንቋ እንዲህ እንላለን፡- "Every allegation of fact in the statement of claim, if not denied specifically or by necessary implication, or stated to be not admitted in the statement of defence, shall be taken to be admitted."[16] የአባ ዕዝራን ለውግዘት ክስ መልስ ሳይሰጥ

[14] ዝኒ ከማሁ፡ገ.153
[15] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.288-289፤ ካሕሳይ፡ ገ.70
[16] Civil Procedure Code of The Empire of Ethiopia 1965, Article 235 (2)

ማለፍ እንዲያ ተረጎምኳት። "ለሁሉም ክሶች መልስ ሰጥቶ[17] ሳለ ውግዘቱን ግን በግልጽ ስላልካደ እምኗል፤ ወይም እንዳመነ ይቈጠራል" ያም ሆኖ ፍሊጋችን በዚህ አይቆምም!

(2.3.6) አባ ዕዝራ በአፄ ናዖድ (1488-1500 ዓ.ም.) ጊዜ በነበሩት ግብጻዊው ጳጳስ አቡነ ይስሐቅ ፊት ቀርቦ ሲናገር "... እንዳይካኑ ጳጳስ አውግዟችኋል ይሉናል። እኛም በዚህ ጉዳይ ለሁለት ተከፍለናል፤ አንዳንዱ ክፍል ነፍስ ስላስገደለ ከእርሱ[18] እጅ ክህነት አንቀበልም ይላሉ። አንዳንዱ <u>ከሰማንያ አሐዱ የሕግ መጻሕፍት</u> አልወጣንም፤ አባቶቻችን ከሐዋርያትና ከተከተሉአቸው ሊቃውንት የተለየ ትምህርት አላመጣንም፤ ስለዚህ ግዝቱ አይነካንም ይላል። አንዳንዱ ደግሞ ግዝት አንጥስም፤ ክህነት አንቀበልም፤ ምክንያቱም ሳያጣራ እንዳስገደለን ራሱ ያውቃል" በሚል ለሁለት መከፈላቸውን ገልጾ እርሱ ግን "ክህነት እንቀበል" ከሚሉት ወገን እንደ ሆነ ያስረዳል።[19] ይህችን የቃል ልውውጥ እያየን የቀደመ ውግዘት አልነበረም ማለት ያዳግተናል። ጉዟችን ግን አንድ እርምጃ ይቀጥል!

(2.3.7) ጳጳሱ አቡነ ይስሐቅ አባ ዕዝራን "ይኼንን ሃይማኖት" ይዞ እስከ አሁን ሳይናገር ስለ መዘግየቱ ጠይቆት አባ ዕዝራ በሚደርስባቸው መሳደድ ሊመጣ እንዳልቻለ ይገልጽለታል። በመቀጠልም ለጳጳሱ "ሥልጣን ስላለህ <u>የሞቱትንም በሕይወት ያሉትንም ግዝት ፍታ</u>" ይለዋል። በተጠየቀው መሠረት አቡነ ይስሐቅ ዐራት ምስክሮችን አቁሞ "በጠዋት ያሰርኩትን በምሽት እፈታለሁ፤ በምሽት ያሰርኩትን በጠዋት እፈታለሁ፤ አሁንም በሥሉስ ቅዱስ አፍ የተፈቱ ይሁኑ። የማርያምና የመስቀል ፍቅር ያለባችሁ ዛሬ ጥር 21 ቀን የማርያም በዓል ነው። ለእኔም ለእናንተም ምስክር ትሁነን..." ሲል ግዝቱን በይፋ ይፈታል።[20] እናስተውል! አቡነ ይስሐቅ

[17] ዝምታውን ጌታ ጲላጦስ ፊት እንዳሳየው ያለ አሉታዊ ዝምታ (Silence is not acceptance) ነው ብለን እንዳንወስደው ከዐሥሩ ጥያቄ ዘጠኙን መልሶ አንዷን (ውግዘቷን) ብቻ ነው የዘለላት።
[18] ደቂቀ እስጢፋኖስ ሲሰቃዩና ሲገደሉ ካልተቃወመው ግብጻዊ ጳጳስ - ምናልባትም ከራሳቸው ከአቡነ ይስሐቅ? ወይስ አቡነ ገብርኤል?
[19] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.296
[20] ዝኒ ከማሁ፡ገ.297። ባልታተመው የአባ ይስሐቅ ገድል (ዜና ሞቱ?) ተመሳሳይ ጽሑፍ አለ። ንጉሡ ግን አፄ ናዖድ ሳይሆን አፄ ልብነ ድንግል ነው። ወቅቱም አራቅሊጦስ ነው።



ግዝት የፈታው በሕይወት ላሉት ብቻ አይደለም፤ የተጠየቀውም በሕይወት ላሉት ብቻ አይደለም፤ በሕይወት ለሌሉትም ጭምር እንጂ።[21] ከላይ እንደ ተጠቀሰው ደቂቀ እስጢፋኖስ እርስ በእርሳቸው የጳጳሱ "ግዝት አይነካንም" በሚሉና "ግዝቱን አንጥስም" በሚል ለሁለት መከፈላቸውን በራሳቸው እንደብት ገልጸዋል። ይህ ክፍፍል ከገጽ 294-296 በሰፊው እንደ ተተረከው አባ ዕዝራ ለእመቤታችንና ለመስቀል ሊደረግ ስለሚገባው ስግደ በቃሉ በአደባባይ መሰከረ፤ በተግባርም ለሥዕለ ማርያምና ለመስቀል ሰግዶ ግዝቱን ሲያስፈታ ተቋጨ። ከዚያ ወዲያ ንጉሥ ናዖድ "እኔም ትቻለሁ፤ የደቂቀ እስጢፋኖስን ደም ከማፍሰስ አልጨመርም" ሲል የጳጳሱን ግዝት መፍታት በዐዋጅ አፀናው።[22] በ1421 ዓ.ም. ይፋ የወጣው የደቂቀ እስጢፋኖስና የነገሥታቱ/ ካህናቱ ፍጥጫ ልክ ሰምንተኛው ሺሕ ገባበት የተባለው 1501 ዓ.ም. (7001 ዓመተ ዓለም) ከመግባቱ በፊት ነሐሴ 7 ቀን ባረፉት አፄ ናዖድ ዘመን ከሰባ አንድ ዓመታት (1421-1492) ገደማ መለያየትና ሰቆቃ በኋላ ወይም አቡነ ጳውሎስና ፕ/ር ታደሰ ታምራት በጥናታቸው እንዳመለከቱት[23] አባ እስጢፋኖስ ካለፈ ከ50 ዓመታት በኋላ[24] ደቂቀ እስጢፋኖሳውያን ከንጉሡና ከካባሩ ትውፊት ጋር ሰላም አወረዱ፤ ወዲያውኑ ሙሉ ለሙሉ መተማመን ባይፈጠርም ቢያንስ መዋቅራዊ መፋጠጡ ተቋጨ።[25]

[21] በሕይወት የሌሉት ከግዝታቸው መፈታታቸው አግናዊ የሚሆነው አባ ዕዝራ እንደ ተናገረው ለእመቤታችንና ለመስቀል ከሚሰግዱት ወገን ከሆኑ ነው።
[22] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.301
[23] Aba Paulos, Filsata: The Feast of the Assumption of the Virgin Mary and the Mariological tradition of the Ethiopian Orthodox Tewahido Church, 1988, unpublished, Princeton Theological Seminary; p.38
[24] አባ እስጢፋኖስ ካለፈበት እ.ኤ.አ.1444 ዓ.ም. አባ ዕዝራ ወደ አፄ ናዖድ እስከ ሄደበት 1499 ዓ.ም. ስንቈጥር 55 ዓመት ይሆናል። ምናልባት አፄ ናዖድ የነገሡበት እ.ኤ.አ. በ1494 ዓ.ም. ስለ ሆነ አቡነ ጳውሎስና ፕ/ር ታደሰ የእርሱን ንግሥና እንደ እንቅስቃሴው ማብቂያ (እ.ኤ.አ. 1444 — 1494 ዓ.ም) የቈጠሩት ይመስላል።
[25] ከዚህ ዕርቅ በፊት ሰፋ ያለ ክርክር በደቂቀ እስጢፋኖስና በእነርሱ ተቃዋሚዎች መካከል መደረጉን የሚገልጽ ታሪክ በገድለ አቡነ ዜና ማርቆስ ውስጥ ከገጽ 327-370 በስፋት አለ። ገድሉ፡- (1) የአቡነ ዜና ማርቆስ ልጆች ለፋሲካ ወደ ኢየሩሳሌም እንደ ሄዱ፤ (2) በኢየሩሳሌም አባ ዮሐንስ የሚባል ሮማዊ አለቃ ቤት ተጋብዘው ሳለ ሌሎች አምስት መነኮሳት ወደ ማዕዱ ሲጋበዙ "በመካከላችን የሃይማኖት ጠብ ስላለ ከእነዚህ ሰዎች ጋር አንበላም" በማለታቸው ድብደባና እስራት እንደ ደረሰባቸው፤ (3) በታሰሩበት ቦታ ብርሃን እንደ ወረደ፤ (4) ብርሃኑን ያዩ አይሁዳውያን ካወጡዋቸው በኋላ በኃይለ ማርያም በሚባል (ታዋቂና ምሁር የአባ ዜና

(2.3.8) መምህር ካሕሳይ ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ በጻፉት ጽሑፍ መጨረሻ ገጽ 73 ስለ ውግዘት መፈታት ሲጽፉ የቀደመ ውግዘት መኖሩን አምነዋል ውግዘቱ በአጼ ዘርዓ ያዕቆብ አስገዳጅነት የተሳለፈ ነው ቢሉም፡፡ እንደ

---

ማርቆስ ደተ መዝሙር) መሪዎቸው አፈ ጉባኤነት በጌቴሴማኒ ጉባኤ ተደርጎ ስለ እመቤታችን ወላዲተ አምላክነትና ስለሚገባት የጸጋ ስግደት ከአይሁዳውያን (እስጢፋኖሳውያን) "ደብተራ" "አይሁዳውያን" ነው የሚሏቸው፤ እስጢፋኖሳውያን በምላሹ ከንጉሡ በማጣጋት ክርክር መካሄዱን፤ (5) በክርክሩም አሸንፈው ይሏዋል። ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.285ና 286) ጋር ከርከር መካሄዱን፤ (5) በክርክሩም አሸንፈው ይሏዋል፡፡ ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.285ና 286) ጋር ወደ አጼ ናዖድ መላካቸውን ይገልጣል፡፡ (ገድለ አቡነ ዜና ማርቆስ፤ 2ኛ ከሕልማት ጋር ወደ አጼ ናዖድ መላካቸውን ይገልጣል፡፡ (ገድለ አቡነ ዜና ማርቆስ፤ 2ኛ ከሕልማት ጋር ወደ አጼ ናዖድ ብሰ/ ማተሚያ ቤት፡፡)

እትም፤ 2005 ዓ.ም. ብሰ/ ማተሚያ ቤት፡፡) ከገጽ 283-296፡- (1) በአባ ዕዝራ መሪነት ወደ ኢየሩሳሌም ጉዞ በተመለሱበት ወቅት ከሌሎች ገዳማት ተጓዦች ጋር በስጊድ ዙሪያ በተነሣ ጥያቄ ስለ መደረጉ፤ (2) በጉዞው ወቅት ከሌሎች ገዳማት ተጓዦች ጋር በስጊድ ዙሪያ በተነሣ ጥያቄ ሁለት ስለ መነሣቱ፤ (3) ለአነ አባ ዕዝራ ("ትንሣኤስ ለአለ አመነ፤ ብርሃነክ ፈኑ ዲቢሃ ሲባል) የትንሣኤ ብርሃን እንደ ወረደላቸው (T/C በገጽ 291፤ ኅዳግ ቁ.54 የጠቀሱት ሊባል) የትንሣኤ ብርሃን መውረድ ትክክለኛ ጥቅስ አይመስልም፤ ትክክለኛው "ትንሣኤስ ለመስቀልከ ንሰግድ" ለብርሃኑ መውረድ ትክክለኛ ጥቅስ አይመስልም፤ ትክክለኛው "ትንሣኤ ለአለ አመነ" ነው፡፡)፤ (4) ለእመቤታችን ስጊድ ስለ ማድረግ ጨምሮ በብዙ ጉዳዮች እንደ ተከራከሩና በክርክሩ ላይ የነበረውም አቡነ ዮሐንስ የሚባል ጳጳስ እንደ ነበር፤ (5) ከክርክሩ መልስ የአባ አበከረዙንን ዕረፍት ተረድተው ካስቀበሩት በኋላ በእሽናፊነት ወደ አጼ ናዖድ አደባባይ መጥተው ሃይማኖታቸውን መስክረው ግዝት እንዳስፈቱ በቅደም ተከተል ተጽፏል፡፡ ይህ ክርክር በተአምረ ማርያምም ስለ መመዝገቡና የአባ ዕዝራ ገድል ጸሐፊ እንደሚለው ዮሐንስ የሚባል ጳጳስ በወቅቱ በኢየሩሳሌም እንዳልነበረ T/C ጌታቸው በገጽ 289፤ ኅዳግ ቁጥር 39ና 40 ነግረውናል፡፡ ስለዚህ ዮሐንስ የተባለው የክርክር መሪ የአባ ዕዝራ ገድል ጸሐፊ እንደሚለው ጳጳሳ ሳይሆን የአቡነ ዜና ማርቆስ ገድል ጸሐፊ እንደ ተናገረው አለቃ ብቻ ነበር ማለት ነው፡፡ ወይም ምናልባት ክርክሩ ስሙ በአልቅና ከተጠቀሰው ዮሐንስ ፊት ተደርጎ የአባ ዕዝራ ክህነት ግን እንሱ በዚያው ለረጅም ጊዜ ቆይተው በEncyclopedia Aethiopica, Volume 4፤ ገጽ 747 በተጠቀሱት አርመናዊው የኢየሩሳሌም ጳጳስ አቡነ ዮሐንስ (ከ.ኢ.አ.1485-1491)፤ ወይም ምናልባት ዳንኤል ክብረት በዕጨጌ ዕንባቆም መጽሐፋ ገጽ 10 የጠቀሳቸው የግብፁ ፓትርያርክ ዮሐንስ 13ኛ (1476-1516) በኢየሩሳሌም በተገኙበት ተከናውኖ ይሆናል፡፡ T/C ታደሰ አባ ዕዝራ በኢየሩሳሌም ቆይታው እደ ጥበባትን ተምሮ ይህንኑ እየሠራ አጼ ናዖድ ዘንድ መቆየቱን በጥናታቸው ገጽ 114-115 ስለሚገልጹ አባ ዕዝራ ኢየሩሳሌም ሳይቆይ/ ሳይመላለስ እንዳልቀረ መገመት ይቻላል፡፡

ለማንኛውም ከግጥምጥሞሹ እነ አባ ዕዝራ ወደ ነባሩ ኦርቶዶክሳዊ አስተምህሮ የገቡት በአጼ ናዖድ ቤተ መንግሥት በተደረገ ጉባኤ ብቻ ሳይሆን እነርሱን ከማይቀበሉ መነኮሳት ጋር በማለ ሲካሄዱ ከነበሩ ተደጋጋሚ የቀደሙ ክርክሮችና የግብጻውያንን ትውፊት በዐይናቸው ካዩ በኋላ መሆኑን መረዳት ይቻላል፡፡ የአጼ ናዖድ አደባባይ እነ አባ ዕዝራ ስለ ሰጊድ የተከራከሩበት ከመሆን ይልቅ የመመለስ አቋማቸውን ያሳወቁበት ይመስላል፡፡



እውነቱ በአጼ ዘርዓ ያዕቆብና ቀደም ሲልም በአጼ ዳዊት ተአምረ ማርያምና ትዱሳት ሥዕላት ከገብጽ መምጣታቸው እየታወቀ በተአምረ ማርያምና በቅዱሳት ሥዕላት ላይ በምንታዌ የተሞላ አቋም የሚያንጸባርቁትን ደቂቀ እስጢፋኖስ ለማውገዝ የግብጽ ጳጳሳት ከንጉሡ ጋር እስኪደረግባቸው ይጠብቃሉ ማለት ተአማኒነት የሚኖረው አይደለም፡፡

የደቂቀ እስጢፋኖስን እንቅስቃሴ በሚመለከት አያሌ ገድላትን በማገላበጥ ያጠኑት T/C ታደሰ እስጢፋኖሳውያን ተወግዘው እንደ ነበር፤ ቢወገዙም ("Although officially excommunicated") በሚደንቅ መልኩ ሥልጣነ ክህነት ይወስዱ እንደ ነበር፤[26] ኋላ ግን በአባ ዕዝራና በአባ ገብረ መሲሕ ጥረት ከነባሩ ትውፊት እንደ ተዋሐዱ ገድለ አባ ገብረ መሲሕን[27] ዋቢ አድርገው ጽፈዋል፡፡[28] በበኩሌ በዚህ የተነሣ ለአባ ዕዝራ የተለየ ውዴታ አለኝ፡፡ ይህቺን ንኡስ ርእስ እኔም እንደ መምህር ካሕሳይ አባ ዕዝራን ለማዘከር የገድሉ ጸሐፊ ስለ አባ ዕዝራ ቀብር ጽፎ ሲጨርስ በገጽ 314 ባሳረገበት መንገድ ላሳርጋት፡፡ "ዐፅሙን በሳጥን አስቀመጡት፤ ማኅሌት አድርገው በማዕጠንት ዐጠኑት፤ መብራት አበሩ፤ ወንጌሎችንም አነበቡ፤ የሚገባውን ሥርዓት ሁሉ ፈጸሙ፡፡ በዕብራውያን ሐሳብ (አቈጣጠር) በታሙዝ 11 ቀን፤ በግእዝ በሐምሌ 21 ቀን በማርያም በዓል ዕለት

---

[26] T/C ታደሰ በአድናቆት ያዩት 'ተወገዙ' ከተባለ በኋላ ክህነት የመቀበል ጉዳይ ራሱን በመሰወር የሚከናወን በመሆኑ ያን ያህል የሚያስደንቅ አይደለም፡፡ በደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ ገጽ 308ና ኅዳግ ማስታወሻ ቁጥር 144 ይህ ተደብቆ ክህነት የመውሰድና ታቦት የማስባረክ ሁኔታ ተብራርቷል፡፡ ባልታተመው ገድሉ አቡነ ገብረ መሲሕ የጳጳሳት መምጣት ከተቋረጠ ከሠላሳ ዓመት በኋላ ከመጡት አቡነ ይስሐቅ በ63 ዓመቱ ቅስና ሲቀበል ራሱን ሸሽጎ እንደ ነበር "እልቦ ዘአመሮ" እስመ ወሰጠ አልባሲሁ ... ከመ ይሰወር እም አዕይንቲሆሙ ለአሉያን" የሚል ንባብ አለ፡፡ በመጽሐፈ ትዝታ ዘአለቃ ለማ ኃይሉ መጽሐፍ ገጽ 124 እንደምናነበው በአገራችን ቅባቶችና ጸጋዎችም ዘንድ ቤሉለት "ወልድ ዋሕድ በተዋሕዶ ከበረ" እያሉ ክህነት መውሰድ የተለመደ ነው - እሁን ድረስ! ስለዚህ ከውግዘት መፈታት በፊት ክህነት መውሰዳቸው በሸሸግ ስለሆነ አያስደንቅም!

[27] በ103 ዓመቱ እስኪያርፍ ድረስ አበ ምኔታቸው የነበረው የአባ ገብረ መሲሕ ገድል፤ "ወሰገዱ ለማርያም ወለመስቀለ ዋሕድ እንዘ ይብሉ 'አክሊለ ምክሕነ፤ ወውቀኖሚተ መድኃኒትነ፤ ወመሠረተ ንጽሕነ ኮነ በማርያም ድንግል' - ለማርያምና ለአንድዬ መስቀልም ሰገዱ፤ እንዲህ እያሉ፡- የትምክሕታችን አክሊል፤ የመዳናችን መጀመሪያ፤ የንጽሕናችን መሠረት በማርያም ሆነ" ይላል፡፡ (UTCSC Library Digital Scholarship Unit: http://digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3A10133#page/238/mode/2up ; visited on Nov 8, 2016)

[28] Taddesse Tamrat, p.113

በሕይወቱ በተመኘበት መቃብር ቀበሩት። የማኅበሩ አገልጋይ የአቡን ዕዝራ ጸሎትና የብርሃን እናት የእመቤታችን ጸሎት ከእኛ ጋራ ለዘላለም ይኑር፤ አሜን፣ አሜን፤ ይሁን፣ ይሁን።"[29]

አባ ዕዝራን ብቻ አወድሰን አፄ ናዖድን መዘንጋት ደግ አይደለም። ስለ አፄ ናዖድ ይልማ ዴሬሳ የጻፉት ለዚህ ሰላማዊ ውሳኔው መገለጫ መሆን ይችላል። እርሳቸው "አፄ ናዖድ ታላቅ ገገር ከመሆኑ ሌላ ፍርድም ዐዋቂ ነበር። በአደባባይ ፍርድ ማየት ብቻ ሳይሆን ለእያንዳንዱ ሰው በዕለት ሥራው መጠንና ሚዛን ያለው አስተያየት የሚሰጥ ንጉሥ ነበር" ይሉታል።[30] የንጉሣችንን አፄ ናዖድ ነፍስ ጌታ በለምለሙ ቦታ ያሳርፋት! ወደ ሌላ ቅሬታ ልሻገር።

## 2.4. እውን ለእመቤታችን የጸጋ ስግደት መስገድ የተጀመረው ከዘርዓ ያዕቆብ ወዲህ ነው?!

T/C ጌታቸው እና የፐሮፌሰሩን መደምደሚያ እንዳለ እየተቀበሉ የተረኩት መ/C ካሕሳይ የደቂቀ እስጢፋኖስን በመነሻ ወቅት "ለማርያምና ለመስቀል አንሰግድም" የሚል ሃይማኖታዊ አመፃ ለማጽደቅ በሚያስመስል መልኩ "እሰግድ ለኪ - እሰግድልሻለሁ' የሚለውን በተአምረ ማርያም መቅድም ውስጥ ያለ ንባብ ያመጣው አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ነው" ይሉናል።[31] T/C ኤፍሬምም ይኼንኑ ይናገራሉ።[32] አባባላቸውን ለመቀበል ይከብደናል። ስለዚህ መንፈራገጤን ልቀጥል! "እሰግድ ለኪ" ለምትለዋ ቃልና ለተያያዥ የጸጋ ስግደቶች ከዘርዓ ያዕቆብ የቀደመ ትውፊታዊ ማስረጃ ላስስ!

(2.4.1) "በሰጊድ ሰላም ለኵሉን መልክኣትኪ ማርያም" ወይም "እሰግድ ለኪ ከመ ኃጢአትየ ታስተሰርዪ - ለኃጢአቴ ይቅርታን ታሰጪኝ ዘንድ እሰግድልሻለሁ" የሚሉት ከንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ የ1426 ዓ.ም. ንግሥና ቀድመው በ1417 ዓ.ም. ባረፉት አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ መጽሐፈ ሰዓታት

---

[29] ካሕሳይ፡ገ.75። በአብዛኞቹ የእስጢፋኖሳውያን ገድላት ይህ መደምደሚያ አለ።
[30] ይልማ ደሬሳ፣ "የኢትዮጵያ ታሪክ በ16ኛው ክፍለ ዘመን"፣ 3ኛ እትም፣ 2007 ዓ.ም.፣ገ.11
[31] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.149፣የገጻን ማስታወሻ foot note ቁ.107። ካሕሳይ፡ገ.51
[32] Ephraim Issac, p.71.



ውስጥ "ስብሐተ ፍቁር[33] ዘማርያም" ተሰኝተው የተካተቱ ናቸው። በገድሉም ውስጥ "ለስም አጠራሯ ስግደት ይሁንና ከእመቤታችን ሥዕል ፊት ሲጸልይ በፍቅሯ ጣዕም ኅሊናው ተመሰጠ" ተብሎ ተጽፏል።[34]

(2.4.2) ለእመቤታችንና ለመስቀል፣ ለቤተ ክርስቲያን እና ለቅዱሳት መካናት ስለሚገባ የጸጋ ስግደት ቅዱስ ያሬድም አዚሞልናል።

ስለ እመቤታችን፡- "ኵሉሙ ነገሥተ ምድር ይሰግዱ ለኪ፣ ወይልሕሱ ጸበለ እግርኪ፣ ማርያም እምነ፣ ወእሙ ለእግዚእነ - የጌታችን እናት የእኛም እናታችን ማርያም፣ የምድር ነገሥታት ሁሉ ይሰግዱልሻል፣ የእግርሽንም ትቢያ ይልሳሉ..." ይላታል።[35] እንጨምር! ስለ እመቤታችን ለጊድ! በድጓው ለፍሮ ለታኅሣሥ በዓታ "እስመ ለዓለም" ብለን በዜማና በአቋቋም የምንዘምራት ጥዑም ዜማ እንዲህ ትላለች "በጽሐ ሠናይ ወአልጸቀ ዘመን፣ ወበዓላ ለቅድስት ማርያም፣ እንተ በላዕሌሃ ተመርአወ ቃል፣... ዳዊትኒ ይቤላ በአልባሰ ወርቅ፣ ዑዕፍት ወኁብርት፣ ይሰግዱ ለኪ ኵሉሙ ነገሥታተ ምድር፣ ወይልሕሱ ጸበለ እግርኪ - የበጎነት [ጊዜ] ደረሰ፤ ዘመኑ መጣ፣ ቃል (ወልድ) የተሞሸረባት የቅድስት ድንግል ማርያም በዓልም (እንዲሁ ደረሰ)፤... ዳዊት ይላታል፡- (አንቺ!) 'በወርቅ አልባሳት የተጌጥሽና የተሸለምሽ፣ የምድር ነገሥታት ሁሉ ይሰግዱልሻል" ሲል ቅዱስ ያሬድ በመዝሙረ ዳዊት ምዕራፍ 44 ቊ. 12-13 ያለውን ኃይለ ቃል ለእመቤታችን ሰጥቶ ተርጕሞ አቅርቦልናል።[36] ከግዝረት ድጓ አቡንም "ርግብ ዘመከብብ ማርያም... ሰብ እዕመረ ዮሴፍ ንጽሐ ሥጋሃ፣ ሰገደ ላቲ ወእምሃ - ማርያም የመከበብ (ሰሎሞን) ርግብ ናት፤ ... ዮሴፍ የሥጋዋን ንጽሕና አይቶ ሰገደላት፤ እጅ ነሳት" ይላታል። በዚሁ ድጓ ሰላም "ብርሃን ሠረቀ ለሕዝብ፣ መድኀን መጽአ እም እርያም፣... ኢየሱስሃ እስመ ሰመይዎ በሕገ ኦሪት እመ ገዘርዎ፣ ንዑ ናንሶሱ በብርሃኑ፤ ንዑ ንስግድ ለማርያም - ለሕዝብ ብርሃን ወጣ፣ መድኃኒት ከአርያም መጣ፤... በሕገ ኦሪት በገዘሩት ጊዜ ስሙን ኢየሱስ አሉት፤ ኑ! በብርሃኑ እንመላለስ፣ ኑ! ለማርያም እንስገድ" የሚል ሐረግ

---

[33] ድርሰቱ በነገሥታት የገባ ስርዋጽ ነው የሚሉ ቢኖሩም የትውፊቱን ነባርነት አይቀይረውም። ምክንያቱም ድርሰቶች የሚደረሱት ከነባር ትውፊት ነው።
[34] የአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫና አባ በጸሎተ ሚካኤል ገድል፡ገ.120።
[35] ድጓ ዘክሐሊ ኪዳን ምሕረት፡ገ.382
[36] ዝኒ ከማሁ፡ገ.384

አለ::[37] ኤራቅሊስ የተባለው አባት ከቅዱስ ያሬድ ጋር በተባበረ ቃል "...ዮሴፍ፡ ሰገደ ለድንግል ወገነየ ለንጽሐ - ዮሴፍ ለድንግል ሰገደ፤ ንጽሕናዋንም አመሰገነ..." ይላል::[38]

(2.4.3) **ስለ መስቀል ቅዱስ ያሬድ፡-** "በሰማይ ፀሐየ አርአየ፣ ወበምድር ዕፀ መስቀል ተረክበ፣ ከመ ይሳለምዎ እምሰማያት ወረደ - በሰማይ ፀሐይን ገለጠ፣ በምድርም መስቀል ተገኘ፣ ይሳለሙት ዘንድ ወረደ" ይላል::[39] "ለመስቀልከ ንሰግድ"ን በኋላ እናምጣት:: አባ ጊዮርጊስ እንዲሁ "ጌታችን ሆይ በመስቀልህ ፊት እንሰግዳለን፤ ለእጅህና እግርህ ችንካሮችም እንንበረከካለን" ይላል::[40]

**ቤተ ክርስቲያንን ስለ መሳለም፡-** "በሰላም ንጊሣ ለቤተ ክርስቲያን፣ ወበሰላም ንቁም ቅድሜሃ፣ ነአምኀ ንበላ በሀ፣ ምስትሥራየ ኃጢአት ይዕቲ፣ ቅድስት ደብተራ - (ወደ) ቤተ ክርስቲያን በሰላም እንገስግስ፣ በጸጥታ ከደጇ እንቁም፤ እጅ እንንሳት፤ ሰላም (ለኪ) እንበላት፣ የኃጢአት ማስተሥረያ፣ ቅድስት ድንኳን (ደብተራ) ናት::"[41] ባልታተመው የይስሐቅ ዘከስዋ ገድልም ተቃዋሚዎቹ ግዝት ስላሰብን ሰላም አንልህም ባሉት ጊዜ "ሕድጉኒከመ እትአማኀ ቤተ ክርስቲያን፤ እስመ ይቤ 'ንሳለማ ለመድኃኒትነ እስመ ዋካ ይእቲ ወብርሃን' - ቤተ ክርስቲያን እሳለም ዘንድ ተውኝማ! 'መድኃኒታችንን እንሳለማት፤ ብርሃን ፋናም ናትና' ይላታልና"[42] ሲል መልሶላቸዋል::

**ቅድስት እግር ሐዶ ጎልጎታን ስለ መሳለም፡-** "ወአንቲኒ ቀራንዮ፣ መካነ ጎልጎታ፣ እስመ በኀቤኪ ተሰቅለ ኢየሱስ ክርስቶስ፣ ሀየ ሀየ ሀየ ንሰግድ ኵልነ፣ ኀበ ቆመ እግረ እግዚእነ - አንቺ ቀራንዮ፣ የጎልጎታ ምድር፣ ክርስቶስ በላይሽ ተሰቅሏልና፣ የጌታ እግር በቆመበት፣ በ(ዚያ) ሥፍራሽ (3 ጊዜ)

[37] ድጓ ዘግዝረት፡ገ.206-207
[38] ሃይማኖተ አበው ዘኤራቅሊስ ም.48 ቁ. 36፡ገ.158
[39] ድጓ ዘመስቀል፡ገ.111
[40] ውዳሴ መስቀል ዘአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ ትርጉም በዳንኤል ክብረት፣ 2006 ዓ.ም.ገ.78::
[41] ጸመ ድጓ ዘኀብርኀር ሐሙስ፡ገ.136
[42] ቅዱስ ያሬድ፡ጸመ ድጓ ዘሆሳዕና፡ገ.167



ሁላችን እንሰግዳለን" ይላል ሊቁ መዝሙር 131 ቁ. 7 ወሰል ብሎ እየታየው::[43]

ለመስቀሉ እንኳን ሰው ጢስም ሰግዷል:: ቅዱስ ያሬድ ይቀጥላል፡- "ዘዕጣን፡ እንጸረ ሰገደ ጢስ፣ ወተረክበ በጎሚሥ፣ መስቀል ቅዱስ - ዕጣን አመላከተ (አነጣጠረ)፤ ጢስ ሰገደ(ለት)፤ ቅዱስ መስቀል በፍለጋ ተገኘ::"[44]

መጋቤ ብሉይ ሠይፈ በ2001 ዓ.ም. ለመስቀል በዓል ባዘጋጁት መጣጥፍ "...ክብር ለቅዱስ መስቀል በሚደረግበት ጊዜ ለዕንጨት አምልኮት የሚቀርብ የሚመስላቸው ሰዎች ከጥንት ጊዜ ጀምሮ ነበሩ፤ ዛሬም አሉ:: ስለ እነርሱም መምህራችንና አባታችን ቅዱስ ያሬድ 'ህለው እለ ይቤሉ ለዕፅኑ ታመልኩ? ወለዕፅኑ በዓለ ትገብሩ?' - ለዕንጨት ትሰግዳላችሁን? ለዕንጨትስ በዓል ታደርጋላችሁን?' የሚሉ አሉ ይልና ጥያቄውን በጥያቄ ሲመልስ 'ኢቀደሶኑ፡ ደሙ ክቡር? ወበእንተዝ ንሕነ ናመልኮ - ዕፀ መስቀሉን የክርስቶስ ደም አልቀደሰውምን? ስለዚህ እኛ እንሰግድለታለን [እናከብረዋለን]::"[45] ዛሬም ስለ መስቀል ክብር ለሚጠይቁን ሰዎች መልሳችን የቅዱስ ያሬድ መልስ ነው፤" ብለው ነበር::[46] አባ ዕዝራ ከዚህ የመጋቤ ብሉይ ጽሑፍ ጋር በተስማማ ንግግሩ "የምንሰግደው ለዕንጨትና ለድንጋይ አይደለም፤ ሊቀ ጳጳስ ሲቀድሰው ስለሚቀደስ ነው እንጂ፤ ቅዱስ ሜሮን ሲቀባው ያን ጊዜ የእግዚአብሔር መንፈስ ያድርበታል:: የምንሰግደው ስለዚህ ነው፤" ብሎ ነበር በእስራኤል ጉዞው ወቅት ለተፈታተነው ግብጻዊ ሲመልስ::[47]

እነዚህ ማሳያዎች "ለአብ ወልድ መንፈስ ቅዱስ ካልሆነ በቀር ሰጊድ የለም" የሚለውን የ"አምልኮ" (Worship) እና የ"ጸጋ" (Veneration) ስግደት ያቀላቀለ አቋም ይሞግታሉ:: እነ ኢዛና በሳንቲማቸው የቀረጹት፣ እነ አፄ ገብረ መስቀል የተጠሩበት፣ እነ ቅዱስ ላሊበላና እነ አፄ ይስሐቅ በስመ

[43] ድጓ ዘእሌኒ፡ገ.28
[44] ዝኒ ከማሁ፡ገ.28
[45] ድጓ ዘመስቀል፡ ገ.25:: እዚህ ላይ "ናመልኮ" የሚለው የቅዱስ ያሬድ ቃል በዘይቤ ትርጓሜው "ናከብር" ማለት ነው:: (ኪዳነ ወልድ ክፍሌ መዝገበ ቃላት ገጽ 594 ተመልከት::)
[46] መስቀል መልዕልተ ኵሉ ነገር፣ልዩ እትም፣2001 ዓ.ም፡ገ.9
[47] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.292

መንግሥት የተጠቀመበት[48] መስቀል ክብር ለኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት በዘርዓ ያዕቆብ የመጣ ድንገቴ ትምህርት አልነበረም፤ አይደለምም።

(2.4.4) ቅዱሳት ሥዕላትን በሚመለከት ትውፊቱ ዓለም አቀፋዊ ይዘት ያለው ነው። ከክርስትና ታሪክ ጋር የተያያዘ ታሪክም አለው።[49]

---

[48] የቅዱስ ላሊበላና የአፄ ይስሐቅ ስመ መንግሥት ገብረ መስቀል ነው። የላሊበላ ባለቤት ስሟ መስቀል ክብራ (ቅድስት) ይባላል። (መስቀል መልዕልተ ኩሉ ነገር፡ገ.9)

[49] ስለ ጌታ ሥዕል አጀማመር፦ (1) ሥዕሉ የተጀመረው ዮሐንስ ወንጌላዊ ሰርሞ ነኝ ጌታ ሥዕል ... ጲላጦስ ስለ ጌታና ስለ እመቤታችን ለጢባርዮስ ጢባርዮስ ጌታን በማለለት ጊዜ ነው፤ (2) ጲላጦስ ስለ ጌታና ስለ እመቤታችን ለጢባርዮስ ... ቁመታቸውንና ባሕርያቸውን ገላጭ ደብዳቤ መላኩን ነው፤ (3) ቬሮኒካ በላከው ጽሑፍ እንደገለጸው ... ፊቱን እንዲያደርቅበት ጌታ በሰጠው ጨርቅ መስቀሉን ተሸክሞ ወደ ቀራንዮ ሲወጣ ፊቱን እንዲያደርቅበት ጌታ በሰጠው ጨርቅ ምስሉ ታትሞ ስለ ቀረ ነው፤ (4) በመታብሩ (እንዲጠርግበት) ሸሙን ሰጥታው በሸሙ ላይ ምስሉ ታትሞ ስለ ተገኘ ነው የሚሉ ትውፊቶች ያሉ ሲሆን በተገኘው ሰበዝም (ከፊን) አካሉ ታትሞ ስለ ተገኘ ነው የሚሉ ትውፊቶች ያሉ ሲሆን የእመቤታችንን ሥዕል በሚመለከት የመጀመሪያው ሠዐሊ ቅዱስ ሉቃስ መሆኑ በእኛም ሆነ በሌሎች አብያተ ክርስቲያናት በስፋት ይታመናል። (አቡነ ጎርጎርዮስ፤ የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ታሪክ፡ገ.115-120።)

... ያለው ይመስላል። ለምሳሌ። (1) በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ሥዕል የመሣል ትውፊት ረዘም ያለ ዕድሜ ያለው ይመስላል። ለምሳሌ። (1) በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ሥዕል የመሣል ትውፊት ረዘም ያለ ዕድሜ ያለው ይመስላል። (2) በኢዛና ሳንቲሞች ላይ የተቀረጸ በጥንታው አባ ገሪማ ወንጌል ቅዱሳት ሥዕላት ይታያሉ። (2) በኢዛና ሳንቲሞች ላይ የተቀረጸ ... (በላይ ግደይ፤ "ገንዘብ፣ ባንክና መድኅን በኢትዮጵያ" ፤ 1994 ዓ.ም፤ የመስቀል ምስል አለ። (በላይ ግደይ፤ "ገንዘብ፣ ባንክና መድኅን በኢትዮጵያ" ፤ 1994 ዓ.ም፤ 2ኛ እትም፡ገ.23።) (3) በላሊበላ ሕንጻ (በተለይ ቤተ ጎልጎታ) ልዩ ልዩ በዓለት ላይ የተቀረጹ ሥዕላት አሉ። (Encyclopadia Aethiopica, 2007, Volume 3, p.818.) (4) በአፄ ዳዊት ዘመን ከግማደ መስቀሉ ጋር ሥዕለ ማርያምና የኩርዐተ ርእሱ ሥዕል ስለ መምጣቱና ለሥዕላቱ አፄ ዳዊት ስለ መስገዱ ተጽፏል። (መጽሐፈ ጤፉት፡ገ.48-49።) (5) በጣና ማርያም፣ ግሸን ደብረ ከርቤ፣ ዝዋይ ደሴት ገዳማት፣ አንኮበር ኪዳነ ምሕረት፣ ደብረ ወርቅ ማርያም በ13ኛውና በ14ኛው ክፍለ ዘመን የተሣሉ የማድግዳና የመንበር ሥዕላተ ማርያም እንዳሉባቸው በጥናት ተረጋግጠዋል። (Stanisaw Chojnack, Aethiopica 5 (2002), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, "Notes on a Lessor Known Marian Iconography in 13th and 14th Century Ethiopian Painting", p.42-66.) (6) በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን ፍሬጽዮን የሚባል የእመቤታችንን ሥዕል በመሣል የታወቀ መነኩሴ እንደ ነበር እርግጥ ነው፤ ከእሱ ዘመን ቀደም ብሎ በቤተ ክርስቲያን ግድግዳና በመጻሕፍት ብቻ ይሣል የነበረው ሥዕለ ማርያም በእሱ ዘመን በስፋት በተንቀሳቃሽ ብራና ለብቻው እየተሣለ ለምዕመናን መመጸኛ የዋለ ይመስላል። (Encyclopadia Aethiopica Volume 5, p.148.) (7) በበዕደ ማርያም ዘመን በእትርጌጎስ ማርያም በፈረንጅ (ጣሊያናዊ የተሣለ ካቶሊክ ምናልባት - Francesco de Brancaleon - ፍራንቼስኮ ደ ብራንካሌዎን) የተሣለ ሥዕል እመቤታችን ጌታን በቀኝዋ ሳይሆን በግራ እጇ ታቅፋ ስለሚያሳይ አጣላጭ ትውፊታችንን ለቀል የሚል ክርክር ተነስቶ እንደ ነበር መዘገቡ የትውፊቱን ነባርነት ያሳያል። (ዓለመ ኃይሉ፣ የአፄ በዕደ ማርያም ዜና መዋዕል፡ መግቢያ፣ አልቫሬዝ (ትርጉም የናስ ቢጋስ)፡ገ.264-5።) (8) በደቂቀ እስጢፋኖስ ገዳማትና ገድላትም የሥዕል ጥበብ አለ። በተለይ የአባ መዝገበ ሥላሴን ገድል ወልደ ኢየሱስ የተባለ ሰው ወብ አድርጎ አሥሎታል።



"የቅዱሳት መጻሕፍትን ምሥጢር በሥዕል መግለጽ የተጀመረው በዘመነ ሰማዕታት ነው። ክርስቲያኖች በስደት ዘመናት በየዋሻውና በየጉድጓዱ እየተደበቁ ሥርዓተ አምልኮታቸውንና ቅዱሳት መጻሕፍትን የማመስጠር ሥራቸውን ያከናውኑ ነበር።... ትምህርተ መስኮት ይተላለፍ የነበረው በሥዕል ነው። የካታኮምፕስ [ግበበ ምድር/ የምድር ውስጥ ዋሻ] ክርስቲያኖች ይጠቀሙበት የነበረው በሥዕል የቅዱስ መጽሐፍን ምሥጢር የመግለጽ መንገድ ለትውልድ ተላልፏል።"[50] አባታችን አቡነ ጎርጎርዮስ ካልዕ "በሥዕል ፊት ቆሞ መጸለይ ከባለ ሥዕሉ ረድኤት በረከት ምልጃ መሰመን መማጠን ነው። ለሥዕል መስገድ ሥዕልን መሳም ደግሞ በፊት የሥዕል ተቃዊዎች ወይም ጸረ ሥዕሎች (አይኮኖማኪ[51]) እንደሚሉት ዛሬም ብዙ ጸረ ማርያሞች እንደሚያጥላሉት ለጣዖት መስገድ ጣዖት መሳም አይደለም።... በሥዕሉ አማካይነት ለሥዕሉ ባለቤት ክብርንና ፍቅርን ለመግለጽ ነው። ይኸውም የቤተ ክርስቲያን ህልውና ከታወቀበት ጊዜ ጀምሮ የነበረ ጥንታዊ ትውፊት (Tradition) ነው። በእምነትና በፍቅር የሆነ ነገር ደግሞ ያንጻል እንጂ አይጎዳም። የእግዚአብሔር መንግሥት የሚወረሰው በፍጹም እምነት ቅንነት በተሞላበት ፍቅርና ትሕትና እንጂ በተጥባበ ነገር (Rationalism)[52] አይደለምና" ይላሉ ሶርያዊውን የስምንተኛ መቶ ክፍለ ዘመን የቤተ ክርስቲያን ሊቅ ዮሐንስ ዘደማስቆን ጠቅሰው።[53] የእርሳቸውን ጥቆማ ተቀብለን ዮሐንስ ዘደማስቆን እንፈልገው!

(2.4.5) ምስጋና ለዘመናዊው የመረጃ መረብ አገልግሎት ፈጣሪዎች ይሁንና በ8ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የነነውንና በእኛም የትርጉሜ መጻሕፍትና[54]

---

[50] ገ/ዮሐንስ ገ/ማርያም፣ ክርስትና በኢትዮጵያ፣ በ16ኛው ክፍለ ዘመን፡ገ.22

[51] Iconclasts

[52] የሌላ ቤተ እምልኮ ሰዎች በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ላይ ያላቸው የተዛባ እይታ ከዚህ ይመነጫል። በእነርሱ ቤተ እምልኮ ያሉትን የተአምራት፣ የፈውስ፣ የትንቢት፣ "የክንፍረንስ"...ዘይቤዎች ሁሉ ሲሆን በእምነት ዐይን እንድንመዝን ይገፋፉናል። ወዲህ ሲመጡ ደግሞ ነገሮችን ሁሉ በምክንያትና ውጤት ግንኙነት እየለኩ በፍልስፍና ዐይን ለማጣጣል ሌሉ እምነት ማለት መገለጥ መሆኑን ረስተው ደምበኛ አስላሳይና የአመክንዮ ሰዎች ሆነው ይቀርባሉ።

[53] አቡነ ጎርጎርዮስ፡ገ.99

[54] ለምሳሌ፦ በማቴ 7:7 አንድምታ ገጽ 93 ዮሐንስ ዘደማስቆ በቀርባን ጊዜ የቢታውን ካልበቃው የመለየት ጸጋ እንደነበረው ተገልጿዋል።

በስንክሳር[55] ስሙ የሚታወቀውን ዮሐንስ ዘደማስቆን [John of Damascus (675-745)] አገኘነው። ዋይ ዋይ! እርሱ ትንታግ ነው! ዐፅሙን ያለምልም! ጥሜን ቆረጠልኝ! ከንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ንግሥና 700 ዓመታት ገደማ ቀድሞ የተነሣው ሊቅ ሰጊድን በሁለት ክፍሉ ሲተነትን እንዲህ ይላል፦

"Worship is the symbol of veneration and of honour. Let us understand that there are different degrees of worship. First of all the worship of latreia, which we show to God, who alone by nature is worthy of worship. When, for the sake of God who is worshipful by nature, we honour His saints and servants, as Josue and Daniel worshipped an angel, and David His holy places, when be says, 'Let us go to the place where His feet have stood.' (Ps. 132.7) Again, in His tabernacles, as when all the people of Israel adored in the tent, and standing round the temple in Jerusalem, fixing their gaze upon it from all sides, and worshipping from that day to this, or in the rulers established by Him, as Jacob rendered homage to Esau, his elder brother, (Gen. 33.3) and to Pharaoh, the divinely established ruler. (Gen. 47.7) Joseph was worshipped by his brothers. (Gen. 50.18) I am aware that worship was based on honour, as in the case of Abraham and the sons of Emmor - ሰጊድ የማክበርና የወዳጅነት ትዕምርት (ምልክት) ነው። የተለያዩ ዓይነት ሰጊዶች አሉ። የመጀመሪያው የአምልኮ ስግደት ነው፤ ለፈጣሪ ብቻ ይቀርባል፤ እርሱ ብቻ ነው በባሕርዩ የአምልኮ ስግደት የሚገባው። አምልኮ ለባሕርዩ ስለሚስማማው አምላክ ስንል እርሱ ያከበራቸውን ቅዱሳን አገልጋዮቹንም እናከብራለን፤ ኢያሱና ዳንኤል ለመልአኩ እንደ ሰገዱለት፤ ዳዊት 'እግሮቹ በቆሙበት ቦታ እንሰግዳለን' (መዝ.131:7)[56] እንዳለ፤ እሥራኤላውያን የቃል ኪዳኑ ታቦት ባለበት ቤተ መቅደስ ዙሪያ ተሰባስበው በአንቃዕድዎ እንደሰገዱ፤ ያዕቆብ ለታላቅ ወንድሙ ለዔሳውና ለፈርዖን እንደሰገደ (ዘፍ.33:3፤ 47:7)፤ ለዮሴፍ ወንድሞቹ እንደሰገዱለት (ዘፍ.50:18) እንሰግዳለን። ይህ ሰጊድ እንደ ዔቦር ልጆችና እንደ አብርሃም የአክብሮት (የጸጋ) መሆኑን ዐውቃለሁ" ይላል። ሁለቱ ቃላት

[55] የታኅሣሥ 8 ስንክሳር ዮሐንስ ዘደማስቆን ስለ ክብረ ቅዱሳት ሥዕላት ባደረገው ተጋድሎ ይጠቅሰዋል። ሊቁ በእምነት ረገድ የምሥራቅ ኦርቶዶክስ (ኬልቄዶናዊ/ መለካዊ) መሆኑን ምንጮች ቢያመለክቱም የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ትውፊት መለካዊነቱን ሲያጎላው አይታይም። (Encyclopadea Ethiopica, Vol 3, p.295).

[56] መጽሐፍ ቅዱስ፤ የብሉይና የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት፤ 1980 ዓ.ም.፤ አ.አ፤ ብ/ሰ/ማ/ድ።



ይሰመርባቸው! "worship of latreia, which we show to God, who alone by nature is worthy of worship" እና "worship based on honour" የሚሉ አገላለጾች በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. "የአምልኮ ስግደት" እና "የጸጋ ስግደት" በሚል በጉልህ ይታወቃሉ።

(2.4.6) ሊቁ አመክንዮ ይደረድራል። "ለመጽሐፍ አንባብያን ፊደሉ፣ ለማያነቡ ሥዕሉ፥ ቃሉን ይነግራቸዋል። ቃል ለጆሮ፣ ሥዕል ለዓይን ይናገራሉ" ይላል ታቦትን ማንጸሪያ አድርጎ። በራሱ አንደበት፦

"We proclaim Him also by our senses on all sides, and we sanctify the noblest sense, which is that of sight. The image is a memorial, just what words are to a listening ear. What a book is to the literate,that an image is to the illiterate. The image speaks to the sight as words to the ear; it brings us understanding. Hence God ordered the ark to be made of imperishable wood, and to be gilded outside and in, and the tablets to be put in it, and the staff and the golden urn containing the manna, for a remembrance of the past and a type of the future. Who can say these were not images and far-sounding heralds? And they did not hang on the walls of the tabernacle; but in sight of all the people who looked towards them, they were brought forward for the worship and adoration of God, who made use of them. It is evident that they were not worshipped for themselves, but that the people were led through them to remember past signs, and to worship the God of wonders. They were images to serve as recollections, not divine, but leading to divine things by divine power - እርሱን በመላ ሕዋሳታችን እናገንነዋለን፤ ክቡር የሚሆን ሕዋሳችንን ለእርሱ እንቀድሳለን፤ ይኸውም ዓይናችን ነው። ሥዕል (ለዓይን) ማዘከሪያ ነው፤ ድምጽ ለጆሮ (ማንቂያ) እንደሚሆነው ሁሉ። መጽሐፍ ለአንባቢ ነው፤ ሥዕል ለመሃይምናን። ሥዕል ለዓይን ይናገራል፤ ቃላት ለጆሮ እንደሚያቃጭሉ ሁሉ፤ ሁለቱም ተደምረው ተዘክሮአችንን ከፍ ያደርጋሉ። ከዚህ የተነሣ ጽላተ ሕጉ ይቀመጥበት ዘንድ እግዚአብሔር ታቦት

ከማይነቅዝ ዕንጨት እንዲሠራና ውስጡና ውጩ እንዲለበጥ፣ ለመና መያዣም እንዲሆኑ ወጭቶችንና ጭልፋዎችን ከወርቅ እንዲቀረጹ አዘዘ፤ ያለፈውንና የሚመጣውን ለማስታወስ ይሆን ዘንድ (ዘጸ. 25-29):: እኒህ ምሥሎች አፍ አውጥተው የሚሰብኩ አብሣሪዎች አልነበሩም የሚል ማን ነው? ምሥሎቹ ስውራን አልነበሩም፤ ለሚያያቸው ሁሉ ለስጊድና ለአምላክ ፈጣሪ ፊት ለፊት ይታዩ ነበረ እንጂ:: የሚሰገድላቸው ስለ ራሳቸው አይደለም፤ በእነርሱ የተነሣ ያለፈውን ለማዘከርና ገባሬ ተአምር እግዚአብሔርን ለማመስገን እንጂ:: የማዘከሪያ/ የመታሰቢያ ምሥሎች ናቸው፤ (በራሳቸው) መለኮታውያን አይደሉም፤ ነገር ግን በአምላክ ኃይል ወደ እርሱ ያቀርቡናል::"[67]

(2.4.7) አቡነ ጎርጎርዮስና ረዳት ፕሮፌሰር ሉሌ መላኩ እንደሚሉት ከ787 ዓ.ም. የሁለተኛው ኒቅያ ጉባኤ በኋላ በካቶሊክ፣ በምሥራቅ ኦርቶዶክስና በኦሪየንታል አብያተ ክርስቲያናት ያለ ልዩነት ሥዕል የጸጋ ስግደት ይደረግለታል::[58] ለእመቤታችን ሥዕል፣ ክብርና አማላጅነት ደግሞ ሁሉም ከፍ ያለ ቦታ ይሰጣሉ:: ለሥዕላቱ የጸጋ ስግደት ይሰግዳሉ፤ ምዕመናን ሻማና ጡዋፍ ያበራሉ፤ ካህናት በማዕጠንት ያጥናሉ:: ይህን ደግሞ መፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ ዝንባሌ ስላቸው ማብራራት አልፈለጉም እንጂ ፕ/ር ጌታቸውም በጥልቀት ያውቁታል፤ በመጠኑም በመግቢያቸው ነካክተውታል::[59]

ምሥራቃውያን ኦርቶዶክሶች፣ ኮፕቶችና ካቶሊካውያን ለእመቤታችን ብቻ ሳይሆን ለመስቀልም "Before thy Cross, we bow down in worship, O Master, and thy holy resurrection we glorify" እያሉ እንደሚዘምሩ አነበብን::[60] በተመሳሳይ ይዘትና ድምጸት ቅዱስ ያሬድ በስቅለት ጾመ ድጓ

[57] Apologia of John of Damascus Against those who Decry Holy Images:p.7
[58] ምሥራቃውያን የጸጋ ስግደትን "ፕሮስኪነሲስ - proskynesis"ይሉታል:: (The Encyclopedia of Eastern Orthodox Christianity Edited by John Anthony McGuckin , 2011, p.332. ) ቅድመ ሥዕል እስተብርኮ ማድረጉ በግብጻውያኑም ዘንድ አለ:: (Gawdat Gabra , et'al, The A to Z of the Coptic Church,The Scarecrow Press, Inc. Lanham • Toronto • Plymouth, UK 2009, p.156.)
[59] ደቂቀ እስጢፋኖስ፣ መግቢያ፡ገ.54፤ ኀዳግ ቁ.51::
[60] https://oca.org/orthodoxy/the-orthodox-faith/worship/the-church-year/elevation-of-the-cross :11 October 2016



ከጌታ ሥዕለ ስቅለት ሥር ሆነን እንድንዘምር ሥርዓት ሠርቶ "ለመስቀልከ ንሰግድ ኦ ሊቅነ፣ ወለትንሣኤከ ቅድስት ንሴብሕ ኵልነ፣ ይዕዜኒ:: ወዘልፈኒ - መምህራችን ሆይ! ለመስቀልህ እንሰግዳለን፣ ቅድስት ትንሣኤህን እናወድሳለን፣ ዛሬም ዘወትርም የሚል ቃል አኑሮልናል::[61]

(2.4.8) አቡነ ጳውሎስ በሦስተኛ ዲግሪ ማሟያ ጥናታቸው ገጽ 147 "veneration ... ' is given to the Holy Virgin Mary as well as to the Holy Cross because they have been chosen to be the instruments of salvation - ለቅድስት ድንግል ማርያምና ለቅዱስ መስቀል የጸጋ ስግደት ይደረግላቸዋል፤ ምክንያቱም ምክንያተ ድኂን ለመሆን ተመርጠዋልና" ይላሉ:: እንደ ገና ወረድ ብለው ስለ ክብረ ሥዕል በገጽ 155 ይናገራሉ፤ "The veneration of icons is a part of the Ethiopian Orthodox Church tradition; it is however, directed not to the images but to holy persons whom they represent - ለቅዱሳት ሥዕላት መስገድ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት ነው፤ ያም ሆኖ ስግደቱ ለሥዕሉ (ሥዕሉ ላረፈበት ቁስ አካል) ሳይሆን በሥዕሉ ለተወከሉት ቅዱሳን ነው" ይላሉ አለቃ አያሌውን ዋቢ አድርገው::

(2.4.9) እነ አለቃ አያሌው አርመውና አስተካክለው በማዕላዊው የሊቃውንት ጉባኤ የበላይ ጠባቂነት እንዲወጣ ያደረጉት ድርሳነ ሚካኤል የሰኔ ወር በገፃ በ12ኛው ቀን በሚነበበው ክፍል "ወሥዕላትሰ ቅዱሳት ...ትእምርታተ ምስጢር:: ወመጻሕፍተ ግብረ እግዚአብሔር እለ ይከውኑ ረድኤተ ለኀሊና ሰብእ... ወያዜክርዎ ምስጢረ ረቂቀ...:: ወሶበ ንሰግድ በቅድመ ሥዕላት አምሳካውያት አኮ ዘንሰግድ ለረቅ ወለቀለም ወለግብረ እድ - ቅዱሳት ሥዕላት ... የምስጢር ምልክቶች ናቸው...:: የሰው ኀሊና ... ተስፋ ላይ ያርፍ ዘንድ ረዳት የሚሆኑ ... ረቂቅ ምስጢርን የሚያሳስቡት ድንቅ የሆነ የእግዚአብሔር የሥራው መጻሕፍትም ናቸው... :: ...አምላክ በሚገለጥባቸው ሥዕላት ፊት በምንሰግድበት ጊዜ ለቀለሙ፣ ለወረቀቱ፣ ለቅቡ፣ ለንድፉ የምንሰግድ አይደለም" ሲል የነ ዮሐንስ ዘደማስቆንና የእኅት አብያተ ክርስቲያናትን

[61] ጾመ ድጓ ዘስቅለት፣ ጊዜ ስድስቱ ሰዓት፡ገ.176

"ቅዱሳት ሥዕላት የሚታዩ ቅዱሳት መጻሕፍት ናቸው - Sacred Arts are Visual scriptures" የሚለውን ብሒል ያፀናል።

(2.4.10) የሚያሳዝነው በአንድ በኩል በአበው ወእኃው፣ በአባ አበከረዙን እና በአባ ዕዝራ ገድላት ውስጥ ደቂቀ እስጢፋኖስ ለንጉሡ መስገድንና መምህራቸው እስጢፋኖስን መስደብን እምቢ ብለው እያሌ መሥዋዕትነት እየተነገረ፥ በሌላ በኩል ለማርያምና ለመስቀል መስገድን መከፈላቸው እየተቀበሉ መሔዳቸው በገድላቸው ተርጓሚ "የአባትን ፈለግ እንደ መተው" እየቆጠርም። ፕ/ር ጌታቸው እንጂ "ወደ ትክክለኛው መንገድ እንደ መመለስ" አይቆጠርም። ፕ/ር ጌታቸው እንጂ "ለቅድስት ማርያም ሥዕልና ለክርስቶስ መስቀል እንስግድም ማለታቸውንም ቢሆን... የኒሰኞቹ ልጆች ትተውታል" ሲሉ ሒደቱን የ"መመለስ" ሳይሆን የ"መተው" አድርገው አቅርበውታል።[62] ለእነሱ በመወገን (በመቆጨት) ሳይሆን 'ከስህተታቸው ተመለሱ' ለማለት ነው "ትተውታል" የሚለውን ቃል የሚጠቀሙት ብለን እቃንተን እንዳንተረጉመው በገድሉ ትርጉም መግቢያቸው ደቂቀ እስጢፋኖስን ልክ እንደ ሉተር ተደላድሎ የተቀመጠን እርጌ ሥርዓት ለመለወጥ የተነሡ ታላላቆችና ገናኖች አድርገው በአድናቆት አስቀመጠዋቸዋል። ይህን (ወደ ነባር ርቱዕ/ ኦርቶዶክሳዊ/ ትውፊት የመመለስ) ሒደት በመግለጽ ረገድ ፕ/ር ታደሰ በጥናታቸው ገጽ 113 የተጠቀሙት "by the end of the Century, they already begun conforming with the rest of the Church - በክፍለ ዘመኑ (በ0ሥራ አምስተኛ ክፍለ ዘመን) ፍጻሜ ከተቀረው ቤተ ክርስቲያን (ነባር ትውፊት) ጋር መጣጣም/ መስማማት ጀመሩ" የሚል ገለጻ በመጠኑ ይሻለኛል።

(2.4.11) እስኪ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከቀደመ አመጻቸው ተመልሰው በሒደት ለእመቤታችንና ለመስቀል ሰጊድ የፈጸሙባቸውን አጋጣሚዎች እንጥቀስ።[63] በገጽ 151 እና 178 ማርያምን እንደሚያምኑ እና እንደሚሰግዱላት ተጽፏል። በአባ አበከረዙን ገድል ውስጥ በገጽ 232 ቤተ ክርስቲያን ሲሳለሙና አበምኔት እጅ ሲነሱ እናገኛቸዋለን። በአባ ዕዝራ ገድል ገጽ 293 እንዲሁ እጅ መንሳት አለ። አባ አበከረዙንና አባ ዕዝራ በትእምርተ መስቀል

[62] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.31

[63] ባልታተሙት ገድላትም እስጢፋኖሳውያን ለእመቤታችን ሰጊድ ማድረጋቸው ተጽፏል፡ ለምሳሌ፦ የአባ ኢሳይያስ፣ የአባ ሃ/ሥላሴ (ቅዳሴ ማርያም መቀደስ የሚወድ)፣ የአባ ይስሐቅና የአባ ገብረ መሲሕ (ቀዳማዊና ዳግማዊ)፣ የአባ ሳሙኤል ዘክስዋ፣ የአባ ተክለ ነቢያት ገድላት።



ያማትባሉ።[64] ስሞቻቸው ገብረ መስቀል፣ ብርሃነ መስቀል፣ ገብረ ማርያም፣ ንግሥተ ማርያም የተሰኙ እያሌ ደቀ መዛሙርት አሏቸው።[65] በገጽ 286 አባ ዕዝራ "ለማርያምና ለመስቀል መስገድ እንሰግዳለን፤ ለንጉሥ እንድንሰግድ ግን መጽሐፍ አላዘዘንም!" ብሏል። እዚያው ወረድ ብሎ በገጽ 289 እንዲሁ "ለመለኮት እሳት ልብሱ ለሆነች፣ የዚህ ዓለም ቆሻሻ ላልነካት ለማርያም እንሰግዳለን። ለመስቀልም የስቃዩ አልጋ ስለሆነ እንሰግዳለን። ነቢዩ (ሄኖ.25፡22) ስለ እርሱ በመስዕ (ደቡብ) አቅጣጫ የተተከለ የተመሰገነ ዕንጨት አየሁ፤ ከፍሬውም ለምርጦች ሰጠሁ ይላል። ይህ ስለ መስቀል ነው" ሲል ተናግሯል። በ294 እና 295 አባ ዕዝራ ለማርያምና ለመስቀል እርሱ ብቻ ሳይሆን መምህሮቹም እንደሚሰግዱ ተናግሯል፤ ለንግግሩም ከላይ የቀረቡትን መዝ.131፡7፣ ኢሳ.49፡23 እና የቅዱስ ያሬድ መዝሙራትን ይጠቅሳል፤ ጥቅሱን በተግባር አሳይቶ ግዝቱን አስፈትቷል። ይህ የአባ ዕዝራ ድርጊት "ከጫና እና ሰቆቃ ብዛት የመጣ ነው" ይባል ይሆናል። ነገር ግን ከላይ በተጠቀሱት ለእመቤታችንና ለመስቀል በሰገዱባቸው ጊዜያት ሁሉ "ለንጉሡ ስገዱ፤ መምህራችሁን ስደቡ" ሲባሉ ፈቃደኛ ባለመሆን መራር ሰቆቃዎችን ስለ መቀበላቸው አንብበናል። በመሆኑም የእነ አባ ዕዝራን የሰጊድ ድርጊት የቀደመ አባታቸውን (አባ እስጢፋኖስን) መንገድ የ"መተው" አድርጎ ከማየት ይልቅ ከቀደመ "ስሕተት" የመመለስ አድርጌ መቀበልን እመርጣለሁ።

(2.4.12) ፕሮፌሰርም ቢሆኑ የደቂቀ እስጢፋኖስ በመነሻቸው አካባቢ የነበረ ዓይነት አስተምህሮ በአፄ ያግብአ ጽዮን ዘመን (1278-1286 ዓ.ም.) ተነሥቶ በዐዋጅ "ለሥዕልና ለመስቀል ያልሰገደ... አንገቱ ለገመድ...፣ ንብረቱ ለሠራዊት፣ ... ቤቱ ከጠብመንጃ ለሚወጣ እሳት ይዳረጋል"[66] በመባሉና ዐማፅያኑ ዐዋጁን ተቀብለው "ንጉሡ ያዘዘንን ሁሉ እናደርጋለን፤ ለመስቀልና ለሥዕል እንሰግዳለን" በማለታቸው ዓመፃው ማክተሙን አስፍረዋል።[67] ይኸን ብለው ሲያበቁ ከመነሻው አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቹ ተአምረ ማርያም መቅድም ላይ ያለውን "እሰግድ ለኪ!" ብቻ ለይተው ያልተቀበሉ ይመስል ግሁን በፊት ለአብ፣ ለወልድ ለመንፈስ ቅዱስ እሰግዳለሁ[68] ሲባል እንጂ

[64] ዝኒ ከማሁ፡ገ.246 እና 285

[65] ዝኒ ከማሁ፡ገ.124፣127፣156፣297

[66] የ'እንሰግድም' የአመጻ እንቅስቃሴውን ግርማ እግዚእ የሚባል የአካባቢው ገዥ ለማስቆም ባለመቻሉ በአጋጣሚ በአካባቢው የተገኘው ንጉሥ ያግብዐ ጽዮን ለቅዱሳት ሥዕላትና ለመስቀል በመስገድ አርአያ ሆኖ አማጽያኑን ካሳመነ በኋላ ከዚያ እስከ ደቂት ሁሉም ሰው ሰጊዱን እንዲያከብር አውጇል። (አማርኛ የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 6፣ ገ.157።)

[67] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.24

[68] ድርጊ ብለን በስድሳ ስድስቱ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ እንኳድ ከተባለ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ቃል በቃል 'ለአብ፣ ለወልድ ለመንፈስ ቅዱስ እሰግዳለሁ' የሚል ቃልም አናገኝም።

ለማርያም እሰግዳለሁ ሲባል አላገኘንም" የሚል አመጻቸውን ለማጽደቅ በሚመስል መልኩ "ምንጮች እንደሚሉት ከሆነ፣ እውነትም 'እሰግድ ለኪ' ('እሰግድልሻለሁ') የሚለውን ተአምረ ማርያም ውስጥ ያለውን ጸሎት የመጣው ዘርዓ ያዕቆብ ነው" ይላሉ:: "ሰላም ለኪ፣ እንዘ ንሰግድ ንብለኪ..." የሚለው ቃል በቅዱስ ያሬድ ምዕራፍ ሰፍሮ የዜማ፣ የቅዳሴና የጸሎት መግቢያና ማሰረጊያ ትውፊት በሆነበት አገር፣ ትውፊቱ በእኅት አብያተ ክርስቲያናትም መኖሩ እየታወቀ፣ ከያግብዐ ጽዮን ወደ 150 ዓመታት ገደማ ዘግይቶ የነገሠው ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ በመቅድመ ተአምር 'እሰግድ ለኪ'ን አስገብቷል ብሎ በደምሳሳው እየቀረበ ያለውን "ለማርያም እሰግዳለሁ ሲባል አላገኘንም" የሚል ከቅን ልቡና ያልመነጨ መልስ ለማለዘብ መሞከር ለደቂቀ እስጢፋኖስ የመነሻ ስህተት የተጋነነ ከለላ መስጠት ይመስላል:: ከዘርዓ ያዕቆብ ወዲህ ለእመቤታችን የጸጋ ስግደት መስገድ የተጀመረው "እሰግድ ለኪ" ነባር ንባብ እንደሆነ ለሚያስመስሉ ቈናጽላን በር ላለመክፈት ተአምረ ማርያም ግን ከ"እሰግድ ለኪ" ጋር መሆኑን ጠቅሰው መቅድመ (ለምሳሌ:- ከሃይማኖተ አበው ዘዮሐንስ አፈወርቅ "እዌድሰኪ") ከየመጻሕፍቱ ከተአምሩ ጋር መጠረዙን ቢገልጹት ተቀምጦ በላዩ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን የተሻለ ይሆን ነበር የሚል ትሁት እይታ አለኝ::

## 2.5. በመቅድመ ተአምረ ማርያም ዙሪያ... T/C ጌታቸው ከየት አምጥተው አገናኙት?!

T/C ጌታቸው ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ተአምረ ማርያምን ከዐረቢ(ኛ) አስተርጉሞ በአገር ውስጥ የተፈጸሙ ተአምራትን አካትቶ ለየገዳማቱ መላኩ አንድ የጭቅጭቅ ምንጭ እንደ ሆነ ይገልጻሉ::[69] በተለይ "ፍጥረት ሁሉ ስለ እመቤታችን ተፈጠረ፣ አዳምና ሔዋን ስለ እመቤታችን ተፈጠሩ፣ ቁርባን መቀረብ ያልቻለ ተአምሯን ሰምቶ ይሒድ፤ እንደ ቆረበ ይቈጠርለታል' የሚሉ ንባቦችና "የበላዔ ሰብእ ታሪክ" በየገዳማቱ አበምኔቶች ዘንድ ተአምሩን ለመቀበል አስጨናቂ አድርጎት እንደ ነበር ጽፈዋል:: ይሁን እንጂ T/C ጌታቸው በመጽሐፉ መግቢያ ገጽ 26 ካስቀመጡልን የግምት ማሳያ ንባብና የግርጌ ማስታወሻ[70] ውጭ ደቂቀ እስጢፋኖስ እና ዘርዓ ያዕቆብ በእነዚህ

[69] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.25-26

[70] T/C ጌታቸው ምንጭ ጠቅሰው ደቂቀ እስጢፋኖስ ተአምረ ማርያምን ከቤተ ክርስቲያናቸው ሥርዓት እንዳላስገቡ ጥርጣሬያቸውን ይገልጻሉ:: በማኅበራዊ መገናኛ ብዙኃን ያገኘኋቸው



ምንባባት ይዘት ስለ መጋጨታቸው (ፕሮፌሰር) በተረጎሟቸው ገድላት ውስጥ አናገኝም:: ተአምረ ማርያም በገድሉ ገጽ 128 ብቅ ብሎ እናየዋለን:: ሆኖም በንባብ ሰዓት አወሳሰን ካልሆነ በቀር በይዘት ደረጃ ያን ያህል የውዝግብ ምንጭ ሆኖ አልቀረበም::

የተነሣበት ጥያቄ ሁለት ነው:- "ከወንጌል ንባብ በኋላ ይነበብ ወይስ አይነበብ?" የሚልና ለመጽሐፈ ተአምረ ማርያም 'እጅ የመንሳት' ጉዳይ:: የእጅ መንሳት ጥያቄውን ከደቂቀ እስጢፋኖሳውያን ወገን የሆነው መነኵሴ ተአምሩን ይዞ ከመጣ መልእክተኛ ተቀብሎ ካነበበው በኋላ እጅ በመንሳቱ ሲቋጭ እናገኘዋለን:: የተአምረ ማርያም ንባብ እንደ ቅዱስ ወንጌል፣ ግብረ ሐዋርያት፣ መልእክተ ጳውሎስና ሌሎች የሐዋርያት መልእክታት በቅዳሴ መካከል ሳይሆን ከቅዳሴ ውጭ የሚነበብና የሚሰማ ተደርጎ ሥርዓት በመሠራቱ የንባቡ ሰዓት በዘላቂነት የማጨቃጨቅ እድል ያለው

አንዳንድ ወዳጆቼም በደቂቀ እስጢፋኖስ ገዳማት እስካሁን ድረስ ተአምረ ማርያም እንዳልገባና እንደማይነበብ ነግረውኛል:: በድረ ገጽ ያገኘኋቸው መጣጥፎች ግን ይህን ያስተባብላሉ:: ( http://digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3A13074#page/222/mode/2up : Visited on Nov. 8, 2016.) ተአምሩን ያለመቀበል አዝማሚያ ቀደም ሲል ነበረ ከተባለም አዝማሚያው ከላይ ከተጠቀሱት የመቅድሙ ይዘቶች ይልቅ በተአምሩ ውስጥ የአባ እስጢፋኖስና የተከታዮቹ የቀደመ የአመጻ ታሪክ በዝርዝር ስለ ቀረበ ራሳችንን በራሳችን፣ በገዛ ገዳማችን እናሰድብም ከማለት የመነጨ ሊሆንም ይችላል:: ምክንያቱም (ከአባ ዕዝራና አባ ገብረ መሲሕ ጀምሮ) በአሁን ሰዓት ያሉት ገዳማውያን ስጊድን ጨምሮ ለእመቤታችንና ለመስቀል አንድ ኦርቶዶክሳዊ ሊያደርግ የሚገባውን ክብር ሁሉ ይሰጣሉ:: (Denis nosnitsin, New Branches of the Stephanite Monastic Network? Cases of Some Under-Explored Sites, Hamburg University, 2013):: ለምሳሌ:- በአባ ገብረ መሲሕ ገድል ውስጥ እመቤታችን ሥዕሏን ለሣለ ሰው ስላደረገችው ተአምር፣ ልጇ ውሃን ስለማፍለቁ (በእንተ ዘአንቅዐ ማየ ወልዳ) በተአምረ ማርያም መልክ ተጠቅሷል:: ንባቡም "መንክረ ግብረት እግዝእትነ ማርያም - እመቤታችን ማርያም ድንቅን አደረገች" ነው የሚለው:: (ከላይ በተጠቀሰው ድረ ገጽ የሚገኝ ገድለ አቡነ ገብረ መሲሕ) በተአምር ዙሪያ ጥያቄ የተነሣው በገድለ አበው ወአኃው ሲሆን ይህ ገድል ደግሞ የተጻፈው T/C ሺፈራው በቀለ በደቂቀ እስጢፋኖስ ቀዳሚ ቃል እንደጠቀሱን እ.ኤ.አ. ከ1468-1478 ዓ.ም. (በእኛ 1460-1471 ዓ.ም.) ነው:: ይህ ማለት አባ እስጢፋኖስና ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ካለፉ በኋላ ነው:: በመሆኑም ዘርዓ ያዕቆብ ካለው በዘመኑ የተደረጉ ሁነቶችን የማስመዝገብ ልምድ አንጻር እ.ኤ.አ. በ1441 ዓ.ም. (በእኛ 1433 ዓ.ም) በተጻፈው ተአምር ውስጥ ከአባ እስጢፋኖስ ጋር እ.ኤ.አ. በ1437 ዓ.ም. (በእኛ 1429 ዓ.ም. አካባቢ) የተደረገው ክርክር የመካተት ዕድል አለው:: ምናልባትም በመቅድሙ ይዘት ሳይሆን የስግደት ተቃዋሚነታቸው ታሪክ በተአምሩ በመካተቱ የተነሣ መጀመሪያ ላይ ተአምሩን ስላልተቀበሉ ይሆናል በማኅሌተ ፅጌ "ዘለ ይልብ አፈቅረኪ ወኢያፈቅር ተአምርኪ ክርስቲያናዊ፣ ኢክርስቱን ውእቱ አይሁዳዊ፣ ወሰርፀ እስጢፋ ሐሳዊ..." የተባሉትና እነሱም ቀደም ሲል ተአምሩን ለመቀበል ፈቃደኝነት ያጡት::

አይመስለኝም:: ከቅዳሴ በፊት ወይም በኋላ ካልሆነ በቀር በጸሎተ ቅዳሴ ጊዜ ከራሱ ከቅዳሴው፣ ከወንጌል፣ ከሐዋርያት ሥራ፣ ከመልእክታተ ጳውሎስና ከሰባቱ መልእክታተ ሐዋርያት ውጭ እንደ ገድልና ተአምር ያሉ መጻሕፍት እንደማይነበቡ አሁን ድረስ የፀና ሥርዓት ነው::[71] ከዚህ ውጭ ተአምረ ማርያም በደቂቀ እስጢፋኖስና በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ መካከል ያለ መግባት ምንጭ ስለ መሆኑ በተተረጎሙት ገድላት ውስጥ በግልጽ አልሰፈረም:: Ch... ጉዳዩ ከተነሣ ዘንድ ግን ጥቂት ልናገር!

(2.5.1) ተአምረ ማርያም መጻፍና ማንበብ የተጀመረው ድንገት አይደለም:: በግብጽም ሆነ በኢትዮጵያ የእመቤታችን ተአምር ከ10ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በፊት[72] ባለው ጊዜ በተበታተነ መልኩ ይነገር እንደ ነበርና በ12ኛውና በ13ኛው ክፍለ ዘመን ደግሞ በስብስብ መልኩ መጠረዙን፣ ጥራዙ መጀመሪያ ወደ ልሳነ ዐረቢ፣ ከዚያም ወደ ግእዝ እንደተተረጎመ አቡነ ጳውሎስ በዶክትሬት ማሟያ ጥናታቸው ገጽ 52 ምንጭ ጠቅሰው ጽፈዋል::[74] ስለ ሆነም ተአምረ ማርያም ድንገት በ15ኛው ክፍለ ዘመን የመጣ ጽንሰ ሐሳብ አለመሆኑ ሊሰመርበት ይገባል:: በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን በቤተ ክርስቲያን የአገልግሎት ሥርዓት ተቋማዊ በሆነ መልኩ ከመግባቱ በቀር ትርጉሙም የተጀመረው በአፄ ዳዊት ዘመን እንጂ በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ አለመሆኑ

[71] በቅዳሴ ጊዜ ስላለው ሥርዓት፦ "ይደሉ ከመ ይኩን አርምሞ ወተደሞ ውስቴቱ . (በቅዳሴ ጊዜ) አርምሞና ተደሞ ሊሆን ይገባል...ከ4ቱ ሐዲሳት (ወንጌል፣ የሐዋ.ሥራ፣ መልእክታተ ሐዋርያት እና መልእክታተ ጳውሎስ) በቀር ሌላ እንደ ገድል እንደ ተአምር ያለ አይነበብም[.]::" (መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፣ ሥርዓተ ቅዳሴ ቁጥር 44፡ገ.96::)
[72] እመቤታችን ስትፀነስ ጀምሮ ሕይወቷ በተአምር የታጀበ ነው:: በዚህ ዓለም በኖረችበት፣ ዛሬም በዐፀደ ሥጋ፣ ነገም - እስከ ዳግም ምጽአት - በአማላጅነቷ ተአምር ይደረጋል ብለን እናምናለን:: እስካሁን በተገኘው መረጃ ተአምሯ ከ10/11ኛው ክፍለ ዘመን ወዲህ ነው ለብቻው በመጽሐፍ መልኩ የተጠረዘ ማለት ከዚያ በፊት ስለ ተአምሯ አይነገርም ማለት አይደለም::
[73] ተአምረ ማርያም በአውሮፓ በተጠናከረ መልኩ መጻፍና መነገር የጀመረው ከ1128-1129 በፈረንሳይ በነበረ ቻንሰር የእመቤታችን አማላጅነት በመታየቱ እንደሆነ የሚገልጹ ጥናቶች አሉ:: (Veronika Six, Aethiopica 2 (1999), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, "Water — The Nile — And Taamra Maryam. Miracles of Virgin Mary in the Ethiopian Version", p.54.) በኢትዮጵያ እሑድ ከቅዳሴ በኋላ ተአምረ ማርያም ማንበብ የተጀመረው እ.ኤ.አ በ1441 ዓ.ም.፣ በእኛ አቆጣጠር በ1433 ዓ.ም. ይመስላል:: (ዝኒ ከማሁ፡ገ.53:: የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 4፣ ገ.160::)
[74] ሙተሲኦች መጽሐፈ ተአምረ ማርያም በጥራዝ መልክ ለብቻው የተሰባሰበው በ11ኛው መቶ ክፍለ ዘመን እንደሆነ ይገልጻል (Miracles of The Blessed Virgin Mary, 1928, Edited by G.G.Coulten and Eilen Power, Published by Harcourt, Brace and Company, introduction, p.x. http://www.strobertbellarmine.net/books/Herolt-MiraclesofBlessedVirginMary.pdf)



ይታወቃል::[75] እንዲያውም ኋላ አፄ ዘርዓ ያዕቆብም በዘመኑ ማስገልበጡና ማስፋፋቱ ባይካድም በ1392 ዓ.ም.፣ በአፄ ዳዊት ዘመን የተአምሩ ትርጉም ተጠናቆ እንደ ነበርና ተአምሩ አሁንም በግሸን ደብረ ከርቤ እንደሚገኝ የሚገልጽ መረጃም አለ::[76] ከአፄ ዳዊት በኋላ ዘርዓ ያዕቆብ በእመቤታችን አማላጅነት በአገር ውስጥ የታዩ አዳዲስ ተአምራትን አስጨምሮ ማስጻፉን የምንነቅፍ ከሆነ ደግሞ የእመቤታችን አማላጅነት ለኢትዮጵያ ሲሆን መጻፍ የለበትም የምንል ያስመስልብናል:: ግብጻውያን በ20ኛው ክፍለ ዘመን እመቤታችን በዘይቱን መገለጹዋን እንደ ተአምር ሲያትቱ እያየን ከኢትዮጵያ የሆኑትን ተአምራት በዘርዓ ያዕቆብ ዘመን መካተታቸውን መንቀፍ አሳማኝ አይሆንም:: እስከ ዳግም ምጽአት እንደሚቀጥል የምናምነው የእመቤታችን አማላጅነት ከዚያ በፊት የሚቆም፣ ወይም ለኢትዮጵያውያን ሲሆን የማይሠራ፣ ቢሠራም የማይጻፍ እንዳናስመስል መጠንቀቅ አለብን::

በተአምረ ማርያም የተካተቱት የእመቤታችን ልደቷ፣ ጽንሰቷ፣ ሕይወቷ፣ ዕርገቷ፣ በምስጢረ ሥጋዌና በነገረ ድኅነት ያላት ሱታፌ በቅዱስ ያሬድ ዜማዎች ውስጥም ተሰጥሮው ይገኛሉ:: ይህ እንዳለ ሆኖ መቅድመ ተአምረ ማርያምን በሚመለከት በየጉባኤ ቤቱ ጥያቄዎች እንደሚነሡ መካድ የለበትም:: ቢያንስ እኔ ስማር ጥያቄውን የሚያነሡ የመጽሐፍ ተማሪዎች አይቻለሁ:: በአንድ በኩል ከላይ ፕሮፌሰር ያለ ቦታቸው ከደቂቀ እስጢፋኖስ እንቅስቃሴ ጋር ያያዟቸውን ጥያቄዎች እያነሡ 'መቅድሙ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያንን ለነቀፋ የሚዳርጉ ምንባባት ይዟል' የሚሉ አሉ:: ምክንያቶቻቸውም፦ "የተጠቀሱት ምንባባት ይዘት ከመጻሕፍትና ከቀደመው ኦርቶዶክሳዊ ትውፊት አይጣጣምም፣ በምንም የማይተካውን ሥጋ ወልደ እግዚአብሔር ተአምር በመስማት የሚፈጸም በማስመሰል ምሥጢረ ቁርባንን ያቃልላል፤ የበላዔ ሰብእ ታሪክም ኃጢአትንና ኃጢአተኞችን በማበረታታት እማንያንን ንዝህላል ያደርጋል፤ ምንባባቱና ታሪኩ ተአምረ ማርያም መጀመሪያ በተጻፈባት የግብጽ ቤተ ክርስቲያን የማይገኙ እና እዚሁ የተጨመሩ ስርዋጾች ናቸው፤" የሚሉ ናቸው:: መ/ር ካሕሳይም ይኸንኑ የትችት አሳብ አንጸባርቀዋል::[77]

(2.5.2) በሌላ በኩል የነቢዩ ኤርምያስ ከእናት ማኅፀን ጀምሮ መመረጥ ሊኖር እንደሚችል የሚያሳይ ጥቅስ (ኤር.1፡5)፣ የቅዱስ ያሬድ "ማርያምሰ ተሐቱ

[75] Taddessee Tamrat, p.11, foot note, 1. ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ ገ.25::
[76] ዲ.ን. ዳንኤል ክብረት፣ የቤተ ክርስቲያን መረጃዎች፡ገ.64:: መጽሐፈ ጤፉት፡ገ.33
[77] ካሕሳይ፡ገ.49

ውስተ ከርሱ ለአዳም ከመ ባሕርይ ፀዐዳ - ማርያም በአዳም ሆድ (ዘር) ውስጥ እንደ ነጭ ዕንቁ ታብራ ነበር" የሚሉ እንዲሁም "ዘእንበለ ይትፈጠር ሰማይ ወምድር፤ ወዘእንበለ ይግረር ምድረ ገነት፤ ሀለወት ስብሕት ቅድስት ወቡርክት ይዕቲ ማርያም - ሰማይና ምድር ሳይፈጠሩ፤ የገነት ምድር ሳትመሠረት፤ የተመሰገነች፤ የተለየች (የተቀደሰች)፤ የተባረከች ማርያም ነበረች" የሚሉ ዜማዎች አሉ።[78] በመጽሐፈ ቀሌምንጦስ ምዕ. 6 ቁ. 51-52 "ከቅድስት ድንግል ማርያም ዘንድ ሥጋ ለመልበስ ባልፈልግ ኖሮ አዳምን፤ ሰማያትንና ምድርን ባልፈጠርኳቸው ነበር።... ሰዎችንም ባልወድ ኖሮ በዚሁ በለበስኩት ሥጋ ባልተገለጽኩላቸው ነበር፤ ይቺ ቅድስት ድንግል ማርያም (የምትፈጠር) ባትሆን ሔዋንን ባልፈጠርኳት ነበር - ሶበሰ ኢኮነት ዛቲ ቅድስት ድንግል ማርያም እም ኢፈጠርክዋ ለሔዋን፤" ተብሏል።[79] ስለሆነም በተአምሩ መቅድም የሰፈረው ሀሳብ አዲስ አይደለም፤ "አጣሞ" ሳይሆን "አጣጥሞ" የሚተረጉም እስካለ ድረስ ነገሩን ንባብ መነካካት አያስፈልግም፤ "ማርያምሰ ተሐቱ ውስተ ከርሡ ለአዳም..." በትርጉም ይቃናል የሚሉ አሉ። "ማርያምሰ ተሐቱ ውስተ ከርሡ ለአዳም..." መባሉ የአዳምን ተስፋ አለመቁረጥና ከእርሷ የሚወለደው ከመንጸፈ ደይን እንደሚያወጣው የሚያመለክት የተስፈኝነት ቃል አድርገን መውሰድ እንችላለን። "ዓለም ሳይፈጠር እመቤታችን ነበረች" ማለት አነዋወሯ (ሕላዌዋ) በግዘፈ ሥጋ ሳይሆን በሕሊና ሥላሴ ነበረች ማለት ነው - የሥላሴን የሚመጣውንና የሚሆነውን አስቀድሞ ዐዋቂነት ለመግለጽ የተቀመጠ የዘይቤ አገላለጽ ነው።

(2.5.3) ቁርባንን በሚመለከት "ተአምር ቁርባንን ይተካል" አልተባለም፤ "እንደ" ወይም በግእዙ "ወይከውና ህየንተ ቁርባን ለእመ ሰምዐ በእሚን" በሚል ሕጹጽ ማንጸሪያ መቁረብ ላልቻሉ ማጽናኛ ነው የተቀመጠው የሚል አተያይ አለ። አተያዩ ሲቀጥል፡- የመቅድሙ ዓላማ ከጸሎተ ቅዳሴ በኋላ ምእመናን ተአምሯን ሳይሰሙ እንዳይሔዱ ማድረግ ነው፤ ተአምር መስማት ቁርባን ይተካል ተብሎ ቢታሰብ'ማ ከቅዳሴ ውጭ ሳይሆን ከቅዳሴ በፊት ወይም በቅዳሴ መካከል በመሥዋዕት ማሳረጊያነት ይነበብ ነበር፤ በዚያው ላይ ጥያቄውን የሚገፉት ብዙ ጊዜ በምሥጢረ ቁርባን የማያምኑ ቀሳጥያን ስለ

[78] ድጓ፡ ገ.389

[79] መጽሐፈ ቀሌምንጦስ፡ገ.93



ሆኑ ዓላማቸው በሰበቡ መላውን ተአምር ማነወር እንጂ ችግራቸው ከመቅድሙ ብቻ ስላልሆነ ከነቱ ላይመለሱ እነርሱን ሰምቶ መጽሐፉን መነካካት አያስፈልግም፤ የተሐድሶ ባዑራቸው የነገረ ሃይማኖት መቆሚያ ፌርማታ ስለሌለው ለእነርሱ መንገድ አንከፍትም ይላል።

የበላዔ ሰብእ ታሪክ የእመቤታችንን አማላጅነት የወንበዴ ዋሻ ያደርጋል ስለ ተባለው የሃይማኖት ሕጸጽ እንጂ የምግባር ሕጸጽ በቅዱሳን አማላጅነት አምኖ ለተማጸንና ቀዝቃዛ ውኃ ሳጠጣ ይቅር ስለሚባል (ማቴ.10:42)፤ ጌታ ከብዙዎች ጻድቃን ይልቅ በአንድ ኃጥእ መመለስ ደስ ስለሚለኝ፤ በተባለው መልኩ የእመቤታችንን አማላጅነት ማቃለል ጌታን ከመፀብሐን (ቀራጮች) ጋር ካመሳሰሉት ወገኖች (ማቴ.9:11)፤ ወይም ዘኬዎስ ቤት ገባ ብለው እንዳሙት ሐሜተኞች (ሉቃ.19:1)፤ ወይም የማርያም መግደላዊትን ሽቱ በመቀባቱ ከዘማውያን ጋር ዋለ (ሉቃ.7:38) ብለው እንዳሙት ተጠራጣሪዎች እንደሚያስቈጥር ቀደምት ሊቃውንት ጽፈዋል።[80] አሁን ባለው ሁኔታ ጥሬ ንባቡ ላይ ከማተኮር ይልቅ የመቅድሙን ቃላት በማቃናት የሚተረጉመው የጊለኛው አስተሳሰብ ገዥ እንደ ሆነ ግልጽ ነው።

እርግጥ በተአምረ ማርያም ኅትመት በኩል ማዕከላዊነትን ያለመጠበቅ ችግር ይታያል።[81] ከዚህ እንጻር ቀደም ሲል በራዕየ ማርያም ባለስርዋጽ ኅትመት

[80] መ/ብ አድማሱ ጀንበሬ፤ኩትኩሐ ሃይማኖት፡ገ.161

[81] በየገዳማት እና አድባራቱ ውስጥ ባሉ የተአምረ ማርያም መጻሕፍት ውስጥ በተአምር ቍጥር መብዛትና ማነስ የተወሰነ ልዩነት አለ። ኅትመቱና ስርጭቱ ብዙ ጊዜ በማዕከል ሳይሆን (የትንሣኤ ዘጉባኤ ባለ 200 ተአምራት ገጸማ ኅትመት እንዳለ ሆኖ) በግለሰብ ነጋዴዎች ስለሚከናወን አንዳንድ የቅርብ ዘመን ታሪኮች ሳይቀር ሳይፈተሹ እየተካተቱበት መታተሙ ደግማግንና ቀኖናንን ከማስጠበቅ አንጻር ተገቢ አይመስለኝም። እነዚህ ነጋዴዎች የሚያሳትሙት ትልቁ ተአምረ ማርያም በጸጋ (ሦስት ልደት) ደጋፊነታቸው የሚታወቁትን የንጉሥ ኀይለ ሥላሴ ታሪክ ቀባብዞ ከማቅረቡም በላይ የአፄ ምኒልክንና የአፄ ቴዎድሮስን ታሪክ በተአምሩ ውስጥ አካትቶ የአፄ ቴዎድሮስን ታሪክ በማጠየም መጻፉ ብዙዎቻችንን ያሳዘነ ነው። በተአምሩ የገዢዎችና ኅትመት ወቅት ምንም ዓይነት የሊቃውንት ተሳትፎ ያለ አይመስልም። አንዳንዴ ተአምር/ ድርሳንና የነገሥታት ዜና መዋዕል በተጋነነ መልኩ ተቀላቅሎ ይታያል። ያለ አግባቡ ተአምራትን ለማብዛት የሚካሄድ ጥንቃቄ ያልተከለበት ቀናኢነትም ያለ ይመስላል።

ለምሳሌ፡- እንጋፋው የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ባለውለታ ተስፋ ገብረ ሥላሴ ዘብሔረ ቡልጋ በ1987 ዓ.ም. በ111 ምዕራፍ ብቻ ባሳተሙት ተአምረ ማርያም መግቢያ "የእመቤታችን የተአምራቷ ዜና... በ1961 ዓ.ም. እትሜ ካወጣሁት ተወስዶ በማዋቴ ቁጭቱ በአእምሮዬ ተቀርጾ ሲኖር...

ቤተ ክርስቲያንን ባልዋለችበት አውለው በኦሮሞና ሺናሻ ወንድሞቻችን ላይ ጸያፍ ንባብ በማስገባት ዋጋ ያስከፈሉ ነጋዴ አሳታሚዎች በቤተ ክርስቲያን ስም ስለሚያወጡዋቸው መጻሕፍት ከማዕከላዊው ተቋም እንዲናበቡ ሊሠራ ይገባል። ኦርቶዶክሳውያን መዛግብት በተለይ ዋና ቅጂዎቹ (ኦሪጅናሌዎቹ) ሊቃውንት ሳያዩዋቸው አንድ ቅጂ ብቻ ከአንዱ ደብር አንጠልጥሎ ለኅትመት መሩጠን ተገቢ አይደለም፤ ሊታረም ይገባዋል። ጠቅላይ ቤተ ክህነት፣ የሊቃውንት ጉባኤና ቅዱስ ሲኖዶስ በዚህ ረገድ ማዕከላዊነት ለማስጠበቅ ቢበረቱልን መልካም ነው።[82] ወደ ሌላ ርእስ…

---

ተአምር ጋር ሌሎች የተአምራቷን መጻሕፍት አክዬ ለማሳተም ቃል መግባቱ ይታወሳል፤ ከሉ በኋላ ባለ 402 ተአምር መጽሐፍ ማሳተማቸውን ያበሥሩናል። እዚህ ላይ የሚታየው ቀናኢነትና ለእመቤታችን ክብረ ተአምራት መገላት ያለው ትጋት መልካም ሆኖ ሳለ ተአምራቱን በየገዳማቱ ካሉ የብራና መጻሕፍት አመሳክሮ ወጥ መጽሐፍ ለማሳተም ሊቃውንትን ለማሳተፍ ጥረት አለመደረጉ ትጋቱን ያጎድለዋል። ገርውንትንም ይፈጥራል። ይህ ችግር በገ/መሳል ብርሃኑ ዘብሔረ አክሱም የመጻሕፍት ኅትመትም ይስተዋላል፤ እርሳቸውም በ2002 ዓ.ም. በግዕዝና በአማርኛ ባሳተሙት መዝሙረ ዳዊት ገጽ 260፤ መዝሙር 150 ላይ "ሰብሕዎ በአውታር ወበእንዚራ" በሚለው ንባብ ውስጥ ጊታር ከ1986 ዓ.ም. ጀምሮ በሲኖዶስ የታገደና በትውፊታችንም የማይታወቅ መሆኑን ባለማገናዘብ "እንዚራ" የሚለው ቃል "ጊታር" እንደ ሆነ ጠቅሰው ያለአግባቡ አሳትመዋል። በትውፊታችን እንዚራ ማለት እርሳቸው እንዳተሙት ጊታር ሳይሆን ተራ በገና ማለት ነው። (መዝሙረ ዳዊት፣ንባቡና ትርጓሜው፡ገ.671።)

[82] ድርሰቱ እነ አባ እስጢፋኖስ ካለፉ በኋላ የተደረሰ መሆኑ እየታወቀ አንዳንድ ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች አባ እስጢፋኖስ መስተብቍዕ ዘመስቀልንና ዘማርያምን የተቃወመ ያስመስላሉ፡ ስሕተት ነው! በመስተብቍዕ ዘመስቀል ውስጥ "ለእሉ ክልኤቱ ፍጡራን ስብሐተ ፈጣሪ ይደልዎሙ፤ እስመ ተዐረዩ በክብርሙ - ለእነዚህ ሁለት ፍጡራን የፈጣሪ ምስጋና ይገባቸዋል፤ በክብር ተካከለዋልና" የሚል ጥሬ ቃል ከንባቡ አወራረድና በይዘቱ ከተካተተ "ክቡር አንተ ንጉሠ ሰዐዋት መስቀል … ለማርያምሰ ዘንሰግድ ሳቲ እስመ ንሥእ ሥጋ እምሥጋሃ እግዚአብሔር ፈጣሪሃ" የመሳሰሉ የደራሲውን ፍጡርና ፈጣሪ በደንብ ለይቶ እንደሚያውቅ የሚገልጹ ቃላት ስላሉ ድርሰቱ የሚናገረው ስግደት የጸጋ መሆኑ ለቅን አንባቢ ግልጽ ነው። ያም ሆኖ የሊቃውንት ጉባኤ ቀናጽላን ላይ በር ለመዝጋት እንዲቻልና ለተ ቀሊላን አንባቢዎችን ለማጽናት ሲባል "ለእሉ ክልኤቱ ፍጡራን ስብሐት ይደልዎሙ፤ እስመ ተሰዐሩ በክብርሙ - ለእነዚህ ሁለት ፍጡራን ምስጋና ይገባቸዋል፤ በክብር ከፍ ብለዋልና" ሊል ቢያቃናው መልካም ሆኖ ይታየኛል። እስተያየቴ በእትሕቶ ርእስ የቀረበ ኦርቶዶክሳዊ አስተያየት ነው።

አስተያየቴ እንዳለ ሆኖ "ለእሉ ክልኤቱ ፍጡራን ስብሐተ ፈጣሪ ይደልዎሙ፤ እስመ ተዐረዩ በክብርሙ - ለእነዚህ ሁለት ፍጡራን የፈጣሪ ምስጋና ይገባቸዋል፤ በክብር ተካከለዋልና" የሚለው ሐረግ ውስጥ 'ስብሐተ ፈጣሪ ይደልዎሙ' ማለት 'ከፈጣሪ የሆነ ምስጋና ይገባቸዋል' ለማለት እንጂ 'ለፈጣሪ የሚገባ ምስጋና ለእነሱም ይደረግላቸው ዘንድ ይገባል' ማለት አይደለም፤ 'እስመ ተዐረዩ በክብርሙ - በክብር ተካከለዋልና' ማለትም 'ከፈጣሪያቸው ጋ



## 2.6. እውን የደቂቀ እስጢፋኖስ ሥራዎች በንጽጽር የእመቤታችንን ስም እምብዛም አያነሡምን?!

አባ እስጢፋኖስ ለተከታዮቹ በምሳሌያዊ መንገድ ቃለ ምዕዳን ሲያስተላልፍ "…እስራኤልን ለበዓሉ ዕለት በብዙ መገለጫ ጋበዛቸው። የግብዣው ጊዜ ሲደርስ በአስደናቂ መገለጥ ያለሰው ዘር ከንጽሕት ድንግል የዳዊት ልጅ ሰው ሆኖ ከዓለም በፊት ያዘጋጃትን ምክሩን ፈጸማት" ይላል።[83] ተርጓሚው ፐ/ር ጌታቸው ደግሞ በኅዳግ ማስታወሻ ቍጥር 97 "ከዘመኑ የቤተ ክርስቲያን ሥነ ጽሑፍ ጋራ ሲተያይ በእስጢፋኖሳውያን ዘንድ የማርያም ስም ብዙም አይታይም" ይላሉ። በቀደመው ንባቤ ይህን የፐ/ር መደምደሚያ በየዋኅነት እንዳለ ተቀብዬ አንጸባርቄው ነበር። እየቆየ ግን መደምደሚያቸውን አጠረጥረው ጀመር። ስጠረጥር ለማነጻጸር ተነሣሁ። ገድለ እስጢፋኖስን ዲ/ን ዳንኤል ክብረት ከተረጎመልን "ዐራቱ ኃያላን" በሚል ርእስ በአንድ የተተጠረዙ ዐራት ገድላተ ቅዱሳን ኅትመት ጋር አነጻጸርኩት። በንጽጽሬም

---

ሳይሆን እርስ በርሳቸው መስቀልና እመቤታችን በክብር ይተካከላሉ' ለማለት ነው ብሎ መውሰድም ይቻላል። ለትርጉማችን ኢጋዥ ንባብ እናምጣ!

ፐ/ር ጌታቸው ውዳሴ መስቀልን ከግእዝ ወደ እንግሊዝኛ በተረጎሙበት ጥናት መግቢያ የአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫን መጽሐፈ ምስጢር ጠቅሰው ኅዕበ ወበ ዘሮፀ ዜና ውስተ አበኒን ከመ ይትከሀዱ በእንተ ማርያም ወመስቀል፤ መንፈቆሙ እንዘ ይብሉ ተዓቢ ማርያም እንተ ወለደቶ እምዕፀ መስቀሉ፤ ወመንፈቆሙኒ ይብሉ የዐቢ መስቀሉ ዘተጠምቀ በደመ ሕማማቲሁ … - አለ፤ ዳግመኛም ስለ ማርያምና ስለ መስቀል እንደሚከራከሩ በጆሮአችን ሰው ያለ ወሬ አለ፤ የቀሩትም (በኋላ) ግማሾቹ ከዕፀ መስቀሉ (ጌታን) የወለደችው ማርያም ትበልጣለች ይላሉ፤ የቀሩትም (በኋላ) ግማሾቹ የስቃይ ደም የተነከረው መስቀሉ ይበልጣል ይላሉ" የሚል ጥያቄ ከአጼ ዘርዓ ያዕቆብ ድርሰት በፊት እንደ ነበረ ይጠቁሙናል። ይህን ጥያቄ አንሥቶ መልስ የሰጠው አባ ጊዮርጊስ የራሱን አቋም ሲገልጽ "እኛ ግን ማርያ[ም] እሷ ወላዲተ አምላክ እንደ ሆነች እናምናለን ። ከመስቀት በተዋሕዶ ሥጋው ደም የተቀደሰ መስቀሉም የብርሃን ምልክት እንደ ሆነ እናምናለን" ይላል ሳያወዳድር፤ የከበሩቸውን ምክንያት ገልጾ ለየብቻ እንደሚያከብራቸው በማብራራት (Getachew Haile, Aethiopica 14 (2011), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, Praises of the Cross, Wedase Masqal, by Aba Giyorgis of Gasecca ውዳሴ፡መስቀል, p.47.)።

የአጼ ዘርዓ ያዕቆብ ድርሰት እንደ ሆነ የሚታመነው መስተብቍዕ ዘመስቀልም ፈጣሪን ከፍጡር ለማስተካከል ሳይሆን በዚህ ክርክር ጥላ ስር አልፎ ሊሆን ይችላል "ለእሉ ክልኤቱ ፍጡራን ስብሐተ ፈጣሪ ይደልዎሙ፤ እስመ ተዐረዩ በክብርሙ - ለእነዚህ ሁለት ፍጡራን የፈጣሪ ምስጋና ይገባቸዋል፤ በክብር ተካከለዋልና" የሚለውን ሐረግ የተጠቀመው።

[83] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.86

T/C ጌታቸው አባ እስጢፋኖስ ለእመቤታችን አለመስገዱን ከገለጹበት ጥሬ ሀቅ በቀር እርሳቸው ከጻፉት የማይስማማ መደምደሚያ ላይ ደረሱ:: ላላይ....

(2.6.1) በአባ እኖሬዎስ ገድል ውስጥ በእኔ ፍለጋ የእመቤታችን ስም በቀጥታ ሲነሣ ያገኘሁት አንድ ጊዜ ብቻ ነው፤ እርሱም ጸሎተ ማርያምን ከሉቃስ ወንጌል ምዕራፍ 1 ቁ. 52 ጋራ በማስተባበር በገጽ 324:: በተቀረ በክርስትና ስም መጠሪያነት በገጽ 335 እና 340 የእመቤታችን ስም አገልግሎት ላይ ውሏል፤ እንጂ የአባ እኖሬዎስ ገድል ስሟን ደጋግሞ ሲያነሣ አላጋጠመኝም::

(2.6.2) በአባ ፊልጶስ ገድል (የፍልሰቱን ሳይጨምር) ውስጥ የእመቤታችን ስም በ6 አጋጣሚዎች መጠራቱን አንብቤያለሁ:: አባ ፊልጶስ "እመቤቱ ሆይ ልመናዬን ስሚኝ፤ በዚችም ሰዓት ኃጥእ ባሪያሽን ከተስፋዬ አታሳፍሪኝ..." እያለ ጠበል በመርጨት በላዩ ላይ ባደረው መንፈስ ቅዱስ ኃይል ድውያንን ይፈውስ፤ አጋንንትን ያወጣ እንደ ነበር ተጠቅሷል::[84] በተጨማሪም በአባ ፊልጶስ ገድል ውስጥ በገጽ 220፣ 233፣ 252፣ 274 እና 278 የእመቤታችንን ስም እናገኘዋለን::

(2.6.3) ወደ ደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላት ስንመለስ ከገጽ 57 እስከ 115 በሚዘልቀው የአባ እስጢፋኖስ ገድል ውስጥ የእመቤታችን ስም በሦስት አጋጣሚዎች በራሳቸው እነሳሽነት ቀጥታ በበጎ ተነሥቶ እናገኘዋለን:: በገጽ 69 አባ እስጢፋኖስ በመንፈሳዊ ተመስጦ ውስጥ ሆኖ "ቅድስት ድንግል ማርያምን እስኪያያትና ቃሏን እስኪሰማ ድረስ የተመሰገንች ሰማያዊ ምሥጢር[85] የሚያይ' ሆኖ እንደ ነበር ተጽፏል:: በገጽ 85 እና 86 አባ እስጢፋኖስ ስለ ጌታ ሰው መሆን ሲያስተምር "ከንጽሕት ድንግል ተወለደ" ይላል:: በገጽ 110 ፕሮፌሰር በጎዳና ማስታወሻ ቢገዳደሩትም የአባ

[84] አራቱ ኃያላን:ገ.203

[85] በመጽሐፈ መነኮሳት ዐሥሩ መዓርጋት ከተባሉት ውስጥ አባ እስጢፋኖስ ሰባተኛ መዓርግ የሚባለው "ንጽሬ መላእክት" ላይ መድረሱን ለመግለጽ ነው:: ያልታተመው የአባ ገብረ መሲሕ ገድል አጼ ናዖድ እስጢፋኖሳውያንን ማሳደድ ትቶ "ለማርያም ወለመስቀለ ዋሕድ ለእመ ሰገዱ ኅድግዎሙ" ለእሉ መነኮሳት - ለማርያምና ለአንድዩ መስቀል ከሰገዱ እኒህን መነኮሳት ተዋቸው (አታሳድዷቸው)" ሲል ንጉሡ የጠራው ገዳማቸውን በዘመቻ ሲያቃጥሉ ይህችን ንባብ የያዘውን የአባ እስጢፋኖስ ገድል አግኝቶ ንባቧን ሦስት ጊዜ ካስነበበ በኋላ መሆኑን ይገልጻል::



እስጢፋኖስ እስኬማ የእመቤታችን ንጽሕና አምሳል ሆኖ ቀርቧል:: ፕሮፌሰር ግን "አርያም" ለማለት ፈልጎ ነው "ማርያም" ያለው ምክንያቱም እስኬማ በእመቤታችን አይመሰልም የሚል ክርክር ያቀርባሉ:: ክርክራቸውን በተከታዮቹ ምክንያት ለመቀበል ይከብዳል:: (1) በፊልክስዩስ መቅድም የተጠቀሰው "እስኬማከኒ እስኬማ መላእክት" የሚል የባሕርይ ንጽሕና ማንጸሪያ በቦታው ካልተገኘ የመላእክት መኖሪያ ከሆነው አርያም እመቤታችን ትቀርባለችና ወደ ትርጓሜና ትንታኔ ከመግባት ቃሉን እንዳለ መቀበል የተሻለ ነው:: (2) ገዳሙ ባሳተመው ገድልም "እስኬማ ልብሱቱ እንተ ይዕቲ አርአያ ንጽሕ ዘማርያም" ተብሎ ነው የተጻፈው::[86] (3) በገድለ አቡነ ገብረ መሲሕ ገድልም እንዲሁ ስለ ምንኩስናው ሲናገር ሁሉቱንም በማስተባበር፤ በተመሳሳይ አገባብ "ወለብሰ ልብሰ ምንኵስና ወእስኬማ ዘመላእክት እንተ ይእቲ አርአያ ንጽሕ ዘማርያም በእደዊሁ ለብፁዕ አቡነ አበከረዙን"[87] በማለት ቃሉን ደግመውታል:: (4) በአባ ኢሳይያስ ገድል እንደ ገና "ወአልበስዎ ልብሰ ምንኵስና እንተ ይእቲ ማኅተመ ብፅዕ አርአያ ንጽሕናሃ ለማርያም ወላዲተ አምላክ"[88] ሲሉ ሠልሰውታል:: (5) በአባ ተክለ ኒያት ገድልም ይኼው ቃል እንደ ወረደ አለ::[89] ስለዚህ ቃሉ "አርያም"ን ወደ "ማርያም" በመለወጥ ሳይሆን ሆን ተብሎና ታስቦበት የሚገባ መሆኑ ይታያልና ደቂቀ እስጢፋኖስን ለውጹእን እንዳናመቻች እንጠንቀቅ!

(2.6.4) በገድለ አበው ወእኃው ውስጥ ታሪካቸው በሰፈረው የአነ ንግሥተ ማርያም ገድል የእመቤታችን ስም ከገጽ 146 እስከ 149 በስፋት ይነሣል:: እርሱ በሰጊድ ዙሪያ በነበረው ክርክር ስለ ሆነ እንለፈው:: ነገር ግን በገጽ 140 "የአምላክ እናት ሆይ! እነሆ ከምሕረትሽ ጥላ ሥር ተደግፈናል፤ በጭንቅ ጊዜ ልመናችንን አትናቂ" የሚሉ ፍጹም ኦርቶዶክሳዊ ተማጽኖዎች በገጽ 152 እና 154 "አክሊለ ምክሕነ - ልቡናችንን ያንሰፈስፉታል::

[86] ገድለ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዶ:ገ.156::

[87] ገድለ አቡነ ገብረ መሲሕ፣ ብራና ቅጠል 23፣ ወይም http://digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3A5453#page/23/mode/2up ፡ Visited on 8 Nov, 2016

[88] ዝኒ ከማሁ፣ ገድለ አባ ኢሳይያስ፣ ብራና ቅጠል 6::

[89] "አልበሶ (ገብረ መሲህ) እስኬማ ቅድስት እንተ ይእቲ ማኅተመ ንጽሕ ዘማርያም ተስፋ ለእማንያን ወክበድ ለንፉቃን - ለእማኞች ተስፋ ለተጠራጣሪዎች ሸክም የምትሆን ይህቺውም የማርያም ንጽሕና ማኅተም ቅድስት እስኬማን አለበሰው!" ይላል ገድለ ተክለኒያት::

የትምክሕታችን አክሊል" እያሉ ስሟን ከውዳሴ ማርያም (ዘሠሉስ) እያጣቀሱ ሲጠሩት ስንሰማ እንደነግጣለን:: ይሄ ማስረጃ 100 በማይሞሉ የገድላቱ ገጾች በዳሰሳ የተገኘ ነው:: ከዚህ አንጻር ፕ/ር ጌታቸው ኃይሌ "ከዘመኑ የቤተ ክርስቲያን ሥነ ጽሑፍ ጋራ ሲተያይ በእስጢፋኖሳውያን ዘንድ የማርያም ስም ብዙም አይታይም" በሚል የደረሱበት መደምደሚያ ተጨባጭ ንጽጽር ተሠርቶ የቀረበ አይመስለኝም! ቢያንስ የእመቤታችን ስም ከገድለ አባ እኖሬዎስና አባ ፊልጶስ ጋር ሲነጻጸር በደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላት በተደጋጋሚ ተነስቷል:: በአባ ዕዝራ ገድል ውስጥ'ማ ስለ እመቤታችን ክብርና ውዳሴ ያለው ማስረጃ የት የለሌ!

(2.6.5) በዚህ ረገድ (ከመነሻው እንቅስቃሴው ባራመደው አቋም ተወግዞ ነበር የሚል አቋም ቢኖረኝም) በእመቤታችንና ደቂቀ እስጢፋኖስ ሁለንተናዊ ግንኙነቶች ዙሪያ መ/ር ካሕሳይ እንደሚባለው ደቂቀ እስጢፋኖስ "ጸረ ማርያም" እንዳልነበሩ ማሳያዎችን በመደርደር አስመስጋኝ ሥራ ሠርተዋል ብዬ አምናለሁ:: ከላይ የጠቀስኳቸውን ስሟን የሚያነሣሱ ድርሰቶቻቸውን፣ አባ ገ/ማርያም የተባለ የደቂቀ እስጢፋኖስ መነኩሴ "እኔ የማርያም ባሪያ ነኝ" ማለቱን[90]፣ የመሠረቷቸው ገዳማት ሁሉ በእመቤታችን ስም መሆናቸውን፣ በጻፏቸው መጻሕፍት ሁሉ የምስለ ፍቁር ወልዳ ሥዕል መኖሩን፣ አንቀጸ ብርሃንና ውዳሴ ማርያም መድገማቸውን፣ ወዘተ... በመጥቀስ ጸረ ማርያም እንዳልሆኑ ተከራክረዋል::[91] አባ እስጢፋኖስ ስለ እመቤታችንና ስለ መስቀል የደረሰው 38 ገጽ ድርሰት ብለው ቈንጥረው ያቀረቡልን በውብ የግእዝ ቋንቋ የተከሸኑ ምንባባት ምናልባት በትክክል የእርሱ ስለ መሆናቸውና በገድሉ ላይ ከተንጸባረቀው አቋሙ ጋር ስለ መጣጣማቸው ተመሳክሮ የሚቀርብ ሰፋ ያለ ጥናት የሚፈልጉ ሳይሆኑ አይቀሩም::[92] ድርሰቶቹ ግን ሲያምሩ! ግእዙ "...

[90] ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.156
[91] ካሕሳይ:ገ.55
[92] በአፄ ናዖድ ቤተ መንግሥት እንደ ታየው እነ አባ ዕዝራ በአደባባይ ለመስቀልና ለእመቤታችን ለማደው ወዲያው ከግዞታቸው ተፈትተዋል:: አባ እስጢፋኖስ በተመሳሳይ ለግዴ ግዞት ያልተፈታሉት በለመሆኑ ማስረጃ የለም፤ ገድሉም ስላለመስገዱ የተነሣውን ክስ አያስተባብልም:: "መምህራችሁን ስደቡ/ አውግዙ" የሚል ጫና እስከ መጨረሻ ቀጥሏል:: ከዚህ አንጻር ከመጀመሪያው አባ እስጢፋኖስ እንዲህ የእርሱ ድርሰት ተብሉ እንደ ቀረበው ጽሑፍ ዓይነት አቋም ያንጸባርቅ ነበር ብሎ ለማመን ያዳግታል:: ድርሰቱ በኋለኞቹ ተነሳሕያን ልጆቹ የአባት ሐሚታና መገለል ለማስቀረት የተጻፈ ስርዋጽ ሊሆን ይችላል::



ንሕነስ ኢኮነ ጸላእያኒሃ ለማርያም..." ብሎ ነው የሚጀምረው:: እርሱን ትቼ አማርኛውን ብቻ ጥቂት ልጥቀስ፤ "...እኛ ከመጠራጠር የተነሣ ሰዎች እንደሚሉን የማርያም ጠላቶች አይደለንም:: ቃላችንም አይደለም፤ አይደለም፤ አዎን፤ አዎን ብቻ ነው:: እኛ ፊታችንን እያማተብን የድንግል ማርያም አገልጋዮች ነን፤ ባሮቹዋም ነን፤ ፊታችንን በሥላሴ ስም እያማተብን አበሳችንን የሚደመስስ ስለ ወለደችልን እንሰግድላታለን::... እንዲህ እያልን እመ ብርሃንን እናመሰግናታለን:: አንቺን ከፍ እናደርግሻለን፤ በስብሐትና በውዳሴም እንሰግድልሻለን:: ዓሳ ከውኃ ወጥቶ በየብስ ለመኖር እንዳይችል ነፍስ የተለየው ሥጋም እንደማይንቀሳቀስ፤ ከግንዱ የተቆረጠ ዕንጨትም እንደማያፈራና እንደሚደርቅ ክርስቶስን በወለደች ማርያም የማያምንም ከመጽሐፍ የተፋቀ (የተደመሰሰ) ነው" ይሏታል ይሉናል::[93] እውነትም የእመቤታችንን ዘለዓለማዊ ድንግልና ስለማይቀበሉ በእኛ ቤተ ክርስቲያን "እፅራረ ማርያም" በመባል የሚታወቁትን "አንጢዲቆንማርያስ[94] - Antidicomarianites[95]" ደቂቀ እስጢፋኖስ በግልጽ ይቃወሟቸዋል::

(2.6.6) ፕሮፌሰር ጌታቸው በገጽ 271 አባ አበከረዙን "...በዘመናችን በትግላችን ጊዜ ረዳት እንዲሆነን እግዚአብሔር አቡነ እስጢፋኖስን አስነሣልን" ሲል ባደረገው ንባብ ላይ በኅዳግ ማስታወሻ ቍጥር 156 "እንዳቸውንም ሌሎቹን የኢትዮጵያ መነኵሳት፣ ለምሳሌ የደብረ ዳሞውን አባ ዮሐኒ፣ የደብረ እስቦት/ ደብረ ሊባኖስ አቡነ ተክለ ሃይማኖት አያነሡም" የሚል ኮርኳሪ ነጥብ ያነሣሉ:: አባ አበከረዙን ከጳውሎስና ጢሞቴዎስ ወዲህ ያሉትን ሐዋርያትና ሊቃውንት በጅምላ ጠርቶ ሲያበቃ መምህሩን ጠቅሶ ማቆሙ ለምን እንደሚያስገርም አልተገለጸልኝም:: ነጥቡ በዘመን ሒደት የታየውን የአቋም ለውጥ ባገናዘበ መልኩ ስላልቀረበ ደቂቀ እስጢፋኖስ እስከ መጨረሻው የአቡነ ተክለ ሃይማኖትን ቅድስና እንደማይቀበሉ በሚያስመስል

[93] ካሕሳይ:ገ.54
[94] ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.216:: አንጢዲቆንማርያስ ፀረ ማርያም ማለት ነው:: (ሲዳ ወልድ ... በሉሌ" እየተባለ ይፈታል:: በእኛ ቤተ ክፍሌ:ገ.231):: በቅኔ ቤትም "ዝ ውእቱ ፀረ ማርያም ብሒል" ... ከወለደች በኋላ ከዮሴፍ ተገናኝታለች ክርስቲያን በ4ኛው ክፍለ ዘመን የተነሡ ጌታን ... የተነሣውን ሉተር በዚህ ("ተደመረት ምስለ ዮሴፍ") የሚሉ መናፍቃንና በ15ኛው ክፍለ ዘመን ... ቃሉ በትውፊታችን ፕሮቴስታንት ስም እንጠራቸዋለን:: (መጽሐፈ ምስጢር:ገ.9፤ 105-109::) ... ፀረ ማርያም! ለሚለው ስያሜ ተለዋጭ ሆኖም ያገለግላል - ፀረ ማርያም::
[95] *Antidicomarianites* - opponents of Mary - እፅራረ ማርያም::

መልኩ አሳሳች እንዳይሆን እፈራለሁ። አባ እስጢፋኖስም ሆነ ተከታዮቹ በቀብ (በማዕረገ ምንዙስና ሐረግ) ቤተ ተክለ ሃይማኖት ናቸው። ጽሑፋቸውም እንደሚመሰክረው ደቂቀ እስጢፋኖስ የአቡነ ተክለ ሃይማኖትንና የደቀ መዛሙርቶቻቸውን ቅድስና ይቀበላሉ። በገዳማቸው እስጢፋኖሳዊው አባ መዝገበ ሥላሴ ያስጻፈው አባ ዮሐኒን ጨምሮ የሚያካ የአቡነ ተክለ ሃይማኖት ገድል ተገኝቷል።[97] በዚህ ገድል አባ እስጢፋኖስ በቀብ ቤተ ተክለ ሃይማኖት መሆኑ በግልጽ ሰፍሯል፤ በአቡነ ተክለ ሃይማኖት ስም የሚጠራ ቤተ ክርስቲያንም በገዳማቸው (ደብረ ገሪማ ጕንዳጕንደ ማርያም) ውስጥ አለ።[98] በተጨማሪም በገድላትና በመጽሐፈ መነኩሳት የተጠቀሱ ገናና ኢትዮጵያውያንና የውጭ ቅዱሳንን ስም በግብረ ሕማማት የብራና መጽሐፋቸው ማሳረጊያ በዝርዝር ያነሳሉ። እንዲህ እያሉ፡ "… አባ ዮሐንስ ከማ … ወአባ ተክለ ሃይማኖት … በረከቶሙ ወትንብልና ሳሕሎሙ፣ ወገድለ ጻማሆሙ፣ ወጸጋ ረድኤቶሙ፡ ወትረ የሀሉ ምስሌነ ለዓለመ ዓለም አሜን!… የአባ ዮሐንስ ከማ - የአባ ተክለ ሃይማኖት በረከታቸው፣ ልመናቸው፣ የገድላቸው የድካም ዋጋ፣ የትሩፋታቸው ጸጋ፤ ዘወትር ከኛ ጋር ይሁን፤ አሜን!"[99]

[96] (1) አቡነ ተክለ ሃይማኖት አቡነ መድኃኒነ እግዚእን፣ (2) አቡነ መድኃኒነ እግዚእ አቡነ ሳሙኤል ዘቈየጻን፣ (3) አቡነ ሳሙኤል ዘቈየጸ አባ እስጢፋኖስን፣ የእርሱ ተከታይ የነበሩትን አባ አበከረዙንንና አባ ይስሐቅን፣ (4) አባ አበከረዙን አባ ገብረ መሲሕን፣ አባ ይስሐቅ አባ ዕዝራን አመንኩሰዋል። (Taddesse Tamrat, p.104. እስጢፋኖሳዊው አባ መዝገበ ሥላሴ ያስጻፈው ያልታተመ ገድለ ተክለ ሃይማኖት፣ ቅጠል 147)

[97] http://digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3A5135#page/5/mode/2up : visited on Nov. 8, 2016. (ሥዕላቸውም በአባ መዝገበ ሥላሴ - ካልዕይ ወይም ሣልሳይ መዝገበ ሥላሴ - ገድል አለ።)

[98] Paul B. Henze, "A Visit toGundaGunde (Irob)", Feb, 1998, https://irrob.org/eco-tourism-in-iroblandvisit-to-gunda-gunde/

[99] ግብረ ሕማማቱን ተከታዩን የኢንተርኔት አድራሻ ተጠቅሞ ማየት ይቻላል http://www.ethiopianorthodox.org/amharic/holybooks/gibre%20himamat%20-%20Gunda%20Gunde.pdf : revisited Oct 27,2016





(T/C ታደሰ ታምራት ያቀረቡትን መነሻ በማድረግና ገድሎቻቸውን በማመሳከር ተሻሽሎ የቀረበ የእስጢፋኖሳውያን አበ ምኔቶች ሐረገ ምንኵስና)[100]

[100] (1)ይስሀቅ፣ (2)ገ/መሲህ፣ (3)ሀ/ሥላሴና (4)መዝገበ ሥላሴ በሙ ምክሼዎች አሏቸው፤ አበምኔቶቹ በተመሳሳይ ስም ቢጠሩም ከአንድ በላይ ናቸው።

## 2.7 እግረ መንገድ ገድላተ ደቂቀ እስጢፋኖስን ከዘመነኞቻቸው ጋራ እናነጻጽር

ደቂቀ እስጢፋኖስ ከዘመናቸው ጋራ ተቀራራቢ በሆነ ወቅት ከተነሡ መስተጋድላን ጋራ ማነጻጸር ከጀመርን ተጋድሎአቸውን እና ክርክራቸውን ጥቂት ገፋ አድርገን በንጽጽር እንየው፡፡ ንጽጽሩ በወቅቱ የነበረውን ጠንካራ ክርስቲያን የሆኑ ግን እምባገነን ነገሥታትና ከእነርሱ ጋር ያበሩ የተባበ ሐሳውያን ካህናት ደብተራ በአንድ ወገን ሆነው፤ በሌላው ወገን ደግሞ ጥብቅ የምንኩስና ሕይወት የሚከተሉ መነኰሳት ተሰልፈው ተጋድሎ ያደረጉበትን የመካከለኛው ዘመን የኢትዮጵያ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ለመረዳት ፍንጭ ይሰጠናል፡፡ እንደ እውነቱ ዘመኑ በኢትዮጵያ ብቻ ሳይሆን በዓለም አቀፍ ደረጃ ባለው ክርስትና ንውጽውጽታ የበዛበት ነው፤ የገዳማውያንና የነገሥታት ፍጥጫ በምዕራቡም በምሥራቁም ያየለበት ዘመን መሆኑን መረጃዎች ይጠቁማሉ፡፡ የራሳችንን ለመመዘን በደቂቀ እስጢፋኖስና በሌሎች መነኰሳት መካከል ንጽጽራችንን እንቀጥል...

(2.7.1) አፄ ዓምደ ጽዮን ዕቁባት ማብዛት አመጣ፡፡ ሦስት ሚስት አበጀ፡ ከሐሳውያን ካህናተ ደብተራ ወገንም ዘአማኑኤል የተባለው የወሰቃ መምህር "አንተ ንጉሥ ሆነህ በአንዲት ሚስት ልትኖር አትችልም፡፡ ለንጉሥ'ማ ሦስት ሚስቶችን ያገባ ዘንድ ታዞለታል ብሎ አሳሳተው፡፡" አባ ፊልጶስ ቀጣው ነደደ፡፡ ዘአማኑኤልን ይተገትገው ጀመር፡፡ እንዲህ እያለ "...ዘአማኑኤል ሦስት ሚስት በአንድ ጊዜ እንዲያገባ ለንጉሡ ታዟል አለ እንጂ ለሁሉም አላለም፤ በዚህም እግዚአብሔርን ፊት የሚያይ፣ ስለ መንግሥቱ (ንጉሡን) የሚፈራ፣ ድኻንም ስለ ድኽነቱ የተነሣ የሚንቅ አደረገው፡፡ በዚህም በአምላካችን ላይ ዋሸ፡፡ 'ለነገሥት ሦስት ሚስት ያገቡ ዘንድ ታዝዟል የሚለውን ከየት አገኘው?' ሕግ መሲሐዊት (ክርስቶሳዊት) ከተገለጠች በኋላ ከመጽሐፈ ኪዳን ነውን? ወይስ ከወንጌል፣ ወይስ ከሐዋርያት መልእክት፣ ወይስ ከእነርሱ ጋር ሱታፌ ካለው ልሳነ ዕፍረትም ከተባለ ጳውሎስ ነውን? ከዲድስቅልያ ነው? ወይስ ከመጽሐፈ ሲኖዶስ፣ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ከተቀበለቻቸው፡፡... የጽድቅ ቃላትን ከሚናገሩ መጻሕፍት ሁሉ ይኽንን ትእዛዝ ብንፈልግም አላገኘነውም፡፡... ከሐዲስና ከብሉይ ምስክር በዚህ ነገር



ላይ እናመጣ ነበር፤ ነገር ግን እንዳይረዝም ብለን ተውነው" ይላል፡፡[101] በተመሳሳይ አባ እስጢፋኖስ አባ ሲኖዳ ጋር በንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ የፍርድ አደባባይ ቀርበው ሲከራከሩ ሲኖዳ 'ለመነኰሳት ተብሎ የተለየ ሥርዓት አልተሠራም' ባለው ጊዜ "ለክርስቲያን ሁሉ በየሥርዓታቸው እንዲኖሩ በሲኖዶስ ተሠርቷል--ምእመናን በሚስቶቻቸው እንዲጸኑና ልጆቻቸውን በእውነት እንዲያሳድጉ፤ ካህናትም ለመኖሪያቸው እሥራትና በኵራት እንዲወስዱ አዟል፡፡ ይህ ለእናንተ ዓለምን በመተው ከጌታ ጋር ኪዳን ለገባችሁት መነኰሴዎች ምስክር ነው" ሲል ከአባ ፊልጶስ ጋር ተመሳሳይ በሆነ መልኩ መጽሐፈ ሲኖዶስን ጠቅሶ ይከራከረዋል፡፡[102]

(2.7.2) ንጉሥ ሠይፈ አርዕድ አባ ፊልጶስን "እኔ ከማልገዛው ምድር ልትደርስ ትችላለህን?" ባለው ጊዜ ሲመልስ "እኔስ ምድር የአንተ ሳትሆን የእግዚአብሔር እንደ ሆነች ዐውቃለሁ፡፡ ነገር ግን አባቶቼ ሐዋርያትን እመስላቸው ዘንድ ስደትን እቀበላለሁ" ይለዋል፡፡[103] ተመሳሳይ ጥያቄ ለአባ እስጢፋኖስ ከንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ቀርቦለት "ቤተ ክርስቲያን የታነጸችው በቅዱሳን ሐዋርያት ላይ እንጂ በምድር ንጉሦች ላይ አይደለም፡፡ ስለዚህ ሞገዶች በማያናውጹዋት ክርስቶስ በገነባልን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ እንኖራለን" ሲል ይመልስለታል፡፡[104]

(2.7.3) አባ ፊልጶስ ከሠይፈ አርዕድ "የቤተ ክርስቲያን ሹማምንት ሁሉ ከእኔ ጋር ተባበሩ፤ አንተ ብቻ ትእዛዜን ሳትቀበል ቀረህ" የሚል ቊጣ ደርሶበት ነበር፡፡ የአባ ፊልጶስ ምላሽ ግን "ፈርቼ ሕጉን ከኻርኩ'ማ የመጀመሪያው ገድሌን በከንቱ አደረግሁት፡፡ ...ዕርፍ ይዞ ወደ ኋላ የሚያርስ የለም [ሉቃ.9:62]" የሚል ነበር፡፡[105] በዚሁ መንገድ ለአባ እስጢፋኖስ ከካህናተ ደብተራ ጥያቄ ቀርቦለት ሲመልስ "...ጌታ ሕይወትን ስለ መውረስ ለጠየቀው ባለጸጋ 'ፍጹም ለመሆን ከፈለግህ ሒድና ንብረትህን ሁሉ ሽጠህ ለድኻ ሰጥተህ ና ተከተለኝ' [ማቴ. 19:21] እንዳለው ቅዱስ ወንጌል ምስክሬ ነው፡፡... ደግሞ ዕርፍ ይዞ ወደ ኋላ የሚሔድ የለም፤ ምክንያቱም መንግሥተ ሰማያት ቀጥታ ናት [ሉቃስ 9:62]" ይላል፡፡[106] በደቂቀ

---

[101] አራቱ ኃያላን፡ገ.268
[102] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.89
[103] አራቱ ኃያላን፡ገ.292 - 293
[104] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.110
[105] አራቱ ኃያላን፡ገ.291
[106] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.89

እስጢፋኖስ ገድል ውስጥ መክብዩንና ንግሥተ ማርያምን[107] የመሳሰሉ ጠንካራ መነኩሳዪያትንና እማሆችን እንደምናገኘው ሁሉ በአባ ፊልጶስ ገድል ውስጥም መክብዩ[108]ና አርኒ[109] የተባሉ ጽኑዓት መነኩሳዪያትን እናገኛለን።

(2.7.4) የደስክና የዲና ጣዖታት አምላኪዎችም ላመኑበት ሲሞቱ አይተናልና መሪር ስቃያን መቀበል ሁልጊዜም የዐላማ ትክክለኛነት ማሳያ ይሆናል ባይባልም በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ የደረሰውን ስቃያ እና ኢሰብአዊ ቅጣት ልናስተባብለው አንችልም። በመጠናቸው እነርሱ ላይ ከደረሱት ጋራ ይተካከላሉ ባይባሉም እጅግ መሪር ሊባሉ የሚችሉ ቅጣቶች በዚያው ዘመን ይተካከላሉ ... በተነሡ የመካከለኛው ዘመን መነኩሳት ላይም ደርሷል፤ ዲ/ን ዳንኤል ክብረት በ"ዐራቱ ኃያላን" ከገጽ 92-102 እንደ ተረከው። ለምሳሌ፡- አባ ፊልጶስ በሽመል ተወቅተዋል፤ ዕርቃናቸውን ተደርገው በጅራፍ ተገርፈዋል፤ የጺማቸውና የንፍረተ ሥጋቸው ጸጉር ተነጭቷል፤ ታስረዋል፤ ተግዘዋል፤ ከታሰሩ በኋላ እንደ ሮማውያን ግላዲያተር የተራቡ ውሾች ተለቀውባቸዋል። እነ አባ በጸሎተ ሚካኤል፣ አኖሬዎስ፣ አሮን፣ ተክለ ሐዋርያት፣ ሳሙኤል ዘደብረ ወገግ የነገሥታቱ የጭካኔ በትሮች ዐርፈውባቸዋል። የእነ አባ ቀውስጦስ የንጉሥ ዓምደ ጽዮን የሥጋ ዘመዶች መሆን ተግሣጽ በንጉሡ ላይ በሰነዘሩ ጊዜ 400 ግርፋት ከመቀበል፣ ጺማቸውን ከመነጨት፣ እጆና እግራቸው እንደ ድንኳን አውታር ተወጥሮ ከመታሰር እና በመጨረሻም ጎናቸውን በጦር ተወግተው የሰማዕትነትን ጽዋ ከመጎንጨት አላዳናቸውም።

(2.7.5) ሞትን በሚመለከት ንጽጽር ብንሠራ ደቂቀ እስጢፋኖስ በገጽ 221 እንደሚነግሩን በ"ደብ ጸር"[110] (አጼ ዘርዓ ያዕቆብ) እጅ ብቻ 1004 ደቂቀ

---

[107] ዝኒ ከማሁ፡ገ.142ና 132።
[108] "መክብዩ" የተባሉት መነኩሳዪያት በተለያየ ገዳም፣ በተለያየ ጊዜ፣ መጠነኛ ልዩነት ባለው ዐላማ፣ በተለያዩ መነኩሳት (በደብረ ሊባኖሱ አባ ፊልጶስና በጕንዳጕንዶው አባ እስጢፋኖስ)፣ በተለያዩ ነገሥታት (በአጼ ሠይፈ አርዕድና በአጼ ዘርዓ ያዕቆብ) የተሳደዱ ሁለት የተለያዩ ስመ ሞክሼ እኅትት ናቸው።
[109] አራቱ ኃያላን፡ገ.287።
[110] ገጸሙ ያስተመው ገድል "ደብ ፀር የአጼ ዘርዓ ያዕቆብ ስመ መንግሥት ነው" ሲል በተዘዋዋሪ ያስተባብላል። (አባ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዶ፡ገ.33፣ ኀዳግ ቁ.1።) ሆኖም "ደብ" የሚለው ቃል ከጅብ ነው የሚያያዘው። (ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፡ገ.335።) የዘርዓ ያዕቆብ የንግሥና ስም "ቈስጠንጢኖስ" መሆኑም ይታወቃል። ስለዚህ ቃሉን በበጎ ትርጓሜው ለመቀበል ይከብዳል።



እስጢፋኖሳውያን በንጉሡ የግድያ ትእዛዝና በግዞት አልቀዋል። በተመሳሳይ 128 የአባ አኖሬዎስ ተከታዮች፣ 500 የአቡነ አሮን ተከታዮችና በሺሕ የሚቈጠሩ የአባ ፊልጶስ ተከታዮች በአጼ ዓምደ ጽዮንና ሰይፈ አርዕድ ዘመን ሲያልቁ እንመለከታለን።[111] የመካከለኛው ዘመን የኢትዮጵያ ክርስትና እንደዚህ ነበረ። ነገሥታቱ ለቤተ ክርስቲያን ሁለንተናዊ ትንሣኤ እጅግ በመጣጣራቸው፣ አምልኮ ባዕድን በማክሰማቸው፣ ክርስቲያኑ ግዛት በሙስሊም ጅሐዲስቶች እንዳይዋጥ ከውጭም ከውስጥም ጠንክረው በመከላከላቸው እናደንቃቸዋለን። የምግባር ጉድለታቸውንና ኢክርስቲያናዊ ቅጣታቸውን ስናይ ደግሞ እንሸማቀቃለን። የሆነ ሆኖ፥ "ነገሥታቱ ካለፉ በኋላ እነ አባ አኖሬዎስ፣ ፊልጶስ፣ አሮን፣ ወዘተ ያለ ልዩነት በቅድስና ሲጠሩ ደቂቀ እስጢፋኖስን በሚመለከት ግን ለምን የተለያየ እሳብ ተራመደ?" ብለን መጠየቃችን አይቀርም። የእኔን አቋም ቀደም ሲል ስለ ውግዘትና ስግደት ሳነሣ ያንጸባረቅሁ ይመስለኛል።[112]

---

[111] አራቱ ኃያላን፡ገ.98፣287 እና 351
[112] በመሠረቱ በቤተ ክርስቲያናችን ቅድስና የሚሰጠው ተሠያሚው ሰው ያለ ህፀፀ ሃይማኖት መኖሩ ተረጋግጦ ፡- (1) ከዚህ ዓለም በሕይወተ ሥጋ ካለፈ፣ (2) በአገልግሎት፣ በሙያና በአስተዳደር ስለ ቤተ ክርስቲያን ክብር ከፍ ያለ ተጋድሎ ከተጋደለ፣ (3) በሃይማኖትና በምግባር ፀንቶ ጉልህ ትሩፋትን ከሠራ፣ (4) ስለ ቀናች ሃይማኖት መሥዋዕትነትን ከተቀበለ፣ (5) በእፍና በመጣፍ ምዕመናን ከመናፍቃን ከጠበቀ፣ (6) በምናኔ ለአገርና ለሃይማኖት ሲፀልይ ኖሮ ካለፈ፣ (7) በጾምና በጸሎት ዝጊረ ተአምራትን ማድረጉ ከተረጋገጠ ነው። ከ2-7 ያሉት ዝርዝሮች በማሳያ መልክ (illustrative) እንጂ አንድ ሰው ቅድስና ለማግኘት ሁሉንም ማሟላት አለበት ማለት አይደለም። ሰማዕት ወይም መናኝ ያልሆነም መናፍቃንን የሚረታና አማንያንን የሚያፀና/ የሚያጸናና ጽሑፍ ስላኖረ ብቻ ቅዱስ ሊባል ይችላል። ሰማዕት ከሆነ ደግሞ ቅድስና ለመስጠት ተአምር እስኪታይ ላይጠበቅ ይችላል።

በቅድስና ከተጠራ/ ከተሠየመ በኋላ፡- (1) ገድል/ ድርሳን/ ተአምር/ ይጻፍለታል፤ መልክእ ይደረስለታል፤ ስሙ በሥንክሳር ገብቶ ተጋድሎው ይነበባል። (2) "ንፍስ ይማር" ማለት ቀርቶ ይደረስለታል ... "ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን" ይባላል። (3) መታሰቢያ ቀን ይወሰንለታል። (4) ምንጊዜም "ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን" ይባላል። (5) ጽላት ተቀርጾ በሥሙ ቤተ ክርስቲያን ሥዕሉ በዐርሃን ከበብ ተደርጎ ይሣላል። (5) ጽላት ተቀርጾ በሥሙ ቤተ ክርስቲያን ይታነጽለታል። (6) አጽሙና ንዋየ ቅድሳቱ (አስኬማው፣ መቋሚያው፣ መቁጠሪያው፣ መጻሕፍቱ...) በክብር ይጠበቃሉ። እነዚህ በተቻለ መጠን ተሟልተው (exhaustively) ይፈጸማሉ። (ሰሎሞን የሐንስ (ዲያቆን)፣ የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ወርቃማ ዘመናት፣ 2001 ዓ.ም.፣ ገ.201-203። አራቱ ኃያላን፡ገ.56።)

በመጨረሻ የቅዱሱን ታቦት ለመባረክና ሕንፃ ቤተ ክርስቲያኑን በሚገን ለማክበር በፍትሐ
ነገሥት አንቀጽ 1 እንደ ተጻፈ ጳጳስ የግድ ስለሚያስፈልግ ያለ ጳጳስ እውቅና ቅድስና ይሰጣል
ብሎ ለመደምደም ባይቻልም በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ፀንቶ በኖረው ትውፊት ቅድስና በማዕከል ደረ
የሚሰጥበት ሥርዓት (canonization) የነበረ አይመስልም:: (Encyclopadia Aethiopica,
Volume 3, 2007, p.60.)

በምሥራቃውያኑ በኩል በቅዱሱ አማላጅነት ("እምላከ አከሊ" ተብሎ በተደረገ ተማኅ
የተደረጉ) ተአምራት ሲኖሩ፣ ቅድስናው በራዕይ ተደጋግሞ ሲገለጽ፣ ከመቃብሩ ምልክ
ሲገኝ፣ አስክሬኑን በመፈለስ ተደጋጋሚ ፈውስ ከተገኘ፣ ባረፈበት ቀን የተለየ ምልክት ወይ
ከወትሮው እጅግ የተለየና ሰፊ ቦታ ያካለለ መዓዛ ከሸተተ እንደ ቅድስና ምልክት ይታያል
የምሥራቅ እርቶዶክሳውያን የቅድስና አሰጣጥ እንደ ካቶሊካውያን ከላይ (ከሲኖዶስ) ወደ ታ
ከመሆን ይልቅ ከታች (ከምዕመኑ) ወደ ሲኖዶሱ በሚመጣ የገቢረ ተአምራት ማስረጃ ላይ
የተመሠረተ መሆኑ ይነገራል:: (Fr. Andrew Applegate, The Canadian Journal of
Orthodox Christianity Volume X, Number 1, Winter 2015 The Orthodox Church
Process of Canonization/Glorification, and the Life of Blessed Archbishop
Arseny. የምሥራቃውያኑ ነባር የቅድስና አሰጣጥ ሥርዓት እንደ ካቶሊክ "Canonization -
በቀኖና ሲኖዶስ ሳይሆን "Glorification - በተአምራዊ መገለጥ" ነው::

የኛ ሥርዓት ለምሥራቃውያኑ የሚቀርብ ሆኖ ይታያል:: እርግጥ በነሀድ ሃይማኖታቸው
መጠከረው ለተሠው ሰማዕታት ሲሆን በምሥራቃውያኑም ይሁን በእኛ በኩል ያን ያህል የተዘ
ተአምርና የጊዜ ገደብ ሳይጠበቅ በሲኖዶስ ውሳኔ ቅድስናቸው የሚታወጅበት ጊዜ አ
(የቅድስና አሰጣጡ ሥርዓት በሚገባ በጽሑፍ ተተንትኖ በማመሳከሪያ ሠነድነት ሊጠ
በሚችል መልኩ ባይቀመጥም) ለዚህ አባባል የቅርብ ማሳያ የሚሆነው የአቡነ ጴጥሮስ ሰ
ቴዎፍሎስ ሰማዕትነት በሲኖዶስ ውሳኔ የታወጀበት አጋጣሚ ነው:: (የአቡነ ቴዎፍሎስ በ
ሲኖዶስ "ሰማዕተ ጽድቅ" መሰኘት በዜና ጳጳሳት ኢትዮጵያውያን" ገጽ 60፣ የቅ
ምስክርነት" በተሰኘው የአባ መልከጼዴቅ አሳማሚና ዘለፋ የገነነበት መጽሐፍ ገጽ 66 -
ለማስተዛቀር ቢሆንም - ተጠቅሷል::)

የግብጽ ኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያንም ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ቅድስናን በሲኖዶስ ደረጃ እንደምታ
ምንጮች ይጠቁማሉ:: (Gawdat Gabra , et'al, The A to Z of the Coptic Church
The Scarecrow Press, Inc. Lanham • Toronto • Plymouth, UK 2009, p.57-58)

ካቶሊካውያን ቅድስና ለመስጠት ዐራት ዋና ዋና ደረጃዎችን ይጠብቃሉ:- (1) ተሠያሚ
ትሩፋት ከሠራበት ወይም መሥዋዕትነት ከተቀበለበት ሀገረ ስብከት ምዕመናን ለአ
ሀገረ ስብከት አስተዳደር ለእከሌ ቅድስና ይሰጥልን የሚል ጥያቄ ይቀርባል:: ሀገረ ስ
በማዕከላዊ ሲኖዶስ ፈቃድ ጥያቄውን መርምሮና በማስረጃ አንጥሮ ተገቢ ሆኖ
ለተሠያሚው "የእግዚአብሔር አገልጋይ - Servant of God" የሚል ማዕረግ ይሰጣል፡ (2
የሀገረ ስብከቱ ጳጳስ ስያሜውን ወደ ማዕከል ይልከዋል:: በማዕከላዊ ሲኖዶስ ዘጠኝ አ



(2.7.6) በአጠቃላይ በገድል አጻጻፍ ደረጃ የክርክሩ ጭብጥ ከመለያየቱ በቀር በደቂቀ እስጢፋኖስና "ዐራቱ ኃያላን" በሚል ስያሜ በአንድ ጥራዝ በወጡት በዐራቱ ገድላት ያለው አቀራረብ የተመሳሰለ ሆኖ ይታየናል:: ደጋግመው የሚጠቅሷቸው ጥቅሶች ማቴ.5:10፤ ማቴ.10:39፤ ማቴ.16:24፤ ማቴ.19:21፤ ማቴ.22:21 ሉቃ.9:23፤ ሉቃ.9:62፤ መጽሐፈ ሲኖዶስና ዲድስቅልያ እንዲሁም የቅዱስ ዳዊት መዝሙራትና የእነ አባ እንጦንስና መቃርስ የምናኔ ተጋድሎዎች ናቸው:: እነዚህ ጥቅሶች በቤተ ክርስቲያን ሊታወንት ስለ ምናኔ እና ምንኩስና በአስረጂነት ሊቀርቡ የምናውቃቸው ናቸው::[113] ገድላቸውን የሚጽፉበትን ምክንያትም የገድለ አበው ወእኃው ገድል ጸሐፊ በገጽ 221 ሲናገር "ይኸንን ለእኛና ከእኛ በኋላ ለሚመጡ ማስታወሻ እንዲሆን እንዳገኘነው ጻፍነው" ያለ ሲሆን በተመሳሳይ የአባ እኖሬዎስ ገድል ጸሐፊም "በምስክርነት ካልጻፍነና ካልተናገርን የሚመጣ ትውልድ በምን ያውቃል?... እኛ'ማ እንሞታለን፤ እንጣላለንም:: የሰው ልጅ ሁሉ እንደ ሣር ያልፋልና" ሲል ገድሉን ለመጻፍ ያነሣሣውን ምክንያት ይገልጻል::[114]

## 2.8. በውኑ ደቂቀ እስጢፋኖስ "መጽሐፍ ቅዱስ 'ብቻ' - Bible Alone" ባዮች ነበሩን?

ያሉት ጉባኤ ተቋቁሞ ተሠያሚው እንከለ ህፀፅ መሆኑን ባገኘ ( "devil's advocate" ይሉታል) እቁም ያጣራና ተገቢ ሆኖ ካገኘው "ክቡር/የተባረከ - Venerable" ይሰኛል:: (3) ሰማዕት ከሆነ ወዲያውኑ፣ መናኒ ወይም ትሩፋቱን በአገልግሎትና በትህርምት ያሳየ ከሆነ በእሱ አማላጅነት የታየ ተአምር መኖሩ ሲረጋገጥ "ብፁዕ - Blessed" ይባላል:: (4) ከብፅዕናው በኋላ በእሱ አማላጅነት (እምላከ እከሌ ተብሎ በተደረገ ጸሎት/ ልመና) ተጨማሪ ተአምር ከታየ በሊቀ ጳጳሳቱ (ፖፑ) ልሳን "ቅዱስ - Saint" ተሰኝቶ ቅዱሴ ቤቱ ይከበራል:: (http://www.catholichawaii.org/media/314379/canonization_4_steps_to_becoming_a_saint.pdf : October13, 2016. )

በደቂቀ እስጢፋኖስ በኩል ራሳቸውን በራሳቸው፣ ገና በቁማቸው "ቅዱስ/ ቅዱሳን" እያሉ ቢጠሩም፣ እሁንም አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቹ በቅድስና እንዲጠሩ የሚፈልጉ ጸሐፊዎች መኖራቸው ባይካድም፣ እስካሁን ባለን መረጃ ከእነሱ መካከል ቅዱስ ተብሎ ለቅድስናው የተቀረጸለት ታቦት፣ ወይም የታነጸለት ቤተ ክርስቲያን ቅዱሴ ቤት በፍትሐ ነገሥት አንቀጽ 1 መሠረት በይፋ በሊቀ ጳጳስ ሜሮን የከበረለት እባት ስለ መኖሩ አልሰማንም፤ አላየንም::

[113] መ/ብ አድማሱ ጀንበሬ፣ኩኩሐ ሃይማኖት፡ገ.44-46

[114] አራቱ ኃያላን፡ገ.325

(2.8.1) በአባ እስጢፋኖስ ገድል ገጽ 65 እንዲህ የሚል ቃል ሰፍሯል፤ "ነፍሱን በአምላክ መጻሕፍት ምስክራ በቆመች በጌታ ስምሪት አሰማራት። ከሰው ጠባይ የሚድንበት ውሳኔዎቻቸውንም መጠበቅ ያዘ። ቅዱሱ ለሚሠራው ሁሉ አስቀድሞ እበምኔቱን ይጠይቅና ፈቃድ ይወስዳል።" ፕ/ር ጌታቸው ይህን የገድሉን ጸሐፊ ገለጻ ሲተረጉሙት "Fundamentalist[115] የሚባሉት እንደሚያደርጉት መጽሐፍ የሚለውን ቃል በቃል መጠበቅና እንደ ትእዛዞቹ መሔድ ጀመሩ ማለት ነው" ይሉናል።[116] "Fundamentalist" የሚባሉት እንደ አባ እስጢፋኖስ "ዕርፍ ይዞ ወደ ኋላ የሚያርስ የለም" በሚል እጅግ የጠበቀ የምንኵስና ሕይወት ስለ መከተላቸው፣ ሰማንያ አሐዱ ቅዱሳት መጻሕፍትን፣ ፍና ሐዋርያትንና አሰረ አበውን ስለ መከተላቸው፤ "እምነት ያለ ምግባር ሙት ነው" ብለው በአበምኔት ፈቃድ ስለ ማደራቸው ግን ፕሮፌሰር አልነገሩንም፤ እኛም አላነበብንም።[117] እንደ እውነቱ የአባ እስጢፋኖስ አሳብ ፕሮፌሰር እንዳሉት አይመስልም።

(2.8.2) እርሱ የሚለው የመነኰሳቱ ገቢራዊ አኗኗርና መነኰሳት እንዴት በፍትሐዊ የመቁንን ክፍፍል እየተመገቡ ያለ ሐሜት መኖር እንዳለባቸው የተደነገገው ቀኖና አልተጣጣመም ነው። የጽሑፉን መንፈስ ለማግኘት ከኋላና ከፊት ዘለግ አድርገን እናንብብ፦

"...ማንንም በማዳላት አያመሰግንም፤ ማንንም በክፋት አያማም። ብቻ ሁልጊዜ በጸሎት ላይ ይሆናል። ሥራውን ሲጨርስ በማደሪያው ወይም በቤተ ክርስቲያኑ ውስጥ በብቸኝነት ይቀመጣል። ማታ የስብሰባ ምልክት ሲደውሉ ምግቡን ለመቀበል ወደ ማኅበራቸው ይሄዳል። እነሱ ግን የማኅበራቸውን

[115] ቅዱስ ትውፊት፣ አዋልድ መጻሕፍትና ትርጓሜ የማይቀበሉና መጽሐፍ ቅዱስ በደረቁ ቃል በቃል ብቻ መተርጎም አለበት የሚሉ የፕሮቴስታንት ቅርንጫፎች።

[116] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.65፤ጎዳግ ቁ.35

[117] ፕሮፌሰር ለንጽጽር የተጠቀሙበትን "Fundamentalist" የሚል ቃል በመግቢያቸው ካንጸባረቁት ደቂቀ እስጢፋኖስንና ማርቲን ሉተርን የሚያነጻጽር አተያይ በመነሣት፤ በገጽ 70፤ ጎዳግ ቁጥር 51 የደቂቀ እስጢፋኖስ መመሪያ ሐዲስና ብሉይ ብቻ እንደ ሆነ አድርገው ያቀረቡትን ማስታወሻ በመታዘብ ነው (ከተሳሳትኩ ለመታረም በተዘጋጀ ትሁት መንፈስ) ከፕሮቴስታንቲዝም አዛምደ የተረዳሁት። Fundamentalism በሁሉም ሃይማኖት ቢኖርም ብዙ ጊዜ ቅዱስ መጽሐፍ ቃል በቃል (literal) መተርጎም አለበት ብለው የሚያስቡ የፕሮቴስታንት ክንፎችን ለመግለጽ ነው የሚለውሰው። (Encyclopedia of Christian Theology, 2005, New York. London., p.599.)



ምግብ የማይበቃ ያደርጋሉ፤ አንዳንድ ጊዜ አንድ እንጀራ፣ አለዚያም ግማሽ እንጀራ ይሰጣሉ። ንፍሮ በሚቀቅሉበት ጊዜ የሁለት እጅ እፍኝ ወይም አንድ እጅ ሙሉ እፍኝ ይሰጣሉ። የራሳቸውን ምግብ ግን በማደሪያቸው እንደ ፈለጉ ያዘጋጃሉ። ይህ ቅዱስ ግን እዚያው ተኮልኩሉ የሰጡትን እንደ ቁርባን አንድ ጊዜ ይቀበላል። ብዙም ቢያገኝ ወይም ትንሽ ቢያገኝ እግዚአብሔርን ያመሰግናል። ስላሳነሱት አያጉረመርምም፤ ከሚያሙት ጋር አያማም። በዝምታ ወደ ማደሪያው ይመለስና የሥጋውን ፍላጎት እንዳይከታተል ሐሳቦቹን ይዘጋቸዋል። የማደሪያው ሰዎች ግን ግብር አበራቸው ባለመሆኑ አደሙበት። በቍጣም ዘለፉት። ነፍሱን ሊበጠብጡዋት ፈልገው 'ሁኔታው ሁሉ የሠይጣን ነገር ነው' እስከ ማለት ደረሱ። እርሱ ግን ምንም አይመልስላቸውም።... ቀጥሎ ከአንድ ጻማ ከለበሰ የቀሀ ሽማግሌ ዘንድ ሔደና እንዲህ ሲል ጠየቀው፦ 'አባ ስለ እግዚአብሔር ብለህ ንገረኝ፤ የእግዚአብሔር ፈቃድ እንደማያቸው ሰዎች ነው ወይስ የቤተ ክርስቲያን መጻሕፍት እንደሚሉት?' ሽማግሌው እንዲህ አለው 'የምታያቸው ሰዎች መታገሥ አቅቷቸው ሁሉም እንደ ጠባዩ ሔደዋል። እግዚአብሔር ግን በመጻሕፍት ውስጥ እንዳለው ቃሉ ነው።' ... በዚህ መልስ ለቅዱሱ ደስ አለው።... ነፍሱን በአምላክ ምስክራ በቆመችው በጌታ ስምሪት አሰማራት። ከሰው ጠባይ የሚድንበትን የመጻሕፍቱን ውሳኔዎቻቸውንም መጠበቅ ያዘ። ቅዱሱ ለሚሠራው ሁሉ አስቀድሞ እበምኔቱን ይጠይቅና ፈቃድ ይወስዳል።"[118]

ንባቡ አባ እስጢፋኖስ ቃሉን ከምግባሩ አጣጥሞ ባመነበት መንገድ በጽማዌ ለመኖር ያለውን ምኞትና በአንጻሩ በሌሎች ገዳማውያን ቀኖናን ከምግባር ያለማቀናጀት የፈጠረበትን ቅሬታ ነው የሚያሳየው።

(2.8.3) ፕ/ር ስለ የአባ እስጢፋኖስን ገድል በገጽ 70 "ሥራው መጻሕፍት መቅዳት ሆነ። ... ለማገልገል የሚሆነውን ከብሉይና ከሐዲስ እየወጣ ተረድቶ ... ቆመ" ብለው ከተረጎሙ በኋላ በጎዳግ ማሳታወሻ ቁጥር 51 ንባቡ

[118] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.64። አባ እስጢፋኖስ ቃልና ተግባር መጣጣም አለበት ብሎ እንደሚያምን "ልጆቹ ከውጣላቸው ቀኖና ጋራ ልባቸው በሚዛን ላይ እኩል እስኪሆን ድረስ ኑሮአቸው በቃልም በምግባርም ትክክል እንዲሆን" ደጋግሞ በመናገሩ ይታወቃል። ገድሉን ገጽ 96 ተመልከት።

“አባ እስጢፋኖስ የቤተ ክርስቲያን ትምህርታቸውን ያገኙት ከመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ እንደ ሆነ ለማሳየት የገባ አጻጻፍ ነው” ሲሉ ይደመድማሉ። ድምዳሚያቸው ትክክል ሆኖ አይታየኝም። ምክንያቱም፡- (1) አባ እስጢፋኖስ ስለ ምንኩስና በገጽ 81 ባደረገው ንግግር እንጦንስና መቃርስን መጥቀሱ መጽሐፈ መነኮሳትን ማንበቡን ያሳያል። ገዳሙ ያሳተመው ገድል “ወእምጽንዐ ነገሩ ለቅዱስ ኮኑ እስከ ይከህዱ መጽሐፈ ምንኩስና - ከመልሱ ጽኑዕነት የተነሣ በማፈር ምንኩስናን እንደማያውቁ ሁነው ካዱ”[119] ሲል የአባ እስጢፋኖስን መጽሐፈ መነኮሳት እውቀት ይነግረናል። መቼም በመጽሐፉ ባያምንበትና “መጽሐፍ ቅዱስ ‘ብቻ’ (Bible Alone)” ባይ ቢሆን መጽሐፈ መነኮሳትን ለክርክር ይጠቀማል ተብሎ አይጠበቅም። አባ እስጢፋኖስ የምንኩስና ሕይወትን ለመበየን መጽሐፈ መነኩሳት ቢጠቀስ ተገቢ ነው ብሎ ያምናል።[120] (2) ፕሮፌሰር በገጽ 70 “ሥራው መጻሕፍት መቅዳት ሆነ። ... ለማገልገል የሚሆነውን ከብሉይና ከሐዲስ እያወጣ ተረድቶ ... ቆመ” ብለው የተረጎሙት ቃል አጻጻፉ እሳቸው በኅዳግ ማስታወሻቸው እንደ ገለጹት ‘አባ እስጢፋኖስ የቤተ ክርስቲያን ትምህርታቸውን ያገኙት ከመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ እንደ ሆነ ለማሳየት የገባ አጻጻፍ” ሳይሆን ቀጥታ ከማቴዎስ ወንጌል ምዕራፍ 13 ቁጥር 52 የተገለበጠ ነው። የጕንዳጕንዶ ደብረ ገሪዛን ማርያም ባሳተመው ገድል ገጽ 61 የሰፈረው የግእዝና አማርኛው ንባብ “ወጸሐፈ መጻሕፍተ ... ወቆመ ተረሲዮ ውስተ ሀይቀ መርሶ ... እንዘ ያወጽእ እመዝገበ እግዚኡ ሐዲሰ ወብሉየ” - ከጌታው መዝገብ አዲሱንና አሮጌውን እያወጣ ትጥቁን አንግቦ በጸጥታ ቆመ” የሚል ሲሆን በዚሁ ገድል ኅዳግ ቁጥር 27 የተጠቀሰው የወንጌለ ማቴዎስ ንባብ “ጸሐፊ ዘይጸመድ ለመንግሥተ ሰማይ ይመስል ብእሴ በዓለ ቤት ዘያወጽእ እመዝገቡ ሐዲሰ ወብሉየ - ጻፊ ሁሉ ከመዝገቡ አዲሱንና አሮጌውን የሚያወጣ ባለቤትን ይመስላል” ነው የሚለው። በግእዙ ‘ሐዲሰ ወብሉየ’ ተብለው የተጠቀሱት ቃላት ፕ/ር እንዳሉት ቃል በቃል ሐዲስ ኪዳንና ብሉይ ኪዳንን ለመግለጽ

[119] አባ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዶ፡ ገ.73

[120] ባልታተመው ዜና ሞቱ ለአባ እስጢፋኖስ” ተቃዋሚዎቹ “መጽሐፈ መነኩሳትን በመስደ ከሰማንያ አሐዱ ውጭ ለምስክርነት የሚቆጠር መጽሐፍ (ዘይትጌሣሥ ለሰምዕ) የለም በማለታቸው “ናሁ ስምዕየ መጻሕፍት ወመጽሐፈ ምንኩስናሂ - ምስክሮቼም መጻሕፍት (ሰማንያ አሐዱ)ና መጽሐፈ ምንኩስና ናቸው” ማለቱ ተጽፏል። ይህ ነው “እስከ ይክህዱ መጽሐፈ መነኩሳት” ያሰኘው።



ሳይሆን ከመዝገብ (ሳጥን) የሚወጡ ዕቃዎችን አዲስነትና አሮጌነት ለመግለጽ የሰፈረ ተምሳሌታዊ ንግግር ነው። በምስጢር ሐዲስና ብሉይን ቢያጣቅስም አጻጻፉ የማቴዎስ ወንጌል ግልባጭ እንጂ የገድሉ ጸሐፊ አጻጻፍ ስላልሆነ “አባ እስጢፋኖስ የቤተ ክርስቲያን ትምህርታቸውን ያገኙት ከመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ እንደ ሆነ ለማሳየት የገባ አጻጻፍ ነው” እስከ ማሰኘት አያደርስም።

አባ እስጢፋኖስ የሚጽፈው አቡነ ሳሙኤል ለሚመሩት ደብረ ቊየጣ ገዳም እንጂ ለግሉ አልነበረም። መጻሕፍትን መገልበጥ በገዳሙ የተሰጠው የሥራ ድርሻ ነበር። ስለዚህ በገዳሙ ስር እስካለ ድረስ የሚባለውን ያህል በግሉ ሊከተለው የሚችል አጻጻፍ መኖሩ ያጠራጥራል።

(2.8.4) አባ እስጢፋኖስ “ሰንበታትንና በዓላትን በቅዱስ ሲኖዶስ ውስጥ እንደ ተጻፈ እያከበራችሁ... የሐዲስና ብሉይ... ምስክራ[121] ለመጠበቅ የተዘጋጃችሁ ሁኑ” በማለት ከነባሩ ትውፊትና ቍጥሩ ከሰማንያ አሐዱ ቅዱሳት መጻሕፍት ከሆነው መጽሐፈ ሲኖዶስ ጠቅሶ ሲያስተምር ፕ/ር ጌታቸው በኅዳግ ማስታወሻቸው “አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቹ መጽሐፈ ሲኖዶስን ከተቀበሉ ቅዳሜንም ያከብራሉ፤ ገድሉም ይመሰክራል። በመጽሐፈ ሲኖዶስ ያልተዘረዘሩትን መጻሕፍት ግን በሕግ ደረጃ የሚቀበሉ አይመስልም” ሲሉ ለደቂቀ እስጢፋኖስ በመጽሐፋቸው መግቢያ የሰጡትን ሉተራዊ ተዛምዶ ላለማናጋት የሚጥሩ መስለው ይታያሉ።[122] በወጉ በዓል የሚያከብርና መጽሐፈ ሲኖዶስን የሚቀበል ሉተራዊ አይተው የሚያውቁ ከሆነ መልካም ነው! መጻሕፍትን በሕግ ደረጃ ስለ መቀበል ከላይ በተራ ቍጥር 2.7.1 ከሰፈረው የአባ ፊልጶስ አነጋገር መረዳት እንደሚቻለው ኦርቶዶክሳውያን አባቶች እንኳንስ የሕግ መጻሕፍት በሚባሉት ዐሥራው (ሰማንያ አሐዱ) እና በሌሎች አዋልድ መጻሕፍት መካከል ያለውን ልዩነት መለየት ይቅርና ሐዲስና ብሉይ ያላቸውን አንጻራዊ ሥልጣንም ‘ምሳሌያዊት’ እና

[121] የፕ/ር ቋንቋ ነው፤ “መሰከረ” በግስ አረባቡ እንዲህ መሆን አለበት ብለው መሰለኝ፤ ለምሳሌ በዐራት የተለያዩ ፊደሎች በግእዝ ጀምሮ በግእዝ የሚጨርስ “ገበበ” የሚል ቃል ብንወስድ ስሙ ሲሆን “ግልበጣ” ይሆናል፤ ምንም እንኳን ቃሉ በዕለት ተዕለት መግባቢያነት የተለመደ ባይኾንም ፕ/ር የቋንቋ ሊቅ እንደ መሆናቸው ቃላቸውን ለማክበር እንዳለ እስተምጨዋለሁ።

[122] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.77፤የኅዳግ ማስታወሻ ቁጥር 74

'እማናዊት'፣ 'ብሉይ'ና ሐዲስ፣ 'የተሻረች'ና 'ፍጽምት'/ መሲሓዊት ሕግ እያሉ የከብራቸውን ደረጃ ደርድረው ተረድተው ነው የሚያስቀምጡት::

አባ ፊልጶስ የአጼ ዓምደ ጽዮንን ዕቀባት ማበጀት ኢመጽሐፋዊነት ሲነቅፍ "ከሐዲስና ከብሉይ ምስክር በዚህ ነገር ላይ እናመጣ ነበር፤ ነገር ግን እንዳይረዝም ብለን ተውነው" ማለቱን ቀደም ሲል ገልጸናል:: ስለ አባ ተክለ ሐዋርያት ሐዋርያዊ ስብከት "እክለ [ምግበ] ትምህርትን ለተራቡ ሰዎች ከብሉይና ከሐዲስ እየጠቀሰ ከመጻሕፍት ሁሉ እያጣቀሰ እያስተማራቸው እየመገባቸው ስምንት ወር ቆየ"[123] ይላል ገድላቸው:: አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫም ከአባ እስጢፋኖስ ጋር ፍጹም በሚመሳሰል ገለጻ "በይበልጥ ሐዋርያት በሲኖዶስ እንዳዘዙ ስለ ሁለቱ ሰንበታት አከባበር ይጠነቀቅ ነበር:: .. ስለ እነርሱም ከሐዲስና ከብሉይ በመሰብሰብ የድርሳን ቃላትን አስተካከለ:: በዓላትንም ሁሉ እንደ ሐዋርያት ሕግ በጥንቃቄ ያከብራል" ተብሉ ተጽፎላቸዋል::[124] ደቂቀ እስጢፋኖስ ጥንቆላን፣ ስር ማሽንትንና ሰውነትን መብጣትን፣ ... የመሳሰሉ አምልኮ ባዕዶችንና ልማዶችን ተቃውምን የሚሉትን ያህል መሳው የመካከለኛው ዘመን ቅዱሳንና ራሱ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብም ባዕድ አምልኮን ለማጥፋት የተቻላቸውን[125] ያህል ደክመዋል:: ኢክርስቲያናዊ ምግባራትን በመታገልና በመጻሕፍት አጠቃቀስ ረገድ በእነ አባ ፊልጶስ፣ በነ አባ ተክለ ሐዋርያት፣ በነ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ እና በደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላት መካከል መሠረታዊ ልዩነት አልታየኝም::

(2.8.5) ፕሮፌሰር በቡሩ ሜዳ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ የደረሰው መስተብቍዕ ዘማርያም ኑፋቄ አለበት ተብሉ ከቅዱሳት መጻሕፍት እንዲስማማ ተደርጎ

---

[123] ገድለ አባ ተክለ ሐዋርያት:ገ.48

[124] ገድለ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ:ገ.94

[125] እንዲያውም የዘርዓ ያዕቆብማ ለልጆቹ ጭምር ከተረፈ. መሪርና መደንገጽ ቅጣት ጋር ነው:: በዜና መዋዕሉ- ገላውዴዎስ፣ ዐምደ ማርያም፣ ዘርዐ አብርሃም፣ በትረ ጽዮን የተባሉ 4 ወንዶች ልጆቹና ድል ሠምረ፣ ርግ ገየላና አዳል መንገሣ የተባሉ 3 ሴት ልጆቹ፣ በድምሩ 7 ልጆቹ በባዕድ አምልኮ ታምተው ተገርፈዋል፤ በግርፋቱ የሞቱም አሉ:: (ዓለሙ ኃይሌ:ገ.1-3::) ይህ ያወጣውን ሕግ ለማንም ሳይለይ የመተግበር ቁርጠኝነቱ ንጉሡ ለሕግ ልዕልና ያለውን ታማኝነት ያሳያልና በዚህ ረገድ ለንጉሡ ክብር መስጠት የተገባ ነው:: አካልን በመብጣት፣ በንቅሳትና በውቅራት ስለሚከናዌኑ ልዩ ልዩ የባሕላዊና የአምልኮኘ ልማዶች አባ እስጢፋኖስ የተናገረውን ያህል አፄ ዘርዓ ያዕቆብም በአያሌው ጽፏል:: ጦማረ ትስብእት የተሰኘው ሥራው ይህንኑ ድርጊትና ሟርት ለመታገል የተደረሰ ይመስላል::



መስተካከሉን ነግረውናል:: እኛም በዚሁ ጉባኤ ሦስት ልደት ባዮች ተአምረ ማርያምን ለክርክራቸው ጠቅሰው ሲያቀርቡ ከሰማንያ አሐዱ ካልሆነ በቀር ለነገረ ሃይማኖት መከራከሪያ ተአምረ ማርያም ሊጠቀስ እንደማይገባ በአፄ ዮሐንስ ተነግሯቸው መረታታቸውን አንብበናል::[126] ቅሉ ይህ አባባል የመጻሕፍትን ደረጃ ከመጠቀም በቀር ተአምረ ማርያም ለማነወር እንዳልተነገረ ብናውቅም:: ስለዚህ በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ከሰማንያ አሐዱ መጻሕፍት ውጭ "የሕግ መጽሐፍ" ተብሉ መጽሐፍ ቅዱስን አኽሉ እና ተካክሉ የሚጠቀስ መጽሐፍ እንደ ሌለ የታመነ ነው:: T/C ጌታቸው ግን በመግቢያቸው ካስቀመጧት መደምደሚያ ፈቀቅ ሳለማለት ይመስላል ደቂቀ እስጢፋኖስን እንደ ሉተራውያን "መጽሐፍ ቅዱስ 'ብቻ' - Bible Alone" ባዮች ለማስመሰል ብዙ ርቀት ይጓዙና መልሰው ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ውስጡን በጽሙና የደቂቀ እስጢፋኖስን ተልእኮ እየተቀበለች በመሄድ ላይ እንደ ሆነች ይገልጻሉ::[127] ለዚህ አሳቸው "የማይቀረቁርና ሰላማዊ ተሐድሶ" ሲሉ ለሚጠሩት አሳብ ማሳያ የፈረደባትን መስተብቍዕ ዘማርያም ይጠቅሳሉ::[128]

(2.8.6) እንደ እውነቱ የእመቤታችንን መስተብቍዕ በሚመለከት የግንቦት 21 ቀን 1870 ዓ.ም. የቦሩ ሜዳ ጉባኤ "ወሰወልዳ" እና "ዘምስለ ወልዳ" በሚሉ ወገኖች መካከል ብይን መስጠቱ እውነት ቢሆንም ብይኑ የተሰጠው "ለእመቤታችን ስግደት ይገባል? አይገባም?" ከሚል እይታ ሳይሆን ከምስጢረ ሥጋዌ አንጻር ይመስላል:: አቋሜን ጥቂት ላብራራው:: ጸሐፊ ትእዛዝ ገ/ሥላሴ እንደሚሉት ጎጃሞች[129] "ላቲ ይደሉ ክብር ወስብሐት፣ ወምስለ ወልዳ አምልኮ ወስግደት... ለእርሱዋ ክብርና ምስጋና፣ ከልጇም ጋራ

---

[126] አቡነ ጎርጎርዮስ፣ የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ፡ ገ.73

[127] ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.24::

[128] T/C ጌታቸው የመስተብቍዕ ዘማርያምን የቦሩ ሜዳ የውግዘት ታሪክ በሦስት መጻሕፍቶቻቸው ጠቅሰውት አንብቤያለሁ:: በባሕረ ሐሳብ፣ በደቂቀ እስጢፋኖስና የሕይወት ታሪካቸውን በጻፉበት "እንዳፍታ ላውጋችሁ" ደጋግመው እንደሥተውታል::

[129] ትብዐቶች ለማለት ነበር፤ ሆኖም በእርሳቸው ቤት ጎጃም በሙሉ ትብዐት ነው መሰል! የጉባኤው ዐይነተኛ ሰው ዕጨጌ ቴዎፍሎስ ጎጃሜ መሆናቸውን እንኳ አላሰቡትም::ይህ ዓይነት አባባል በቀደምት ጸሐፊዎች የተለመደ ነው:: አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌም ቅብዐት ለማለት ጎጃምን፣ ጸጋ ለማለት ጎንደርንና ሸዋን፣ ካራ (ተዋሕዶ ነገ የምንለውን አይደላችሁም ለማለት የሚጠቀሙት ስድብ - ካራ!) ለማለት ትግራይንና ደብረ ሊባኖን በተለዋዋጭነት ይጠቀማሉ:: አጠቃቀሙ ጠቅላይነት ስላለው ለእኛ ዘመን አንባቢ ከበድ ሳይል አይቀርም::

እምልኮትና ስግደት ይገባታል" ይሉ ነበር። ቡድኑ "ዘምስለ ወልዳ" ይባላል። በእንጻሩ ከአክሱም እስከ በሽሉ[130] በአድባራቱ ሁሉ "ላቲ ይደሉ ክብር ወስብሐት፤ ወሰወልዳ እምልኮ ወስግደት... ለእርሱዋ ክብርና ምስጋና ይገባል፤ ለልጇም እምልኮትና ስግደት" ይባል ነበር። ይኼኛው ቡድን "ወሰወልዳ"[131] ይባላል። እንደ ጸሐፌ ትእዛዝ አባባል ጸጋዎች ከዚህኛው ወገን ናቸው፤ ምናልባትም እሳቸው እንደሚሉት ከጎጃም ውጭ ሌላው አገር ሁሉ "ወሰወልዳ" በሚለው ብሒል የጸና ነው። በመሆኑም ይህኛው ወገን ለጉባኤው ባቀረበው አቤቱታ መሠረት "ወሰወልዳ ይባል እንጂ 'ዘምስለ ወልዳ' ከተባለ'ማ መልሶ የጸጋ ልጅ መሆኑ አይደለምን?" ተብሎ ለጸጋዎች - በውስጠ ታዋቂ ከአክሱም እስከ በሽሉ ላሉ አድባራት - ተወሰነ።[132]

በጉባኤው "ዘምስለ ወልዳ" ከተባለ ይፋለሳል ተብሎ በዋናነት የተፈራው የእመቤታችን ክብር (ከሚገባው በላይ በአምልኮ ደረጃ) መግነን አይመስልም፤ እርሱ እግረ መንገድ ነው። በዚያ ጉባኤ ደረጃ ያሉ የጎጃም ሊቃውንት ፈጣሪና ከፍጡር ለይተው ሳያውቁ ለክርክር ይቀመጣሉ ብሎ መገመት የሊቃውንቱን የእውቀት ደረጃ ማሳነስ ይሆናል። እውነታው እንዲያ አይመስልም። የንባቡ ፍሰት እንደሚጠቁመው የተፈራው ጸጋዎች "እናትና ልጁን የጸጋ ልደት ያገናኘቻቸዋል" ስለሚሉ "ዘምስለ ወልዳ" ከተባለ ለእርሱዋ የሚሰጠው የጸጋ ስግደት በዚህ ንባብ ተሳስቦ እርሱን ወደ ጸጋ ልጅነት ብሒል ያመጣዋል ነው።[133] እንዴት እንደ ተረዱት ባይገባኝም የክርክሩ

[130] ወሎ ውስጥ የሚገኝ ወንዝ

[131] "ወሰወልዳ" የሚለው "ወላዋይነት"ን የሚገልጽ ስድብ ምናልባት የዚህ ንባብ ነቃፊዎች (የቦሩ ሜዳ ውጉዞ ዘምስለ ወልዳዎች) ያወጡት ይሆን? ደስታ ተክለ ወልድ ቃሉ በአማርኛ ጥቅም ላይ የዋለበትን ከግእዙ የተቃረነ ትርጓሜ ነቅፈው "እንዲት ሴት ስለቁ ማርያም 'ወሰወልዳ ናትና ስ(እ)ሰትሽን ለገርንቁ ማርያም (እንጎለላ/ ሽዋ) ስጪ' አለቻት ይላሉ፤ እንዲሁም ማለቷ ካህናቱን ስትሰድብ ነው።" ብለዋል። (ደስታ ተክለ ወልድ፡ገ.440።) ምላሴው፡- ብሒሉ ወደ ስድብነት ተቀይሮ "ወሰወልዳ" የሚባሉ አድባራትና ካህናት እንደ ነዙ ያሳያል - ምናልባትም ከ1870 ዓ.ም. በፊት በዋናነት ጸጋዎች ገንነው ይኖሩ በነበረበት በሸዋ!

[132] ጸሐፌ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ፤ ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ፤ 2008 ዓ.ም. ፡ገ.68

[133] እንደ ጸጋዎች አባባል፡- ጌታ በለበሰው ሥጋ (በትስብእቱ) የተነሣ ነቢይ፤ ካህንና ንጉሥ ተብሎ ለመጠራት በመንፈስ ቅዱስ ቅብዕነት ከአብ በግብር/ በጸጋ ተወልዶ በሦስተኛ ልደቱ "ወእነ የም ወለድኩከ" ተሰኝቷል። በዚህም የተነሣ ከአብና ከማርያም ከሆኑ ሁለት ልደታቱ በተጨማሪ በሰውነቱ እንደ እኛ "ዳግማይ እዳም፤ በኩረ ምዕመናን" ተብሏል። በዚህ አንጻር 'ዳግሚት ሔዋን እመቤታችን በሰውነቷ በመንፈስ ቅዱስ የጸጋ ልደት አግኝታለች።' በለዚህ እርሷ እንደ ሎጥ ልጆች (ዘፍ.19:30-38) ለልጇ ኢየሱስ ክርስቶስ በአንድ በኩል ወላጅ እናት፤



መንፈስ ከጸጋዎች ወርቃማ አገባብ ("ምስለ - ጋራ") የተቃረነ ሆኖ እየታየ ነው ውሳኔው ለጸጋዎች እንደ ድል ሲቆጥርላቸው የሚታይ። (አንድ ፍቁር ወንድሜ እንደ ነገረኝ) በሸዋ አንዳንድ የ"ዘምስለ ወልዳ"ን ብሒል ያልቀየሩ አድባራት[134] ዛሬ ድረስ ያሉ ይመስላልና 'ምናልባት ጥያቄው በጸጋ ብሒል ተቃዋሚዎች ተነስቶ ጸሐፌ ትእዛዝ ግን አሟዙረው በጸጋዎች ስም መዝገበውት ይሆን?' ሀቁን ለማንጠር እንዳይቻል ደግሞ ይህን የጉባኤ ንግግርና ውሳኔ ከእሳቸው ውጭ የመዘገበ አላጋጠመኝም። ስለዚህ ሌላ ማጣቀሻ እስኪገኝ ጽሑፉን በዚህ (ከዘርዓ ያዕቆብ ጋር ሳይሆን ከምስጢረ ሥጋዌ ጋር የሚያያይዝ) አንጻር ማየቱን እመርጣለሁ። ጥያቄው በጸጋዎች ነው የተነሣው የሚለውንም በምንታዌ (በተከፈለ ልብ) እየዋለሁ። ከገጸ ንባብ አወራረድና ከምስጢር (ትርጓሜ) አኳያ "ዘምስለ ወልዳ" ላይ በተዋሕዶዎች ካልሆነ በቀር በጸጋዎች ተቃውሞ የመቅረብ እድሉ አነስተኛ ነው።

(2.8.7) በሕገ መጻሕፍት አጠቃቀስ ረገድ ደቂቀ እስጢፋኖስ በወቅቱ ከነበሩት ሌሎች መስተጋድላን አበውም ሆነ በዘርዓ ያዕቆብ ወገን ከተሰለፉት

በሌላ በኩል (በጸጋ ከመንፈስ ቅዱስ በመወለድ እንዲሁ) እኅት ናት ይላሉ። እርሷም እርሱም ለባሲነ ሥጋ ስለሆኑ ከመንፈስ ቅዱስ ተወልደዋልና የአንድ የመንፈስ ቅዱስ ልጆች - እኅትና ወንድሞች - ናቸው እያሉን ነው! ለዚህም ደጋግመው የሚጠቅሱት ተከታዩ ሚጠየኑ ነው፡- "ዘዘርዐ እሉሆን ኮና፤ እኅተ ውሉዶን እኃት፤ እመ ወርኀ ሕፅፅ ወንትጋ፤
ለክለ እምላከ፤ ክርስቶስ ቀዳሚ ጸጋ፤
ወለተ ሐና ጠባብ፤ በመንፈስ ቅዱስ እኅትከ፤ እንዘ እምከ በሥጋ።"
ተዛማጅ ትርጉም፡- "(ሰው) በጎደለበትና ባነሰበት ወራት እንትማማቾቹ ከአባታቸው ዘር ተቀብለው የልጆቻቸው እኅቶች ሆኑ። የጸጋ ጀማሪ ክርስቶስ ሆይ! ላንተ[ም] ብልኋ የሐና ልጅ በሥጋ እናትህ ስትሆን ከመንፈስ ቅዱስ (ጸጋ) በመወለድ ግን እኅትህ ናት" ማለት ነው። (ኪዳነ ወልድ ክፍሌ መዝገበ ቃላት፡ገ.610። )
የቅኔው ምስጢር፡- ከላይ እንደተገለጸው ከሎጥና ከሴት ልጆቹ ታሪክ ይዛመዳል። ቅኔው የክርስቶስን የባሕርይ ልጅነት፤ ክህነት፤ ነቢይነትና ንግሥና ከአባትና እናት የዘርና የደም ተከፍሎን ከሚሻ ልደት፤ የሚክን ጳጳስ ወይም ሊቀ ካህናትን ከሚሻ የፍጡራን ክህነት፤ እንጋሽን ከሚፈልግ ዓለማዊ ንግሥና ጋር የሚያምታታ እጅግ ሕፁፅና ውጉዝ ማገጻሪያ ነው ተብሎ ይተቻል። ስለሆነም በቦሩ ሜዳ ጉባኤ "ዘምስለ ወልዳ እምልኮ ወስግደት" የሚለው መስተብቁዕ "ወሰወልዳ እምልኮ ወስግደት" በሚል የተተካው በዋናነት ፐ/ር በሚገልጹት የደቂቀ እስጢፋኖስ ተልእኮ ፈጻሚነት ሳይሆን "ዘምስለ/ ጋራ" በሚለው እያያዥ አገባብ 'ልጁ ከእናቱ ጋራ በጸጋ ልጅነት ይገናኛል' እንዳይባል ተፈርቶ ይመስላል።

[134] በመርሐ ቤቴ ውስጥ "ደለማ ማርያም" የምትሰኝ ደብር ካህናት እሁን ድረስ "ዘምስለ ወልዳ" የሚለውን ብሒል ያፀኑ ናቸው የሚል መረጃ አለ።

ተከራካሪዎች የተለየ አቋም ነበራቸው ለማለት የሚያስችል ተጨባጭ መረጃ የለም። ለምሳሌ፦ ንጉሡ አባ እስጢፋኖስን ሲጠራው "ላገኘህና 'በሕጉ ፊት' መሠረት ሁሉንም ለእግዚአብሔር ላስተካክል እወዳለሁ" ነው ያለው::[135] በጥሬው መሠረት ከመጣም በኋላ እንዳይሔድ ሲያስጠነቅቀው "ጉባኤ አድርጌ አንተ እንዳልከው ሁሉንም በመጻሕፍት ሕግ እስካስተካክል ድረስ እንድትቆይ፤" ብሎት ነበር::[136] በገጽ 147 ንጉሡ "የኢትዮጵያን ሃይማኖት ለምን ለሁለት ትከፍላላችሁ? አሁንም እኛ ዘንድ የጎደለውን እናንተ እየሞላችሁ፤ እናንተ ዘንድ የጎደለውን እኛ እየሞላን 'በመጻሕፍት ይወሰን'" ብሎ ነው የሰበሰባቸው:: ሃይማኖታችሁን "ሐዲስና ብሉይ እየጠቀሳችሁ አስረዱኝ!" እንዳላቸው ራሳቸው በገጽ 128 ጠቅሰዋል:: ዘርዓ ያዕቆብ የአባ እስጢፋኖስን ተከራካሪዎች "በመጽሐፍ ልትከራከሩት ትወዳላችሁን? የአባቶቻችሁ ምስክርነት ማስረጃ ሊሆናችሁ አይችልም፤ ማስረጃችሁ ከመጽሐፍ ይሁን" ነው ሲላቸው የነበረው::[137] ንጉሡ ያለውን ግልጽ የመጽሐፍ ዕውቀት ላወጣው ለንጉሥ የሚገባ የስግደት ዐዋጅ ማስፈጸሚያ ለማዋል ሲል በገጽ 109 በብሉይ ኪዳን አብርሃም ለኬጢ ልጆች (ዘፍ. 23፡7) ያደረገውን ስግደትና ያዕቆብም ለዔሳው (ዘፍ. 33፡3) ያደረገውን ይጠቅስበታል:: በዚህ ጊዜ አባ እስጢፋኖስ " ... በኦሪት ለሱ ብቻ ካልሆነ ለሌላ እንዳንሰግድ ቢቃሉ አዞናል" ይላል - የዘርዓ ያዕቆብ ማስረጃ በራሱ ከኦሪት የቀረበ መሆኑን ችላ ብሎ! እዚህ ላይ አባ እስጢፋኖስ ለንጉሡ ከአክብሮት (ከእጅ መንሳት - እማኄ) ውጭ ለእግዚአብሔር ወይም ለእመቤታችንና ለመስቀል በሚደረግ የጸጋ ስግደት ዐይነት ሊሰገድለት አይገባም ቢል ክፋት አልነበረውም:: እሱ ግን ጠቅልሎ "ኢትስግድ ለሙ ወኢታምልኮሙ" በሚል ለፈጣሪ የሚደረግን ከአምልኮ ጋር የተሰናሰለ የባሕርይ ስግደት ተፈጻሚነት ለጸጋ ስግደትም ሰጥቶ ተርጉሞ መላውን የጸጋ ስግደት ሲጋፋ ይታያል:: ይሄ ደግሞ "የመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ባይነት ፕሮቴስታንታዊ አዝማሚያ ሳይሆን በትርጓሜ መኖር የተማመኑ ሰዎች የአተረጓጎም መለያየት ነው:: ሁለቱም የሚጠቅሱት መጽሐፍ ቅዱስ ነው፤ ዘርዓ ያዕቆብን መውቀስ ካለብን በተግባሩ እንወቅሰዋለን እንጂ የራሳቸው

[135] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.92
[136] ዝኒ ከማሁ፡ገ.96
[137] አቡነ እስጢፋኖስ፤ዘፖንዳትዶ፡ገ.119:: ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.94::



ገድላት እንደሚመሰክሩት እነርሱ ያልተቀበሉትን ሕግ ጠቅሷል ብለን ለማማት መነሻ የለንም:: ከፋም ለማም እርሱም "ጉና በሕጉ ተፃፎ" ነው ያለው:: እንደ ሕጉ ሐዲል/ አልሐደም? ሌላ ጥያቄ ነው:: በጥሬው መሠረት እየቀረቡ ባደረጓቸው ክርክሮች በትርጓሜ ባይስማሙም ሁለቱም ወገኖች በዋናነት ሰማንያ አሐዱን መጽሐፍ ቅዱስ ነው የሚጠቀሙት:: ማሳያ ካስፈለገ በገጽ 88፣ 185፣ 186 እና ከ294-297 ያሉ ጥቃት ክርክሮችንና ምልልሶችን መመልከት ይቻላል:: ዘርዓ ያዕቆብ ለሰማንያ አሐዱ ቀኖና መጻሕፍት ያለውን ታማኝነት ራሳቸው ፕ/ር ወደ እንግሊዝኛ በተረጎሙት ጦማረ ትስብእት የተሰኘ ድርሰቱ "O children of the Gospel, do not accept [secret], reading names which you do not found in the eighty-one canonical books - ውሉደ ወንጌል ሆይ! በሰማንያ አሐዱ ቀኖና መጻሕፍት ውስጥ የማይገኙ ኅቡዐት [የተሰወሩ] የምድጋም [ድግምት] ስሞችን አትቀበሉ"[138] ማለቱን አስነብበውን ነበር:: በአጠቃላይ በእኔ ንባብ መሠረት እልፎ እልፎ በትርጓሜ አለመጣጣም ከመከሰቱ በቀር በመጽሐፍ ቅዱስ ይዘትና በአዋልድ አጠቃቀስ (አቀባበል) ዙሪያ የተነሣ አለመግባባት በገድላተ ደቂቀ እስጢፋኖስ ውስጥ አልተመዘገበም:: ባልተመዘገበ ቃል ብይን መስጠት ደግሞ አያስኬድም! ፕሮፌሰር የዘርዓ ያዕቆብ ድርሰት በተለየ መልኩ ተነጥሎ ጥያቄ ሲነሣበት እንደ ኖረ አድርገው በመግቢያቸው ገጽ 27ና 28 ማቅረባቸውም የመፍቀሬ ደቂቀ እስጢፋኖስ ዝንባሌ ማሳያ ሆኖ ይታየኛል:: በየዘመናቱ በአገራዊ ድርሰቶች ላይ እልፎ እልፎ ጥያቄ ሲነሣ አብሮ ተነሥቶበት እንጂ ለብቻው የእሱ ድርሰት ተነጥሎ የተጠየቀ አይመስለኝም::[139]

[138] Bulletin of the School of Oriental and African Studies, University of London, Vol.43,No.2(1980)., Getachew Haile, A Preliminary Investigation of the "Tomara Tassb't" of Emperor Zar'a Ya'ekob of Ethiopia, pp.207-234
[139] በዐሥራው (ሰማንያ አሐዱ) መጻሕፍት ቁጥር ላይ፣ በቅኔ ላይ፣ በቅዱስ ያሬድ ዜማ፣ በአባ ጊዮርጊስ ሰዓታት፣ በማኅሌተ ፅጌ፣ በሃይማኖተ አበውና በዘርዓ ያዕቆብ ድርሰቶች ለአገልግሎትና ለትሩፋት መዋል ዙሪያ በአፄ እስክንድር፣ በአፄ ሱስንዮስና በዘመነ መሳፍንት ክርክሮች ነበሩ፤ በየጊዜው እልባት ተሰጥቷቸዋል:: (የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 7፡ገ.98:: ድርሳነ ዑራኤል ዘሐምሌ፡ገ.305-307:: መጽሐፈ ትዝታ ዘአለቃ ለማ ኃይሉ፡ገ.103-106::የድጓ መቅድም፡ገ.2::)

# ምዕራፍ ሦስት

## እንቅስቃሴውን ፖለቲካዊ ትርጓሜ መስጠት

ስጀምር የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ "ለትርጉም የተመቸ ነው" ብዬ ነበር። የሆነውም እንዲያ ነው። የደቂቀ እስጢፋኖስን ሰቆቃ መብዛት ፕ/ር ጌታቸው ኃይሌ በወቅቱ የገነነውን ዓለማዊነት የተጫነው ምንኩስና ለመታገል ከተደረገው ጥረት ጋር ያይዙታል፤[1] መ/ር ካሕሳይም የፕ/ር ጌታቸውን አሳብ በመጋራት ከንጉሡ አምባገነንነትና መፍቀሬ ሥልጣን መሆን ጋራ ያቆራኙታል።[2] ፕ/ር ታደሰ ታምራትም ተመሳሳይ አሳብ ያላቸው ይመስላሉ።[3] ፕ/ር መስፍን ከንግግር ነጻነት ነፋጊነትና ከማሰብ ነጻነት ጋራ

[1] አባ እስጢፋኖስ ተቃውሞና ክስ የተነሣበት፦ መጀመሪያ ከብዙኃን ገዳማውያን አበው፣ ከ[illegible] ከአበ ምኔቱ አባ ሳሙኤል፤ በመቀጠል ከየአድባራቱ ሲሆን ነገሥታቱ ፊት መቅረብ የጀመረው በኋላ ነው። ስለዚህ ከመነሻው የተሳሳተ ሃይማኖታዊ አካሄዱን በቅጣቱ መሪርነትና በ[illegible] ደብተራ ድክመት ሸፍነን እንዳናሳልፍ መጠንቀቅ ያስፈልጋል። የአባ እስጢፋኖስ የመጀመሪያ ተቃዋሚዎች ገዳማውያን እንጂ ካሕናተ ደብተራ አልነበሩም። ይህን ለመረዳት በ"ገድለ እስጢፋኖስ" መጽሐፍ በተመዘገበ ገድሉ ከገጽ 70-82 ያሉ ምንባባትን በጥልቀት መመልከት ያስፈልጋል። ፕ/ር ታደሰ ታምራትም ይህንኑ አፈንጋጭነቱንና ከሽሬ አካባቢ ገዳማውያን ጋ[illegible] አለመስማማቱን ከላይ በተጠቀሰው ጽሑፋቸው ከገጽ 105-109 አስፍረውታል።

[2] መምህር ካሕሳይና ፕ/ር ጌታቸውን ከአንዳንድ ወንድሞቼ ጋር ስናወጋ እንዲህ እያልን እናማቸዋለን። - ሁለቱ መፍቀርያነ ትውፊት አበው አሁን ባለው የምንኩስና ሕይወትና የጵጵስና ሥርዓት ደስተኛ አይመስሉም። መ/ር ካሕሳይ "ምንኩስና በኢትዮጵያ ዛሬ ትናንትና" በሚል መጽሐፋቸው እና "ብፁዐን እነ ማን ናቸው?" በተሰኘ መጽሐፋቸው አሁን ያለውን የምንኩስናና የጵጵስና ሕይወት በምሬት ይነቅፋሉ። ፕ/ር ጌታቸው ግለ ታሪካቸውን በጻፉበት መጽሐፍ አሁን ያለውን የሲኖዶስ አደረጃጀት፦ "ሲኖዶስ በአንድ በኩል መንፈሳዊ ጉዳዮችን የሚያይ የአበውና የሊቃውንት ጉባኤ ሲሆን፤ በሌላ በኩል ቤተ ክርስቲያን የተከታዮቿ (የምዕመናንና የካህናት) መሆኗን ያሳያል። ጳጳሳቱ … ሲኖዶስን … የሊቃነ ቤተ ክርስቲያን የምትተዳደርበት ፓርላማ አድርገውት አባላቱን በእነሱ ብቻ ወስነውታል። [illegible] የቤተ ክርስቲያን ሥልጣን ነጥቆ መያዝ ነው። ቤተ ክርስቲያን በዚህ ሕግ ከተዳደረች [illegible] ምዕመን 'በቤተ ክርስቲያን ጉዳይ ምን አገባህ?' ሊባል ነው፤ ተብያለሁም።" እያሉ ያማርራሉ። (ጌታቸው ኃይሌ፤ አንዳፍታ ላውጋችሁ፤ 2ኛ እትም፤ 2006 ዓ.ም.፤ ገ.250።)

ከዚህ አንጻር የመ/ር ካሕሳይና የፕ/ር ጌታቸው ለእስጢፋኖሳውያን የሚደረግ የተጋነ አድናቆት በቅርብ ጊዜያትና በአሁን ዘመን ባለው ከተሜነትና መለካዊነት የሚፈታተነው የምንኩስናና የጵጵስና ሕይወት ደስተኛ ካለመሆንም ሊመነጭ ይችላል - ነገሩ ቅኔም አለው እያልን እናማቸዋለን። ብቻ ሐሜት ነው!

[3] "Zer'a-Ya'qob was deeply concerned with the movemnet in the political sense — ዘርዓ ያዕቆብ የሚብሰለሰለው በእንቅስቃሴው ፖለቲካዊ እንድምታ ነበር" ይላሉ (Taddesse Tamrat, p.112.)



ያይዙታል፤ Maimire Mennasemay የተባሉ ጸሐፊ "The Dekike Estifanos: Towards an Ethiopian Critical theory" በሚል ርእስ ከማኅበረሰባዊ ሒስ (በእርሳቸው ቋንቋ "ሐተታ") ጋር አገናዝበው ለእኔ የማፈጠኝ ውብና በተለየ አንጻር የቀረበ ዳሰሳ አድርገውበታል።[4] አቡነ ጳውሎስና ክሪስቶፍ ብላስዊዝ (Krzysztof Piotr BŁAśEWICZ) የተባሉ በደቂቀ እስጢፋኖስ እንቅስቃሴ ዙሪያ ሁለተኛ ዲግሪያቸውን የሠሩ ፖሊሽ (ፖላንዳዊ) የሥነ መለኮት (ቲዎሎጂ) ሊቅም የደቂቀ እስጢፋኖስን መሳደድ ወደ ፖለቲካዊ ትርጓሜው አድልተው አይተውታል። ዶናልድ ሌቪን እንዲሁ በ"ታላቋ ኢትዮጵያ" መጽሐፋቸው ገጽ 110 እንቅስቃሴውን "መንግሥትና ሃይማኖት እንዲለያዩ የተደረገ እንቅስቃሴ" አድርገው አቅርበውታል። የሁሉንም አሳብ ማስፈር ባይቻልም የተወሰኑትን በስሱ እንያቸው።

(3.1) "Filsata: The Feast of the Assumption of the Virgin Mary and the Mariological tradition of the Ethiopian Orthodox Tewahido Church" በተሰኘ የዶክትሬት ማሟያ ጥናታቸው ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ "...It seems that much of their opposition was politically motivated, directed at the claims of the Solomonic dynasty - የተቃውሞው እንቅስቃሴ ከሰሎሞናዊ ሥርወ መንግሥት የተገናኘ ፖለቲካዊ መነሾ ያለው ይመስላል" ሲሉ የደቂቀ እስጢፋኖስን እንቅስቃሴ ሰሎሞናዊ የንግሥና ሥርዓትን ከመቀበልና ካለመቀበል ጋር እያይዘውታል።[5] አባታችን አቡነ ጳውሎስ እንቅስቃሴውን "ኢትዮጵያዊ ልዩነት /Ethiopian Divergence/" በሚል ርእስ ሥር "አፈንጋጭ ኦርቶዶክስ /heterodox/"[6]

[4] Maimire Mennasemay, The Dekike Estifanos: Towards an Ethiopian Critical theory January 22, 2013 ethiopiawinote ወይም https://ethiopiawinote.wordpress.com/2013/01/22/the-dekike-estifanos-towards-an-ethiopian-critical-theory/ : revisited 26 Oct, 2016

[5] Aba Paulos; p.262

[6] የደቂቀ እስጢፋኖስ የመነሻ እንቅስቃሴ በመግለጽ ረገድ እስካሁን ተስማሚ ሆኖ ያገኘሁት "አፈንጋጭ ኦርቶዶክስ/ heterodox" የሚል ቃል ነው። ቃል አቡነ ጳውሎስ የተጠቀሙት "አፈንጋጭ ኦርቶዶክስ/ heterodox" የሚል ቃል ነው። የምሥራቅ ኦርቶዶክሳውያንና ካቶሊካውያን በተወሰነ መልኩ ከሃይማኖት ያፈነገጠን እምነት ለመግለጽ "አፈንጋጭ ኦርቶዶክስ /heterodox/" የሚል ቃል ይጠቀማሉ። ቃሉ "ኢ-ኦርቶዶክሳዊ/ unorthodox" ከሚለው የከረረ ተቃርኖን ገላጭ ቃል የለዘበ ነው። (http://www.newworldencyclopedia.org/entry/Heterodoxy : 25 October, 2016.) ብቻ እንጂ ከውጉዛን እርግጥ በእነሱ heterodox የሚባል ሰው ብዙ ጊዜ ቀጥሎ ከአፈንጋጮች

በሚል ቃል ሰይመውት ሲያበቁ 'ደቂቀ እስጢፋኖስ ሰጥ ለጥ ብለው ለንጉሡ አለመገዛታቸው ሃይማኖታዊና ፖለቲካዊ አንድነትን መሠረት ያደረገ ግዛት ለመመሥረት ቀርጦ በተነሣው አፄ ዘርዓ ያዕቆብ አደባባይ ቅጣታቸውን እንዲከበደባቸው' ይከራከራሉ::[7] መ/ር ካሕሳይም ይኼንኑ አሳብ ያጠናክራሉ::[8] አቡነ ጳውሎስ ከመ/ር ካሕሳይ ለየት የሚሉት ደቂቀ እስጢፋኖስ የቀደምት አይሁዳውያን ክርስቲያኖች ቅሪቶች ሳይሆኑ አይቀርም የሚለውን የቤተ እስራኤል ታሪክ ጸሐፊዎች አስተሳሰብ ወደ መቀበል በማዘንበላቸው ነው:: እርሱን ወረድ ብዬ እመለስበታለሁ::

(3.2) ካቶሊካዊው የነገረ መለኮት ሊቅ Krzysztof Piotr Blasewicz በተመሳሳይ የደቂቀ እስጢፋኖስ መከራ መብዛት ከሃይማኖታዊ መነሻው ይልቅ ጠኀሆናተ ደብተራ የብልጽግና ኑሮ ላይ ባነሡት ተቃውሞ፤ ከሚከተሉት በራስ የድካም ፍሬ የማደር[9] የጠበቀ የምንኵስና ሕይወት፤ ከጥብቅ የመጽሐፍ ንባብቸውና ያነበቡትን ለመኖር በሚያደርጉት ጥረት፤ ከበዓታቸው እየወጡ በመስበካቸውና ለንጉሡ ባለመስገዳቸው ፖለቲካዊ ይዘት ሊኖረው እንደሚችል ሲተርኩ፡- "The persecution which they experienced were most likely caused by the fact that they refused to pay heed to the ruler reserving it exclusively for God and the unfavourable attitude of the fast becoming rich clergy for their reforming activities such as: living from the work of one's own hands, sharing the crops with the ones in need, emphasis on study and observation of the laws of the Holy Scriptures, propagating their ideas beyond the walls of the monastery and

---

አይደለም:: በእኛ ቤት ካለው ካራዊ ፈተና አንጻር በበዓላትም ሆነ በሥርዓታት አከባበር ረገድ ውግዘታችን ጠበቅ ያለ፤ ፈጣንና የማያወላዳ ይመስላል:: በመሆኑም ደቂቀ እስጢፋኖስ ፕሮቴስታንትና ይሁዲ እንዲልነበሩ ለመግለጽ heterodox ቢባሉም ነገር ግን ውጉዛን ነበሩ::

[7] Aba Paulos, p.263

[8] ካሕሳይ፡ገ.52

[9] ከሥልጣን ሽሽት በድካም ፍሬ ማደርና መንኖ ጥሪት ከደቂቀ እስጢፋኖስ እሴቶች ውስጥ ናቸው:: (ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.76፤ Taddesse Tamrat, 106.::) እሴቶቹ የእነርሱ ብቻ ሳይሆኑ የሁሉም የመከከለኛው ዘመን ታላላቅ የካህናት ደብተራ ተቃዋሚ ገዳማውያን እሴቶች ናቸው:: (አረፋ ኃያላን፡ገ.102-103::) እርግጥ ወደ ኋላ ላይ የእስጢፋኖሳውያን ገዳማት እነ ጉንዳጉንዲ ደብረ ገሪዛን ማርያም ከጎንደር ዘመን ነገሥታትና ከመሳፍንቱ (በተለይም ከደጃች ሰባጋዲስ ጋር) ቅርርብ ፈጥረው ጉልት (የእርሻ መሬት) እስከ ማግኘትና ቅፈሮችን (ሌሎች የገጠር አድባራትን በሥሪቸው አድርገው) እስከማስተዳደር ደርሰዋል:: (Encyclopedia Aethiopica, Volume 4, p.748.) እስከ አፄ ኃይለሥላሴ ድረስ ከዘፋኑ ይቀራረቡ ነበር::



charismatic personalities endowed upon them - የደረሰባቸው ስቆቃ ሰጊድ ለእግዚአብሔር ብቻ ነው ብለው ለንጉሡ እጅ ካለመንሳታቸውና በፍጥነት ወደ ብልጽግና እየተመነደጉ የነበሩትን የቤተ ክህነት ሰዎች በመቃወም በላባቸው ብቻ ማደርን፤ ካገኙት ሲላይ ለነዳያን ማካፈለን፤ ሕገጋተ መጻሕፍትን ማጥናትና መጠበቅን፤ እምነታቸውን ከገዳማት ቅጽር ባሻገር ማስፋፋትንና ባለ ግርማ ሞገስ (ጥቡዐን/ ዕጉሠን) አበው ማፍራትን መነሻ ያደረገ የመሆን እድሉ ሰፊ ነው" ብለዋል::[10]

(3.3) በዚህ ጎራ ያለውን አስተሳሰብ ሙሉ ለሙሉ መካድ ኢፍትሐዊ ይሆንብኛል:: ጥቂት ከበርቴ ካህናተ ደብተራ[11] በንጉሡ ዙሪያ መኖራቸው እውነት ነው:: ንጉሡ ለሥልጣኑ ያለው ቀናኢነት ልጁና ሚስቱ ላይ ሳይቀር ለመጨከን የሚያስችለው ነበር፤ መንግሥቱን ለመገልበጥ አሲራችኋል ሲል ሚስቱን አስገርፎ አስገድሏል፤ ለእናቱ ተገቆርር መባዕ ያስገባውን ልጁን በዕደ ማርያምንም በእስር አግዞታል::[12] በራሱ ዜና መዋዕል እያሌ ቅጣቶች ተመዝግበዋል:: ለንጉሥ ሰጊድ እንዲደረግ በደፋ ሕግ ያወጣውና "አንቱታ"ን[13] ያመጣው እርሱ መሆኑ ከዜና መዋዕሉ እና ከታሪክ መጻሕፍት እንረዳለን::[14] በጊዜው ለደገኛው ክርስቲያን ንጉሣዊ አስተዳደር ተገዳዳሪ ከነበሩት ቆለኛ ሡልጣኔቶችና የቤተ እስራኤላውያን መሳፍንት መካሣት አንጻር ንጉሡ ዙፋኑን ያለ ሃይማኖት አንድነት ማስጠበቅ እንደማይችል ስጋት አድሮበትም ሊሆን ይችላል:: ይህን በመሳሰሉ ምክንያቶች ደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ ክንዱን አበርትቶባቸው ሊሆን ይችላል ቢባል ተገቢ መላምት ነው ብዬ አምናለሁ:: ያም ሆኖ ግን የደቂቀ እስጢፋኖስ "ለመስቀልና ለእመቤታችን እንሰግድም" የሚል አቋም ማስተባበያ እስካልተገኘለት ድረስ ስቆቃቸው "ፖለቲካን ብቻ" መሠረት ያደረገ ነው ብሎ መደምደም ደግሞ

---

[10] Krzysztof Piotr Blasewicz, Ethiopian Monasticism, 1999, p.42

[11] በዚያ እንኳ ጋስ በኢትዮጵያ በሌላውም ዓለም የተጠናከረ ዓለማዊ ተቋም ባልነበረበት ጊዜ እነርሱ ከሌሉ ለነገሥታቱ ፍትሐ ነገሥቱን የሚተረጉም የለምና ሁሉም ካህናተ ደብተራ ከቀዎችና ሐሳውያን ስለ ነበሩ በቤተ መንግሥቱ መኖር አልነበረባቸውም ማለት ነገራቸውን የወቅቱ ሁኔታ አለማገናዘብ መስሎ ቢታይም::

[12] የጧ. በዕደ ማርያም ዜና መዋዕል፡ገ.1-3

[13] እስከማውቀው በግእዝ ቋንቋ አንቱታ የለም:: ምናልባት ክርክሩ ከግእዝ ውጭ ባለ ቋንቋ ተካሂዶ ይሆን? ወይስ አማርኛ ከንጉሩ.ማይሊኑቱ ከግእዝ ጋር ተባገቀ በዚያ ዘመን የንባሌ ቋንቋ መሆን ጀምሮ ይሆን?

[14] ፍሰሐ ያዜ፤ የኢትዮጵያ የ5ሺህ ዓመት ታሪክ፤ 2004 ዓ.ም፡ገ.252

ተአማኒ አይመስለኝም። ጨስ ከሌለ እሳት አይኖርም! የልደት በዓል "ታኅሣሥ 28 ወይስ ታኅሣሥ 29?" ነው መከበር ያለበት በሚል ክርክር ብቻ የብዙኃን ደም በፈሰሰባት አገር[15] ለአመቤታችንና ለመስቀል አለመስገድ እንዲህ እንደ ዋዛ ይታለፋል ማለት ይከብዳል። ስለዚህ በእኔ እምነት ለእመቤታችንና ለመስቀል ያለ መስገዳቸው ጉዳይ መነሻ ሆኖ ከላይ የተጠቀሱት ፖለቲካዊና መደባዊ ጉዳዮች ስቃያቸውን በገድላቱና በተአምረ ማርያም በሰፈረው መልኩ እጅግ ኢሰብአዊ እንዲሆን አድርጎታል።

(3.4) ደቂቀ እስጢፋኖስ የንጉሡን ሰሎሞናዊነት ስላልተቀበሉ ነው መከራ የወረደባቸው የሚለው አነጋገር ከአባባል ባለፈ በገድሉ ሲንጸባርቅ አናየውም። ነገሥታቱ እስራኤላዊ ዝርያ አለን የሚለውን ትምክሕት ባይተዉትም ወደ ኋላ ክርስትናቸውንም ትልቅ የሥልጣን ሕጋዊነት (Legitimacy) ማስገኛና መመኪያ አድርገውታል። ሰሎሞናዊ ነገሥታት ከእስራኤላዊነት የዘር ሐረግ ይልቅ በክርስትናቸው መኩራትን እንደሚያስቀድሙ አፄ ይስሐቅ በገጽ 83 "ከእስራኤል ስምና ከክርስትና ስም የቱ ይበልጣል?" ለሚለው ክርክር "እኛም ትምክሕታችን በክርስትና ነው!" ሲል ለአባ እስጢፋኖስ ደግፎ አረጋግጡዋል።[16]

---

[15] አባ ፊልጶስ "የልደት በዓል ሁልጊዜ ታኅሣሥ 29 ብቻ መከበር አለበት፤ በዓሉን 28 አድርጎ ዕለቱ ረቡዕና ዓርብ ቢውል በዚያ ዕለት የጥሉላት ምግቦችን መመገብ ጾምን ከመሻር ይቆጠራል" በማለቱ ከዓምደ ጽዮን ብዙ መከራ ደርሶበታል። (እራቱ ኃያላን፡ገ.274-277) ተደም ሲል (ከመጥፋታቸው በፊት) ጻጋዎች! ዛሬ ድረስ ቅብዐቶች ልደትን በሁሉም ዘመናት ታህሣሥ 29 ብቻ ያከብራሉ። እኛ በዘመነ ዮሐንስ በ28 ስንፈታ እነሱ ይጾማሉ። በአንጻሩ እኛ በ28 (ልደት ማግሰኞ ወይም ሐሙስ ከዋለ) ፈትተን በኋጋታው 29 ጾም ቀን (ረቡዕ ወይም ዓርብ) ከዋለ ዕለቱን ስንጾም እነሱ የፍስክ ይመገባሉ። ጾሙን (የገና ጾም/ ጾመ ነቢያት) የሚይዙትም ሁልጊዜ ኅዳር 19 ቀን ነው፤ እኛ ምንጊዜም ኅዳር 15 ቀን እንይዛለን። ይህ የዘር ከ1298 ዓ.ም. ጀምሮ ሲጓተትና ሲያወዛግብ ከቆየ በኋላ ጥቅምት 15 እና 21 ቀን 1980 ዓ.ም. በተካሄደ ሲኖዶስ ተወስኖ በተዋሕዶ ወገኖች ዘንድ በወጥነት እየተተገበረ ይገኛል። (የኢ.አ.ተ.ቤ.ክ ከልደተ ክርስቶስ እስከ 2000 ዓ.ም (፳፻ ዓ.ም.)፡ገ.36ና 40)

[16] ቀደምት ሰሎሞናዊ ነገሥታት ከእስራኤላዊ ዝርያ ይልቅ ለክርስትና ያደላ ትምክሕትና ሥነ ልቡና እላቸው። (ክብረ ነገሥት፡ገ.06-108። ዶናልድ ሌቪን፤ ታላቋ ኢትዮጵያ፡ገ.90) ነገሥታቱ ተደጋጋሚ "ፈላሻ" ከሚባሉት የሰሜን ኢትዮጵያ ቤተ እስራኤላውያን ጋር ያደረጓቸው ጦርነቶችም ከሐረገ-ትውልድ ትምክሕት ወደ ክርስትና ትምክሕት ማዘንበላቸውን ያሳያሉ።

# ምዕራፍ አራት

## እንደ ስርዋጽ - ደቂቀ እስጢፋኖስ ነገሥታቱን በተለይ አፄ ዘርዓ ያዕቆብን እንዴት ያዩታል?

የታሪክ መዛግብትን ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር አነጻጽረን ካየን ከአፄ ይስሐቅ (1406-1420 ዓ.ም.) እስከ አፄ ናዖድ (1486-1500 ዓ.ም.) ባለው ጊዜ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥታዊ ዙፋን ከስምንት እስከ ዐሥር ነገሥታት ነግሠዋል/ ተፈራርቀዋል። ሆኖም ከእነዚህ ውስጥ ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋር ስማቸው ተያይዞ በገድላቱ የተነሣው ስድስቱ ብቻ ናቸው። አፄ ይስሐቅን፣ አፄ ናዖድንና አፄ ልብነ ድንግልን[1] ገድላቱ በበጎ ያነሷቸዋል። አፄ ዘርዓ ያዕቆብን፣ ልጁን አፄ በዕደ ማርያምንና አፄ እስክንድርን በመራር ቋንቋ ቅጽል የክፋት ስም አውጥተው ይጠሯቸዋል። ጥቂት እንሒድበት!

(4.1) አባ እስጢፋኖስ ለመጀመሪያ ጊዜ አፄ ይስሐቅ ፊት ተከሶ በቀረበ ጊዜ ንጉሡን ሲመክረው "…መጽሐፍ 'እንግዲህ ንጉሦች አስተውሉ፤ መሬትን የምትገዟት ሁሉ ተገሠጹ፤ ለእግዚአብሔር በፍርሐት ተገዙ' ይላል (መዝ.2፡10)። … ለእግዚአብሔር መገዛት ማለት ሕጉን በመፈጸም ራስክን እየጠበቅህ ሕዝቡንም በእውነትና በትክክል ማስተዳደርና በቅዱስ ሲኖዶስ እንደ ተሠራው ሥርዓት ካህናት መንጋውን በትክክል እንዲጠብቁ፣ ሕዝቡም እንደ ተደነገገው ለእረኞቻቸው እንዲታዘዙ፣ መነኮሴዎች ፍጹም ለመሆን ለሚፈልጉ ወንጌል እንዳዘዘው ራሳቸውም በሰጡት ቃል እንዲቆሙ ሁሉንም በየሥርዓቱ ማደራጀት ነው" በማለት ስለ ተቋማዊ አደረጃጀት ንጉሡን ያሳስበዋል።[2] ንጉሡ በሃይማኖት ጉዳይ ጠልቆ እንዳይገባና ስለ ራሱ ክብርም መጨነቅ እንዳያበዛ "ንጉሥ ሆይ! መንግሥትህን ለእግዚአብሔር አምላክ አገልግሎት አድርገው እንጂ ለራስህ ክብር አይሁን፤… እግዚአብሔር ፍጥረታትን ፈጥሮ ለመንፈሳውያን በመንፈስ፣ ለሥጋውያን በሥጋ የሚኖሩበት ሕግ ለሁሉም አወጣ። ከየወሰናቸው እንዳያልፉም ትእዛዝ ሰጠ"

---

[1] ያልታተመው የአባ ገብረ መሲሕ ገድል - የአፄ ዘርዓ ያዕቆብን ቈስጠንጢኖስ መሰኘት ለማጣጣል በሚመስል መልኩ - አፄ ናዖድን ቈስጠንጢኖስ፣ ልጁን አፄ ልብነ ድንግልን እንዲሁ ዳግማዊ ቈስጠንጢኖስ ይላቸዋል።

[2] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.87

እያለ በለዘብታ ይመክረዋል።[3] ተከራካሪዎቹን መነኮሳትም በሃይማኖታዊ ጉዳይ ለምን ንጉሡ ፊት አቀረቡኝ በሚመስል መልኩ "እውነትን የሚፈልገውን በከንቱ የሚቃወሙ ከሆነ እኔ ደግሞ ወደ የእግዚአብሔር ወይ የቄሳር ባሮች ሁኑ አላቸዋለሁ፤ ምክንያቱም ጌታ፡- 'የቄሳርን ለቄሳር ስጡ፤ የእግዚአብሔርን ለእግዚአብሔር አድርጉ' ብሏል" ይላቸዋል።[4]

(4.2) አባ እስጢፋኖስ የንጉሥ ቃል ገደብ አለበት ብሎ ያምናል። ገደቡም የእግዚአብሔር ቃል ነው።[5] ለመነኰሳት በሥጋዊ ፍርድ መደመር እርም ነው ብሎ ይከራከራል። ለሥጋ ነገሮች ግን መፍረድ እንደ ተፈቀደላቸው ያምናል፤ ያም ቢሆን ታዲያ "በሕጉ መሠረት በእውነት ፍርድ ነው እንጂ [ከሕግ ውጭ] አይደለም (ማቴ.19:25)።"[6] እነዚህንና ከላይ ያነበብናቸውን "ለመንፈሳውያን በመንፈስ፤ ለሥጋውያን በሥጋ የሚኖሩበት ሕግ ሰሁሉም አወጣ። ከየወሰናቸው እንዳያልፉም ትእዛዝ ሰጠ ... የቄሳርን ለቄሳር" የምትለ እንጋገር ስናይ ደቂቀ እስጢፋኖስ የሃይማኖትና መንግሥት መለያየት (separation of state and religion) ጽንሰ አሳብ ሳይኖራቸው አይቀርም ብለን እንገምታለን።

በሌላ በኩል የአፄ ይስሐቅንና የአፄ ናዖድን በመነኮሳት በመታገዝ የተሰጡ ፍርዶች በእነርሱ ላይ መገፋትን ስላስቀሩ በአምንታ ሲመለከታቿው እንታዘባለን።[7] "ነገሥታቱ የእነሱን አስተምህሮ ቢደግፉ ኖሮ ስለ መንግሥትና ሃይማኖት መለያየት ላይናገሩ ይችሉ ነበር" ብለን እንድንጠረጥር ያደርጉናል። ለንጉሡ ሥልጣን መደንገጊያና መገደቢያ ብለው የሚጠቅሱት መዝሙረ ዳዊትን፤ ወንጌለ ማቴዎስንና መጽሐፈ ሲኖዶስን መሆኑም ጨርሰን 'የሃይማኖትና የመንግሥት መለያየት መርሕ አቀንቃኞች' የሚል ቅጽል እንዳንሰጣቸው ይይዙናል። አባ እስጢፋኖስ አፄ ዘርዓ ያዕቆብን ሲወቅሰው "በእግዚአብሔር ሕግ መሠረት ብትፈርድ ኖሮ ከእግዚአብሔር ሞገስን ባገኝ

[3] ዝኒ ከማሁ፡ገ.93
[4] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.81።
[5] ዝኒ ከማሁ፡ገ.81
[6] ዝኒ ከማሁ፡ገ.93
[7] ዝኒ ከማሁ፡ገ.89



ነበር" እያለ ነው።[8] ከዚህ አንጻር ለእነሱ ያልተስማማቸው የሚመስለው የሚዳኙበት መሠረታዊ ሕግ (Substantive Law) ሳይሆን ፥ ሕጉ የሚተገበርበት ሥርዓት ፍትሐዊነት (due process of law) በእነሱ ሚዛን አርኪ አለመሆን፤ ችሎቱ ለዳኝነት በሚመች መልኩ ነጻና ገለልተኛ (Independent and Impartial) መስሎ ሊታያቸው አለመቻሉ፤ የተሠየሚ ዳኞች ተገቢነት (Relevance)[9] ዓለማውያን ስለ ተካተቱበት ጥያቄ ውስጥ መግባቱ፤ ... በአጠቃላይ የሕግ መተግበሪያና መተርጎሚያ ሥርዓቱ (Procedural Law) ይመስላል ቅር ያሰኛቸው።

በጥቅሉ እስጢፋኖሳውያን ከካህናተ ደብተራ ጋራ ሲነጻጸሩ የንጉሡ ሥልጣን በእግዚአብሔር ቃልም ቢሆን ሊገደብ እንደሚገባው፤ ዓለም በቃኝ ብለው የመነኑ መነኰሳት በዓለማዊ ፍርድ መደብለቅ እንደሌለባቸው፤ ማኅበራዊ ግንኙነቱ ሁሉ በተደነገገለት የሥነ ሥርዓት ሕግ መሠረት እንዲሆን ያላቸው የአደባባይ አቋም ከዘመናቸው የተራመደ አስተሳሰብ እንደ ነበራቸው ሊያስቴጥርላቸው ይገባል። የሰጊዷን ጉዳይ ሳንረሳ ንጉሡ በዚህ አስተሳሰብ ካልሔደ እንደ ንጉሥ ላያዩት እንደሚችሉ መገንዘብ እንችላለን።

(4.3) ደቂቀ እስጢፋኖስ እስከ መጨረሻው ድረስ ለንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ መስገድን እምቢ እንዳሉ ነው ያለፉት። "እጅ መንሳት"ና "አምልኮ" ያለው ልዩነት ጠፍቷቸው አይመስለኝም። እርስ በእርስ እጅ ሲነሳሱ አይተናል! እርሱም ቢሆን "እኔን ለሰጣችሁ አምላክ ስገዱ" አለ እንጂ ቃል በቃል "አምልኩኝ" አላለም። ይኼ የጠፋቸው አይመስለኝም። እነርሱ የማይሰግዱለት "በሕግ የማይሠራ አምባገነን ነው" ብለው ስለሚያምኑ ይመስላል።

በገጽ 185 ስለ ንጉሡ በነገረ ፈጅነት የሚከራከሩት ካህናተ ደብተራ እና ደቂቀ እስጢፋኖስ ትንፋሽ የሚያቆምና የቅዱሳት መጻሕፍት ጥቅሶች የተኾነደጎዱበት አስደማሚ ክርክር ያደርጋሉ። በክርክሩ መኻል ከካህናተ ደብተራ ወገን የሆነው ነገረ ፈጅ "ለንጉሡ ለምን አትሰግዱም፤ ሐዋርያት በሲኖዶሳቸው አክብረውት የለምን?" ሲል ላቀረበለት ጥያቄ ደቂቀ

[8] አባ እስጢፋኖስ ዘጉንዳጉንዶ፡ገ.137። ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.102።
[9] በሂደቱ ንጉሡ እንደ ፈራጅም እንደ ተከራካሪም ሆኖ መቅረቡ የሚያመጣው ተፅዕኖ አይኖርም አይባልም።

እስጢፋኖሳዊው ወንድም ሲመልስ "ንጉሡ በሕግ የሚሠራ ቢሆን እንደምትሉት እናከብረዋለን፤ ከሕግ ውጭ የሚሠራ ከሆነ ግን ማምባይ [Dictator] ነው" ሲል የማይሰግዱለት ሕግ ተከትሉ ስለማይሠራ እንጂ የአክብሮት ስግደት (እጅ መንሳት) ስለ ተከለከለ እንዳልሆነ ልባቸው እንደሚያውቅ ይጠቁመናል። በሌላ አጋጣሚ እንዲሁ አንድ የንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ሰላይ ስለ ንጉሡ ክርስትና ያላቸውን አመለካከት ሲጠይቃቸው "ሕግ ከፈጸመ ክርስቲያን እንለዋለን፤ እኛ እንደምናየው ከሆነ ግን አንተም ታየዋለህ" ይሉታል። እነርሱ እንዴት እንደሚያዩት ለማወቅ ይህ ጥቅስ ከሰፈረበት መስመር ዝቅ ብለን ስናነብ "ከሕግ ውጭ መሆኑ እውነት ነው፤ ንጉሥ አይደለም" ሲሉት እናገኛለን።[10] በእነርሱ እይታ፦ ንጉሡ ከሕግ ውጭ ነው፤ ከሕግ ውጭ የሆነ ንጉሥ ደግሞ 'በስም' እንጂ 'በገቢር' ንጉሥ አይደለም! T/C ታደሰ ታምራትም አባ እስጢፋኖስ የኑፋቄ መሪ ከተባለ ምክንያት ሊሆን የሚችለው የቅስና ሥራን ከንግሥና ደባልቆ በተቋማዊ አንድነት በሚመራው ኃያሉ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን በመፈጠሩ እንደሆነ በአጽንኦት ይጽፋሉ።[11] የአባ እስጢፋኖስን ለመስቀልና ለእመቤታችን አለመስገድ ራሳቸው በነጠላ ትእምርተ ጥቅስ ውስጥ ቢሆንም 'ኑፋቄ - Heresy' ብለው ከጠቀሙን በኋላ ድርጊቱ እንደ ኑፋቄ ሲቆጠር እንደማይገባ አድርገው መደምደማቸው ይገርማል። እነ አለቃ ታዬ በ20ኛ ክፍለ ዘመን መባቻ በተመሳሳይ ሥዕል-አስተሀቃሪ አቋም[12] ሲወገዙ አይተናልና[13] አባ እስጢፋኖስ ባራመደው የጸጋ ስግደትን የሚቃወም አቋም ዛሬም ቢኖር ይወገዛል - እንኳንስ በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን[14] - እንላለን!

---

[10] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.156

[11] Taddesse Tamrat, p.115

[12] አርግዮ አለቃ ታዬ በስዊድን ሚሲዮን ተከትከተው ያደጉ የለየላቸው ፕሮቴስታንት ናቸው።

[13] መርስዔ ኀዘን ወልደ ቂርቆስ፣ ትዝታዬ፡ስለ ራሴ የማስታውሰው፣2002 ዓ.ም.፡ገ.146

[14] በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ መንግሥት ውስጥ፦ (1) አምልኮ ባዕድ፣ (2) ለእመቤታችንና ለመስቀል የጸጋ ስግደት አለመስገድ፣ (3) ለንጉሡ ዙፋን ታማኝ ሁኖ እጅ አለመንሳት፣ (4) በማዕ ውስጥ ሰጥና ሰጥ ብሉ አለመገዛት፣ (5) ግብጻውያን ክርስቲያኖችን ጨምሮ ማኛውም ክርስቲያን መተናኮስ በመንግሥት ላይ እንደሚደረግ ትንኮሳ እንደሚቆጠር በዜና መዋዕለ በዝርዝር የቀረቡት የደስክና የዲኖ አምላኪዎች ፍዳ፣ የደቂቀ እስጢፋኖስ መሳደድ፣ የሚስና የልጆቹ ግርፋት፣ የሀድያው ገራድ የሽንፈት ፍጻሜና ግብጽ በተቃጠለችው ደብረ የተሠየመችው የደብረ ምጥማቅ (ጸድቃኔ) አመሠራረት በቅደም ተከተል ይነግሩናል። (ዓፄው የተጠቀሙ የመንግሥት ኃይሌ፣ የዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል፡ገ.1-2፣ 34-35፣ 52፣ 40፣ 28።) የጊዜው የመንግሥት እሴቶች (values) እነዚህን ማለትም አምልኮ እግዚአብሔርን፣ ክብረ ድንግልንና ክብረ



(4.4) ደቂቀ እስጢፋኖስ ንጉሡንም ሆነ ስለ ንጉሡና በእርሱ ዘመን ስለ ተላለፉባቸው ፍርዶችና ውግዘቶች አፈጻጸም የሚያሳድዷቸውን ኃይላት በምግባር ጉድለት፣ በጭካኔ፣ በስግደትና ከንቱ ውዳሴ ፈላጊነት እንጂ በሃይማኖት ሕጸጽ ሲከስሷቸው አናይም። ሲወቅሷቸውም "አሁን ዐውቀዋል፤ ተረድተዋል፤ ተረድተውም መጽሐፍ እንዳለው ዕውሮች ሆኑ" በማለት በዐውቆ አጥፊነት ነው የሚወቅሷቸው።[15] ቤተ ክርስቲያናቸውን ሲያቃጥሉባቸው እንኳ "የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን አጠፉብን፤ ክርስቲያን ሆነው ሳለ በእሳት አቃጠሉት።... ክርስቲያኖች በእግዚአብሔር ቤት ላይ እንዲህ ያደርጋሉን? የጣዖት ቤት መሰላቸው ወይስ ነገሩ እንዴት ነው?"[16] የሚል የትካዜና የብሶት ቋንቋ ይጠቀማሉ እንጂ የአሳዳጆቻቸውን ክርስትና አይክዱም። ቀደም ባለው ጊዜ እንዲሁ አባ እስጢፋኖስ "እናንተ ክርስቲያኖች ሆናችሁ፣ ንጉሡም ክርስቲያን ሆኖ ሳለ ለምን እንደዚህ ያደርጋሉ?... በጉልበት እንዲያጠቁን ያለ ፍርድ ትለቁናችሁን?" የሚል ወቀሳ ተከታዮቹ ሲጠቁ ባልተከላከሉለት የአካባቢው ገዥዎች ላይ ሰንዝሮ ነበር። በተረፈ አፄ ዘርዓ ያዕቆብንና ልጁን (አድማስ በፀር) እንኳንስ በእነርሱ ላይ ስላደረሱት የጭካኔ ተግባር በ'ደስክ' (ጣዖት/ ጋኔን) አምላኪዎች ላይ ስለ ወሰዱት እርምጃ ሳይቀር እያነሡ ስለ ምግባራቸው ይዘልፏቸዋል።[17] ያው እርሱም በድርሰቶቹ በይሁዲነት እና በጸረ ማርያምነት ያብጠለጥላቸዋል። ሆኖም "እስጢፋ" የሚላቸው እነርሱ እንደሚሉት "ሰይጣን" ለማለት ነው ብሎ ለመደምደም ይከብዳል።

(4.5) "እስጢፋ" የሚለው ቃል በቅኔ ቤት ግስ ይታወቃል። የእስጢፋኖስ ከፊል ስም ነው። ከፊል ስም የተለመደ ነው። ጳውሎስ ለማለት "ጳውሊ"፣ ባቢሎን ለማለት "ባቢል"፣ ናቡከደነጾር ለማለት "ክድንጾር"፣ ኢየሩሳሌም ለማለት "ሳሌም" ማለት በቅኔ ቤት የተለመደ ነው። ለምሳሌ፦ ደቀ እስጢፋ

---

መስቀልን፣ ክብረ ንጉሥንና የግዛት አንድነትን፣ ዓለም አቀፍ ክርስቲያናዊ/ ኦርቶዶክሳዊ ወንድማማችነትን ያማከሉ ይመስላሉ። ለባሕረ ነጋሹ በጣም ከፍ ያለ ደረጃ መስጠቱም ለንግድና ለሉዓላዊነት ያለውን ቀናኢነት ሊያሳይ አይቀርም። (ገድ ከማሁ፡ገ.23።)

[15] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.155

[16] ገድ ከማሁ፡ ገ.256 እና 257. (ግእዙ፦ "ቤተ ጣዖትኑ መሰሎሙ፤ ወሚመ ቤተ አረሚ?")

[17] ገድ ከማሁ፡ገ.221

የተባለ ምሁር በአፄ በዕደ ማርያም ዘመን ግሪክ (ግብጽ?) ወርዶ ቅኔ አጥንቶ የተመለሰ ሊቅ[18] በአፈ. ታሪክ ያለ ሲሆን ይኼው የቅኔ ሊቅ የንጉሡን ማለት እስኩብልሉ ስለ ተደረሰበት ከአፄ እስክንድር ጋር ባደረገው የቅኔ ተዋስኦ:-

"...ወሠራቂ ንግሥት አነ፤ 'ደቀ እስጢፋ' ሕሱር፤
አንበሳ እስክንድር፤
እንለ አንበሳ እንዘ ትትፀሀር፤
እም እርአይከ ተንጠኒ ምድር" ብሎ ነበር። መ/ብ አድማሱም በሐዋርያት ሥራ የተጠቀሰውን ቀዳሚ ሰማዕት እስጢፋኖስ በከፈለ-ስሙ በመጥራት:-
"ገሪማ ኢትሁር ዘእንበለ ሰብአ ፍናከ፤
ቀተልተ 'እስጢፋ' አዕባን እስመ ተለው ድኅሬከ"
የምትል ግእዝ ጉባኤ ቃና አለቻቸው። ስለ ሆነም በገድሉ ገጽ 208 ፍሬ ክርስቶስ የተባለው የደቂቀ እስጢፋኖስ ወገን "እስጢፋ በግብጽ ቋንቋ የሰይጣን ስም" ሲል መከራከሩና የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ አጥኚዎችም[19] ይህን መቀበላቸው ከብሒላችን[20] የሚገጥም አይመስልም።

(4.6) በአፄ ዘርዓ ያዕቆብና በደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ ዙሪያ ለንግግር ቢከብድም ሳይነሣ መታለፍ የሌለበት ሌላ ዐቢይ ነጥብ አለ፤ የብሔር ጉዳይ፤ የአማራ - ትግራይ ጥቂት ዘመናውያን ልሂቃን ቁርሾ። ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ታሪኩን በብሔር መነጽር ለማንጸር የመፈለግ አዝማሚያ በማኅበራዊ ሚዲያው አካባቢ ይታያል። ስሁት እይታ ይመስለኛል። ምክንያቱም:-

(1) በዘርዓ ያዕቆብ ዘመን በነበረው ፖለቲካ ትግራይ - አማራ የሚል ፖለቲካዊና መንፈሳዊ የሥነ ልቡና ተጻራሪ አደረጃጀት የነበረ አይመስለኝም። እንደ ዜና መዋዕሉ ከሆነ በዚያ ዘመን አማራ የሚባለው አገር ወሎ አካባቢ ያለውን ግዛት ነው በዋናነት የሚያመለክተው።[21]
(2) የደቂቀ እስጢፋኖስ ቀዳምያን ከሳሾች የአካባቢያቸው መነኰሳት ነበሩ። መጀመሪያ ላይ አባ እስጢፋኖስን በነጻ ሲለቀቅ አፄ ይስሐቅ ዐዋጁ በሸሬም እንዲነገር ያደረገው የእስጢፋኖሳውያን ዋነኛ ተቃዋሚዎች የሽሬ መነኩሳት ስለነበሩ ነው።[22] ቅዱሳንን በትውልድ ቦታ ወስኖ መጥራት ቢከብድም አባ እስጢፋኖስን መከረውት አልመለስ ስላላቸው ከገዳም እንዲወጣ የበየኑበት እንደ'ሉ በአጋመ የተወለዱት ቅዱሱ አባ ሳሙኤል ዘቈየጻ ነበሩ።
(3) በአንጻሩ አባ እስጢፋኖስ በአካባቢው መነኰሳት ሲባረር ከለላ የሆኑት ዛሬ በአማራ ክልል የሚገኙት የጎጃሙ ጣና እና የጎንደሩ ወገራ ነበሩ።[23]
(4) የዘርዓ ያዕቆብ ግዛት የአንድ ብሔር ሳይሆን ኅብረ ብሔራዊ ነበር። ዜና መዋዕሉ እንደሚለው[24] ንጉሡ ከቤተ ክርስቲያን ሲመለስ የጪዋ ሠራዊት 'ያወካሉ፤ በየሀገሮቻቸው ልሳንም (ቋንቋ) ይዘፍናሉ።" እዚህ ላይ "በየሀገሮቻቸው ልሳን..." የሚለው ቃል የቤተ መንግሥቱን ኅብረ ብሔራዊ ገጽታ ያሳያል - ንግሥናው በዘር ሐረግ መሆኑ እንደተጠበቀ ሆኖ።
(5) የንጉሡ ደንበኛ ሚስት የሀድያ ተወላጇ እሌኒ ነበረች።

---

[18] የግእዝ ቅኔያት፣ ቅጽ 1፣ 1980፣ አ/አ/ዩ:ገ.19-22። ይህ ሊቅ እስጢፋኖሳዊው አባ ዕዝራ ሳይሆን አይቀርም የሚሉ መረጃዎች አሉ። (Encyclopadea Ethiopica, Vol. 2, p. 482) ገዳሙ ያሳተመው የአባ እስጢፋኖስ ገድል በመቅድሙ ገጽ 14፣ ኅዳግ ቁ. 23 በጣና ያለችው "ደቅ ደሴት" በደቂቀ እስጢፋኖስ መሰየሟን ይገልጻል። በአባ ገብረ መሲሕና በአባ ዕዝራ ገድል ንጉሡን (አፄ እስክንድርን) በከፋት (በመጠኑ) ያነሡታል። ጉዳዩ ጠለቅ ያለ ጥናት ሳይፈልግ አይቀርም። የመነሻ ጥሬ ሀቆችን ለማኖር ያህል ግን:- (1) ዕዝራ ግብፅና ኢየሩሳሌም መሄዱ እውነት ነው፤ (2) ጠቢብና መክብብ የሚሉ የባለቅኔ ቅጽሎች አሉት፤ (3) ደቂቀ እስጢፋኖስ ወደ ጣና መሰደዳቸው እውነት ነው፤ (4) በግብፅ ወደ ኢየሩሳሌም የሄደው በአፄ በዕደ ማርያም ዘመን መሆኑም እውነት ነው፤ (5) አባ ዕዝራን ንጉሥ እስክንድር ፈልጎት ነበር፤ ግን አላገኘውም። (ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.293።) እንደሚባለው በደቅ ደሴት ተሰውሮበት ይሆን?
[19] አማርኛ የቤ.ክ. መዝገበ ቃላት ቅጽ 9፣ገ.160።
[20] "እስጢፋ" = "ከፈለ ስም"፤ "ለማርያም ስግደት አይገባም ቢሉ ዐጤ ዘርዓ ያዕቆብ በደብረ ብርሃን ከቀጡዋቸው ኹለት ሊቃውንት አንደኛው <u>የደቀ እስጢፋ መም[ህ]ር</u>" (ደስታ ተክለ ወልድ፣ ዐዲስ ያማርኛ መዝገበ ቃላት፣ 1962 ዓ.ም.፣ አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት:ገ.142።)

[21] የአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል:ገ.26ና 28። "ወሎ የአገር ድባብ" የተሰኘ በሌሎቹ ጓታቸው መኩንን በ1984 ዓ.ም. የተዘጋጀ መጽሐፍ አሁን "ወሎ" በመባል የሚታወቀው አካባቢ እስከ አፄ ሱስንዮስ (1599-1624) ድረስ "ቤተ አምሐራ" ይባል እንደ ነበር ይገልጻል። የመጽሐፈ ቅዳሴ ንባብና ትርጓሜ ገጽ 423:- አማራ፤ በገምድርና ጎጃም ኩታ ገጠም አካባቢዎች መሆናቸውን ይገልጻል። ትርጓሜው አማራ የሚለው ወሎን ነው። ስለዚህ ግዛቱን የሚጠቁም አማራ ከሚለው ሌላ እንደሌለ ማስረዳት ሲገባ ዛሬ አማራ የሚባለውን ሁሉ መጠቅለል አይቻልም ... [illegible] ከአማራ በዚሁ ምክንያት ... ንጉሡ መውቀስም ሆነ ማወድስ ሲቻል የዛሬው የአማራ ፖለቲካዊና መልክዐ ምድራዊ ክልል ከነ አወቃቀሩ በዚህ መልኩ ባልነበረበት ጊዜና ሁኔታ የትናንቱን አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ወደዚህ ስቦ በሌሎች [illegible] ይከብዳል። በዜሐረሰባዊ መስኪያ ለመደናትና ለመኩንን መሞከር ስለመጠየኝ ጎሲና ለመቀበል ይከብዳል። አቶ ፐ/ር መስፍን ወ/ማርያምና ላጲሶ ጌ.ዴሌቦ ባወያይነት በመሩትና በብሔራዊ ቴያትር በተካሄደ ውይይት ላይ አቦይ ስብሐት ነጋ ጉዳዩን ከብሔር (አማራ ከመሆንና አለመሆን) ይልቅ በሥርዓት (ንግሥናን በማጽናት) ዐይን እንደሚያዩት ገልጸው ነበር።
[22] ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.88ና 265፤ ካሕሳይ:ገ.35 (ያልታተመው የአባ ገብረ መሲሕ ገድል እንደሚለው ከአሳዳጆቻቸውም ውስጥ ገ/እንድርያስና ዘርዐ ሠናይ የሚባሉ መኳንንት ትግራይ - ትግሬ መኩንን የሚል ማዕረግ ያላቸው - ነበሩበት።)
[23] ደቂቀ እስጢፋኖስ:ገ.73
[24] የአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል:ገ.18

(6) ቀደምት ነገሥታትም ሆኑ ብዙኃን ደቂቀ እስጢፋኖስ ራሳቸውን ከአገራዊ ብሔር ይልቅ ከእስራኤላውያን ነው የሚያዛምዱ።
(7) ንጉሡ በሃይማኖትና በሥልጣን ከመጡበት (ከዚህ ወገን፣ ከዚያ ወገን ሳይል ለመቅጣት) ርኅራኄ እንደ ሌለው በዜና መዋዕሉ የተመዘገቡ የወንድ ልጆቹ ቅጣቶች ያመለክታሉ።
(8) የቅጣቱ መነሻ ብሔረሰባዊ ቢሆን ቀደም ሲል በአፄ ይስሐቅ፣ ኋላም በአፄ ናዖድና ልብነ ድንግል ከዘርዓ ያዕቆብ የተለዩ ፍርዶች እናይም ነበር።
(9) በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዙሪያ ያሉት መነኮሳት ብዙኃኑ ከትግራይ ገዳማት የመጡ ነበሩ[25]። ንጉሡ በደብረ ዓባይ መማሩ በመግቢያችን ተገልጡዋል። ለአክሱም ጽዮን የተለየ ፍቅር ነበረው። ጥር 21 ቀን 1439 ዓ.ም በአካል ሄዶ "ቀርሐት"[26] የተሰኘውን ትውፊታዊ የንግሥና ሥርዓት አድርሶ፣ ለጽዮን የወርቅና የልዩ ልዩ መባዕ ስጦታ አበርክቶ ተመልሷል። በዚህ ምክንያት በአባ ጽንጠሌዎን ገዳም ዕረፍቱ በየዓመቱ ጳጉሜ 3 እንደሚታሰብ ተጽፏል።[27] በአንጻሩ ደቂቀ እስጢፋኖስ በአክሱም ጽዮን በበኩ ስለ መዘከራቸው ማስረጃ የለም። ይህ የሆነው በነገሥታት ጫና ነው እንዳይባል በዘርዓ ያዕቆብ ተሰቃይተው ሕይወታቸው ያለፈውና በእናታቸው ከትግራይ[28] የሚወለዱት አባ ተክለ ሐዋርያት አጽም በአፄ በዕደ ማርያም በክብር ሲፈልስ እናያለን።[29]
(10) እንዲህ ዐይነት አስተሳሰብ ቢኖር ንጉሡ ከኤምስጣቴዎሳውያን[30] ጋር ያለውን አለመግባባት በጉባኤ ለመፍታት ሲሞክር አይታይም ነበር። ደቂቀ እስጢፋኖስም ቢሆኑ አፄ ዘርዓ ያዕቆብን በብሔር ጥቃት በፍጹም አልከሰሱትም። እነሱም ቢሆኑ ትግራውያን ብቻ አልነበሩም። ስለሆነም ታሪኩን ከተጻፈበት ዐውድ ውጭ ለጥጦ ለመተርጎም መፋጠን ለቀናጽሳን ቀዳዳ ከመክፈት በቀር ፋይዳ የለውምና ቅኝታችንን በቅንነት እናስተካክለው።

---

[25] ዓለሙ ኃይሌ፡ገ.13።
[26] ቀርሐት = በመካከለኛው ዘመን የነበሩ ነገሥታት ከቦታ ርቀት የተነሣ ንግሥናቸውን ሸዋ ከፈጸሙ በኋላ አክሱም ሲሄዱ ድጋሚ የንግሥና ሥርዓት በማድረስ ከጽዮን በራኪ/ ምርቃት የሚቀበሉበት ሥልጣንን ዳግም የማስበረክ/ የማስመረቅ ሥርዓት ይመስላል። (የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት፣ ቅጽ 3፡ገ.122።) አፄ ኃይለ ሥላሴ ድረስ ሥርዓቱ የነበረ ይመስላል። ወደ ጽዮን ሲያመሩ በሩ ተዘግቶ በንቡረ ዕዱ "መኑ አንተ?" ሲባሉ "አነ ውእቱ ንጉሠ ጽዮን ወንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ" ብለው ተከፍቶላቸል። (ኮ/ል ፍስሐ ደስታ፣ አብዮቱና ትዝታዬ፣ 2008 ዓ.ም፡ገ.23።) አፄ ሱስንዮስም ይህንኑ ሥርዓት ሲፈጽም ይታያል (ዓለሙ ኃይሌ፣ የአፄ ሱስንዮስ ዜና መዋዕል፣ 2005፣ገ.91-92።)
[27] ሰሎሞን የሐንስ (ዲያቆን)፡ገ.104
[28] ዜና ቤተ ክርስቲያን ቁጥር 94፣ ነሐሴ 30 ቀን 1945 ዓ.ም.፣ በመ/ር ካሕሳይ ምንዝሮና በኢትዮጵያ ገጽ 67 ጎዳኝ የተጠቀሰ።
[29] አራቱ ኃያላን፡ገ.304
[30] ኤምስጣቴዎሳውያን መሠረታቸው ምድረ ትግራይና ኤርትራ ነው።

# ምዕራፍ አምስት

## ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ አይሁዳውያንና ፕሮቴስታንት ጸሐፍት ያላቸው እይታ

በወይኑ ግንድ መገለጥ "እናምናለን" የሚሉ ሰዎች ከማያምኑበት ቅጽር ገብተው ጥቂት አዕፁቆችን ቀጣጥፈው ከቀሰጡ በኋላ አዕፁቆቹ ለምልመው የበቀሉባቸውን የግንድ ቅርንጫፎች እየጨፈጨፉ ስለ ወይኑ ቅርንጫፎች አላበፈላጊነት ሲሰብኩን እንገረማለን። ጌታ የወይኑ ግንድ ነው! ቅዱሳን የእርሱ ቅርንጫፎች ናቸው። ቅርንጫፉን ከግንዱ የሚያዛምድ ታሪክ አለ። ገድል ማለት እርሱ ነው፤ መዓዛ ቅዱሳን - ከወይኑ ግንድ የበቀለ - አዕቀ ቅዱሳን! ይህን ካልኩ በኋላ ወደ ይሁዲና ፕሮቴስታንት ጸሐፍቶቻችን ልመለስ! ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ወደሚጽፉት! በገድል መጻፍ አስፈላጊነት ሳያምኑ ገድል ጠቅሰው ወደሚከራከሩት!

### 5.1. ደቂቀ እስጢፋኖስን እንደ ይሁዲ?!

(5.1.1) የንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ድርሰት ነው ተብሎ በሚታመነውና ንጉሡ ደቂቀ እስጢፋኖስን በ"ይሁዲነት" እና "ጸረ ማርያም"ነት ፈርጆ ጽፎበታል በሚባለው "መጽሐፈ ብርሃን" ዙሪያ ሒሳዊ ጽሑፍ እ.ኤ.አ. በ1973 ዓ.ም. የጻፉት ታዋቂው ኢትዮጵያዊ ይሁዲ (ቤተ እስራኤላዊ) ፕ/ር ኤፍሬም ይስሐቅ በ15ኛ ክፍለ ዘመን በሥላሴ የሦስትነት ጉዳይ ጥያቄ ያነሡ ዘሚካኤላውያንን በማየት፣ በቀዳሚት ሰንበት አከባበር ዙሪያ ጥያቄ አንሥተው ጥያቄያቸው ተቀባይነት ያገኙላቸውን እነ አባ ኤዎስጣቴዎስን በማጥናት፣ መጀመሪያ አካባቢ በነበራቸው አቋም ለመስቀልና ለእመቤታችን መስገድን እምቢኝ ያሉትን እነ አባ እስጢፋኖስ በመጥቀስ ያለ ጥርጥር ሁሉም (ለይሁዲነት ያደሉ) አይሁዳውያን ክርስቲያኖች ነበሩ እያሉ ይጽፋሉ። "there is no doubt that the anti-trinitarian stand, the reverence of Saturday Sabbath, and the refusal to worship Mary and prostrate before the Cross were beliefs held in common by the Jewish Chiristian community - በሥላሴ (አንድነትና) ሦስትነት ብሒል ያላቸው

ተቃውሞ፣ ቀዳሚት ሰንበትን ማክበራቸው፣ ለ(ቅድስት) ማርያምና ለመስቀል አለመስገዳቸው ከአይሁዳውያን ክርስቲያኖች ጋር የሚጋሩት እምነት ነው።"[1]

(5..1.2) የግሪክ ፍልስፍናን፣ የሥነ ምግባርና የአመክንዮ ሕጋጋትን ከአዲስ ኪዳን ጋር ለማጣጣም የሚጥረው ክርስትና "አሕዛባዊ የጥንተ-ግሪክ ክርስትና - Hellenistic Christianity" ይባላል።[2] ኦሪታዊ ትውፊቶችን ጠብቆ ከአዲስ ኪዳን ጋር የተዋሐደው እምነት-ተኮር ክርስትና "የጥንተ-ይሑዲ ክርስትና - Jewish Chiristianity" ይባላል።[3] የፕ/ር ኤፍሬም ይስሐቅ አተራረክ ከዚህ እይታ አኳያ የተነገረ ሳይሆን ኢትዮጵያውን አይሑዶችን (በተለምዶ ፈላሾችን) አዲስ ኪዳንን ከተቀበሉ ኢትዮጵያን ክርስቲያኖች ጋር በማነጻጸር ይመስላል። በሌላ አነጋገር እሳቸው Jewish Chiristian ሲሉ ከይሁዲነት ወደ ክርስትና የመጡትን ወገኖች ሳይሆን ፈላሾችን የሚያመለክቱ ሆነው ይታያሉ። ምክንያቱም የጽሑፋቸው ይዘት ስለ ጥንተ-ይሁዲ ክርስቲያኖች ሳይሆን ስለ ፈላሾች እምነት ነው የሚያያመለክተው። ይህን ደግሞ ከላይ ለእመቤታችንና ለመስቀል አለመስገድን፣ የሥላሴን ሦስትነት አለመቀበልንና ቀዳሚት ሰንበትን ማክበርን ጠቅሰው ደቂቀ እስጢፋኖስን የይሁዲ-ክርስትና ማንጸሪያ ካደረጉበት አካሄድና ከቀጣዩ መደምደሚያቸው መረዳት ይቻላል።

(5.1.3) ፕ/ር ኤፍሬም ይስሐቅ የዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል እና የደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላትን ጠቅሰው "...we now can confirm our original conjecture that the Stephanites formed part of the Ethiopian Jewish Chiristian community that strictly kept the Saturday Sabbath and the law, refusing to worship anyone except God - አሁን እስጢፋኖሳውያን ቀዳሚት ሰንበትን ጠንቅቀ ከሚያከብረውና ከእግዚአብሔር በቀር ለማንም ስገድ ከማያደርገው የኢትዮጵያ አይሁዳዊ ክርስትና ወገን ስለ መሆናቸው ያቀረብነውን ቀዳሚ ጥርጣሬ ማረጋገጥ ተችሎናል፤" ይሉና የእመቤታችንና የቅዱስ መስቀል ክብር በንጉሥ ዳዊት በኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን አማካይነት ተዋውቆ በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን

[1] Ephraim Issac., A New Text-Critical Introduction to Maṣḥafa Berhān with a Translation of Book I. Leiden: E. J. Brill, 1973, p.69

[2] አቡነ ጎርጎርዮስ፣ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ፥ገ.76።

[3] ዝኒ ከማሁ፥ገ.27-47።



ተቋማዊ ቅርጽና ይፋዊ ሥርዓት እንዲኖረው መደረጉን ይገልጻሉ።[4] እንደ እርሳቸው አገማመጊያ ከሆነ ተቋማዊ "ተሐድሶ" ያመጣው ዘርዓ ያዕቆብ ሲሆን ደቂቀ እስጢፋኖስ ግን ነባሩን አይሁዳዊ ክርስትና ለማስጠበቅ የቆሙ "ወግ አጥባቂዎች" ናቸው።

(5.1.4) የፕ/ር ኤፍሬም ይስሐቅን ጽሑፎች በምንጭነት የተጠቀሙት አባታችን ነፍስ ኄር ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስም በጥናታቸው "...they are denounced as 'Jews'... they may indeed have been followers of older Jewish Chiristian beleifs in Ethiopia which the king wanted to abolish - እንደ አይሁዳዊ ተቈጥረው ተወግዘዋል፤ በእርግጥም ንጉሥ (ዘርዓ ያዕቆብ) ለማጥፋት የፈለገውን ብሉይ አይሁዳዊ ክርስትና ተከታዮች ሊሆኑ ይችላሉ፤" ይላሉ፤ ዋናው የደቂቀ እስጢፋኖስ ግጭት መንሥኤ "የሥልጣን ነው" የሚለውን አቋማቸውን ሳይለቁ "ይሁዲ" መሆናቸው ግጭቱን አባብሶት ይሆናል የሚል መላምት በማከል።[5] የአቡነ ጳውሎስ ጥናት የተሠራው በደርግ ጊዜ እ.ኤ.አ. በ1988 ዓ.ም. በስደት አሜሪካ ሳሉ በመሆኑ በደቂቀ እስጢፋኖስ በኩል የነበረውን አቋም ገድሎቻቸውን አመሳክሮ ለማገናዘብ እክል ሳይገጥማቸው አልቀረም ብለን በመገመት በርኅራኄ ካላለፍናቸው በቀር "ደቂቀ እስጢፋኖስ ይሁዲነት ያጠበቁ ጥንታውያን አይሁዳውያን-ክርስቲያኖች እንደ ነበሩ" የሚያስመስለውን አቋም ሳይሞግቱ በማለፋቸው መውቀሳችን አይቀርም።

(5.1.5) ዘርዓ ያዕቆብ ደቂቀ እስጢፋኖስን "አይሁዳውያን" ማለቱ በነገረ ሃይማኖት ደረጃ የአይሁዳውያንን የእምነት መርሆዎች ተቀብለዋል ለማለት ሳይሆን የክሕደታቸውን መጠን አጉልቶ ቅጣቱን ለማክበድ፣ በሕዝብና አሕዛብ መካከል የተጠሉ ለማድረግ መሆኑ ግልጽ ነው። ይሁዲነት ከሐዲስ ኪዳን በኋላ ያለው ታሪኩ ከጌታ ስቅለት ጋር እየተያያዘ ስለሚተረክ በኦርቶዶክሳውያን ደራስያን ለበጎ ስያሜ እንደማይውል ይታወቃል። ምናልባት በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን ሞሶሎኒ እና ሂትለር ቢኖሩ ኖሮ ንጉሡ ደቂቀ እስጢፋኖስን "ፋሺስት" እና "ናዚ" ሊላቸው እንደሚችል መገመት

[4] Ephraim Issac:p,69-71

[5] Aba Paulos;p,262

ነው፡፡ ለነገሩ እነርሱም ስም ለማውጣት አልሰነፉም ከሰብአና አውርደው "ድብፀር" እና "ዝራጉን" ብለውታል፡፡ እነርሱ እንዳያ ስላሉት ግን ዘርዓ ያዕቆብ ጅብ ወይም ደራጎን ነው ብለን ራሳችንን አናቄልም፡፡ ለዚህ ነው የእስራኤላውያኑ ጸሐፍት እና ኋላ የምመጣባቸው የፕሮቴስታንት ጸሐፍት መደምደሚያ የሚያስገርመኝ፡፡ እንዴት ተከሳሹን በከሳሽ ቃል ብቻ እንበይናለን! ዘርዓ ያዕቆብ "አይሁዳውያን ብሎ ስለ ከሰሳቸው "አይሁዳውያን ሳይሆኑ አይቀሩም"! በጸረ ማርያምነት ስለ ተከሰሱ "ፕሮቴስታንት ሳይሆኑ አይቀሩም" እየተባለ ሲጻፍ ስናይ እንግዲያ'ማ "እነርሱም እርሱን እያ ጅብ፤ ዝራጉኑ ስላሉት ጅብና ደራጎን ሳይሆን አይቀርም" እንደ ማለት፤ ወይም በሉቃ.3:23 አይሁድ የጌታችን አባት እግዚአብሔር አብ መሆኑ ስላልተገለጸላቸው "የዮሴፍ ልጅ" እንዳስመሰሉት ይመስልብናል፡፡

(5.1.6) ደግነቱ ይሁዳው የቤተ እስራኤል ታሪክ ጸሐፊ ስቴቨን ካፕላን (Steven Kaplan ) "... the most common usage of the term ayhud in medieval Ethiopia was as a description of Christian groups viewed ... as heretical. This usage was especially popular in the time of the Emperor Zar'a Ya'eqob, who sought to purge the Church of many of its dissident elements as part of his program of religious nationalism - በመካከለኛው የኢትዮጵያ ዘመን ክርስትና 'አይሁድ' የሚለው ቃል የዘወትር ትርጓሜ 'መናፍቅ' ለሚለው ቃል መገለጫነት ነው፤ ይልቁንም በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ያሉ ልዩነቶችን ሁሉ ማስወገድን እንደ ሃይማኖታዊ ብሔርተኝነት መርሐ ግብር አካል አድርጎ በያዘው በንጉሠ ነገሥት ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን ይህ ቃል ገዝኛ ነበር፤" ብሎ ካብራራ በኋላ ምሳሌ ሲያቀርብም አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ደቂቀ እስጢፋኖስን "አይሁዳውያን" ያላቸው ልክ የገዛ ልጁ ዙፋኑን ሲገለብጥ በሞከረበት ወቅት እምነት አጉዳይነቱን ለመግለጽ በ"አይሁዳዊ"ነት በከሰሰበት መልኩ መሆኑን ይነግረናል፡፡ እንዲህ ሲል፦ "His son Galawdeyos, for example, participated in a failed coup against Zar'a Ya'eqob. He and his fellow plotters, we are told, 'betrayed the king, breaking their oath which they swore to [him] that they would never revolt... Galawdeyos became a Jew, abandoning his Christianity and deny-ing Christ.' Since Galawdeyos was a close ally of the Christian saint and holy man, Takla Hawaryat, there appears to be little question that his alleged 'Jewishness' was political in character.He certainly was not a 'Falasha'; nor were the Stephanite monks whom the same Emperor also condemned as Ayhud - ለምሳሌ ልጁ ገላውዴዎስ በከሸፈ የመፈንቅለ ዘርዓ ያዕቆብ ሴራ ተሳትፎ ነበር፡፡ ታሪኩ እንደሚነግረን 'እርሱ (ገላውዴዎስ) ላለማመጽ የገባውን መሐላውን አፍርሶ ንጉሡን አሳልፎ ሰጥቷል፤ ስለሆነም ክርስቶስንና ክርስትናውን የካደ ይሁዳ ነው' ተብሏል፡፡ ገላውዴዎስ ከክርስቲያኑ ቅዱስና ጻድቅ አባ ተክለ ሐዋርያት ጋር ያለውን ጥልቅ ወዳጅነት[6] እናውቃለንና በይሁዲነት መከሰሱ ፖለቲካዊ መሆኑ እሙን ነው፡፡ በእርግጠኝነት (ገላውዴዎስ) ፈላሻ አልነበረም፤ ንጉሡ በአይሁዳዊነት የሚያወግዛቸው ደቂቀ እስጢፋኖስም እንዲሁ አይሁዳውያን አልነበሩም፡፡"[7]

(5.1.7) ስቴቨን ካፕላን (Steven Kaplan) ያስፈረው ፕ/ር ይስሐቅ ላነሡትና አቡነ ጳውሎስ በቸልታ ላለፉት የደቂቀ እስጢፋኖስን እንቅስቃሴ ከ"ከይሁዲ"ነት ጋር የሚያያዝ አተያይ በቂ ማስተባበያ ይመስለኛል፡፡ በተረፈ ከሐዲስ ኪዳን ጋራ ያልተጣረሱ፤ በግልጽ ያልተከለከሉና ከሐዲሱ ጋር ተጣጥመው የቀጠሉ የኦሪት ትውፊቶችን፤ ሥርዓታትን፤ የቤተ መቅደስ መገልገያ ንዋየ ቅድሳትን፤ የአኗኗር ዘይቤዎችን፤ የካህናትና የደባትር የሲመት እና የአለባበስ ይትበሃሎችን የምንጠቃቅስ ከሆነ ደቂቀ እስጢፋኖስን ብቻ ሳይሆን መላዋን የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ክርስትና ወደ "አይሁዳዊ"ነት እንዳናወርዳት መጠንቀቅ ያስፈልጋል፡፡ በደቂቀ እስጢፋኖስ እንቅስቃሴ የገነኑት እነ አባ ዕዝራ የዘር ሐረጋቸውን "ከጸዮን ጋራ ከወጡ ከሌዊ ነገድ" ተያይዞ ስለ ተተረከና[8]፤ አባ እስክረዙን የጳውሎስን 2ኛ ቆሮ.2:11 ጠቅሶ ስለ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ሲናገር "እኔም እንደ እነርሱ

---

[6] አቡነ ተክለ ሐዋርያት የአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ልጅ ለሆነው ገላውዴዎስ ስለ እመቤታችን ፍቅር እንደ ነገሩትና ምሥጢረ መጻሕፍትን እንዳስተማሩት ተገልጦዋል (ገድለ አቡነ ተክለ ሐዋርያት፡ገ.74)፡፡

[7] Steven Kaplan, Indigeenous Categories and The Study of World Religion in Ethiopia: The Case of The Beta Israel (Falasha),1992, (The Hebrew University, Jerusalem) p.215

[8] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.283

ዕብራዊ ነኝ" ስላለ[9]፣ ቀዳሚት ሰንበትን ስለሚያከብሩና ቅድስት አገር ኢየሩሳሌምን ለመሳለም ስለሚጓዙ[10] ይሁዲ ነበሩ ለማለት መሩጠን፣[11] በግልጽ በቅድስት ሥላሴ[12] እንደሚያምኑ[13] እየተናገሩ፣ ስጊድንም ቢሆን መጀመሪያ ለመስቀልና ለእመቤታችን ለመስገድ ቢያወላውሉም ኋላ ከመስገዳቸውም በላይ ለሥሉስ ቅዱስ ሥዕል ስላለመስገዳቸው ማስረጃ ባልቀረበበት እንዲሁም ከአይሁዳውያን በተለየ ቅዱሳት ሥዕላትን በገድሎቻቸው በስፋት ማኖራቸው እየታወቀ አይሁዳውያን ነበሩ ማለት ተአማኒ አይመስለኝም። ባልታተሙት የአባ ገብረ መሲሕና የአባ ይስሐቅ ገድላት ደቂቀ እስጢፋኖስ ለ"ፈላሾች" ከሌላው ክርስቲያን የተለየ[14] አመለካከት እንደሌላቸው የሚገልጹ ምንባባት መኖራቸውም የይሁዲነት ሐሜታውን ተአማኒ አለመሆን ያሳያል። አባ ይስሐቅ እንዲያውም አበኔዘር የተባለው የትግራይ መስፍን ከ"ፈለስ (ፈላሾች)" ሲዋጋ በጸሎት ረድቶታል።

## 5.2. ደቂቀ እስጢፋኖስ ፕሮቴስታንት ነበሩ?! "በአይቴ ሐሊፈኪ[15]...?"

ይኼኛውን ርእስ ጥበብ በተሞላበት ንግግሩ ነፍሴን ፍጹም በተመስጦ የሚወስዳትና የቋንቋ አገላለጽ ውበቱ ጥሜን የሚቆርጥልኝ አባ አበከረዙን

[9] ዝኒ ከማሁ፡ገ.276

[10] ዝኒ ከማሁ፡ገ.288 እና 289

[11] በደቂቀ እስጢፋኖስ መረዎች አባ አበከረዙንና አባ ዕዝራ ታሪክ ብቻ ሳይሆን በቅዱስ ያሬድ፣ በአቡነ ተክለ ሃይማኖትና በአቡነ ዜና ማርቆስ ገድላት የዘር ሐረግን ከሌዋዊነትና ከእስራኤላዊነት ጋር እያይዞ የመቁጠር ትውፊት በስፋት ይስተዋላል። የአባ አበከረዙንና የቅ/ያሬድ ሐረገ ትውልድ ከነገደም ተለይቶ ፕ/ር ፍቅሬ ቶሎሳ ደጋግመው ከሚጠሩት "መደባይ" ከሚባለው ነገድ እንደሆነ በተደጋጋሚ እናነባለን።

[12] ራሳቸው ፕ/ር ይስሐቅ እንዲሁም ፕ/ር ጌታቸው ደጋግመው እንደ ጻፉት ዘሚካኤል፣ ፍሬ ማኅበር፣ ንግሥታዊ የተባሉ ሰዎች ነበሩ በሥላሴ አንድነትና ሦስትነት ዙሪያ በዘርዓ ያዕቆብ አደባባይ የተለየ አቋም ያራምዱ የነበሩ ተከራካሪዎች።

[13] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.107ና 289

[14] በእስጢፋኖሳውያን ገድላት ስለ እስልምና፣ ስለ ቤተ እስራኤላውያን ይሁዲዎች፣ ስለ አርሞ እንቅስቃሴ፣ ስለ ቱርክ ተደጋግሞ ከሚነገረው ገንና የኖረና ከማዕከላዊት ኢትዮጵያ ወደ ሰሜን እያዘመመ ከሚሄድ ትዕነ የተለየ አቀራረብ አላየሁም። በእነዚህ እርእስት ከዘመኑ ገድላት የተለየ ይዘት የላቸውም።

[15] ስውየው የድጓ ምሩቅ ነው። በዐቢይ ጾም ውዳሴ ማርያም ዜማ ምራ ተባለ። ቀረቡ፣ ጨኸቱ ግን ግራ ሆነ፣ በጉባኤ የሌለ ዜማ አመጣ። አልዋለበትማ! ደባትር ተገረሙ። ጀማሪዎች የሚጨኋት ዜማ ለምምህር ተብዬው ስታቅተው እንዴት አይገረሙ?! በማእዘ ተሳለቁበት፣ ተረት ተረቱበት። "በአይቴ ሀሊፈኪ ድጓ ተምህርኪ - በየት አልፈሽ ድጓ ተማርሽ?" ተረቲቱ ለቈናጽላን ትጠቀሳለች። ጠቀስኳት!



በተናገራት ፍጽምት ኦርቶዶክሳዊት ቃል ልጀምር። "ከድካማቸው ጋር ስትደክም ቅዱሳን አባቶቻችንን ለመምሰል አትድከም"[16] ይላል። ከእርሱ በፊትም አባ እስጢፋኖስ "የመንፈስ መንግሥት ማየት ግን በምግባር እንጂ በነገር አይደለም!" ብሏል።[17] ይህቺ ተደጋጋሚ ቃል ምናኩሶናን እና የምናኔ ሕይወትን እያጣጣሉ መነኮሳቱን (ደቂቀ እስጢፋኖሳውያንን) አባቶቻቸው ለማድረግ ለሚታገሉ ሸጋ ተግሣጽ ናት። አባባሏን በቅዱስ ጴጥሮስ ቃል አጥብቀናት እንለፍ። ቅዱስ ጴጥሮስ በ2ኛ መልእክቱ ምዕራፍ 3፡16 "ወአለ አልቦሙ ትምህርት ወአለ ኢለበው ይመይጥዎ ለቃለ መጽሐፍ - ያልተማሩና የማይጸኑትም ሰዎች ሌሎች መጻሕፍት እንደሚያጣምሙ እነዚህን ደግሞ ለገዛ ጥፋታቸው ያጣምማሉ" ይላል። የገድል አጻጻፍ መውጫና መግቢያ የማያውቁ ፕሮቴስታንት ጸሐፍት ገድላተ ደቂቀ እስጢፋኖስን እንዳይሆን አድርገው ቀነጸሏቸው። ሳያምኑበት ተርጉመው ለአጀንዳቸው ማቀጣጠያ አደረጉት። ዓለም አቀፉ ሚዲያም በእነርሱ ስፖንሰሮች የተቃኘ ነውና መነኮሳቱን ባልዋሉበት የሉተር ሜዳ አዋሏቸው።

የፕሮቴስታንት ጸሐፍት ሲደንቀን የግእዝ ዘይቤ ተምረናል የሚሉና በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ጉባኤ ቤቶች አልፈው ዛሬ "ማሊያ ቀይረው ለተቀናቃኝ ቡድን መጫወት" የጀመሩ "ስመ ተሐድሶ ቁንጽሎች"ም ታማኝነታቸውን ለማሳየት ሌሉ ፍጹም ኢ ሥነ ምግባራዊ ቃላት እየተጠቀሙ ያደጉባትን፣ እስልምና በገነነበት የምሥራቅ አፍሪካ ተራሮች መካከል በአስደናቂ መንገድ ተጋድሎ ፈጽማ ከነክብሯ የኖረችውን፣ ቅዱስ መጽሐፍ በምልዐት ተርጉማ ያቆየቻቸውን እናት ቤተ ክርስቲያን በሉሌንት ለአዲስ ጌታ አድረው ለማነወር እንደበታቸውን ሲያላቅቁ ዓይኖቻችን አዩ። ደቂቀ እስጢፋኖስን ተገን አድርገው ብዙ ጸያፍ ቃላት ለነዘሩ። በበራሪ ጽሑፍ፣ በመጽሐፍና በመጠመሪያ (በብሎግ) ታማኝነታቸውን ለማሳየት ከፕሮቴስታንታውያን በላይ ፕሮቴስታንት ሆነው ባልታረመ ዝርው ብዕራቸው ግዳይ ጣሏት። ይሁን! ግዴለም! ከቆናጽላን ተላላኪዎች (messanger boys) ጋር ንግግር የለንም። ጌቶቻቸውን ግን እንደሚከተለው መረር ብለን እንሞግታለን።

[16] ዝኒ ከማሁ 216. ግእዙ፡- "ኢትፍቅድ ትትመሰሎሙ ለአበዊነ ቅዱሳን በእንበለ ትድከም ምስለ ድካሞሙ" ይላል፤ አባ ገብረ መሲሕም ይህንኑ ቃል ይናገራል። ጥዑም ንግግር!

[17] ዝኒ ከማሁ፡ገ.99

(5.2.1) እድሜ ለእኛ መዘናጋት፣ ለኦርቶዶክሳውያን ኮሌጆችና ለዘመናውያን ወጣቶች ቸልተኝነት ይሁንና መድረክነቱ ለማንም ክፍት በሆነው wikipedia፣ በአፍሪካ ፕሮቴስታንታዊ ክርስቲያኖች ዙሪያ በሚዘግበው dacb.org፥ በቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን የታሪክ መጽሐፍ ደቂቀ እስጢፋኖስ ሉተርን ያስናቁ ቀዳምያን ፕሮቴስታንቶች ተደርገው ቀርበዋል። እነሱ ምን ያድርጉ አሞሌውን ባለቤቱ ሲያቀለው?! ኸረው ብሎ የተከፈተ በር ሲገኝ ቀሳጢ ቢያንጎዳጉድ ምን ይገርማል?! በተለይ የቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን የሥነ መለኮት ኮሌጅ በሆነው በ"Ethiopian Graduate School of Theology (EGST)" ውስጥ "Biography of 'Hadege Anbesa' (Abba Stephanos) of the Orthodox Church," (ዜና ሕይወቱ ለሐድገ አንበሳ - አባ እስጢፋኖስ - ኦርቶዶክሳዊ) በሚል ርእስ ወረቀት የሠሩ "መስፍን ሹጉ" የተባሉ ግለሰብና ቀደም ሲል በአ/አ/ዩ. ፕሮፌሰር ሆነው ከጡረታ በኋላ ለdacb.org ጽሑፍ ሲያዋጡ የነበሩ "ድርሻዬ መንበሩ" የተባሉ እንስት ምሁር 'ደቂቀ እስጢፋኖስ ፕሮቴስታንታውያን ነበሩ' የሚለው አነጋገር ወንዝ የተሻገረ አሉባልታ እንዲሆን ደክመዋል።

(5.2.2) የደቂቀ እስጢፋኖስን ታሪክ "ተቀጣጥሎ የከሰመ ወንጌላዊ መነቃቃት" በሚል ርእስ አንድ ምዕራፍ ሰጥተው ልክ እንደ ራሳቸው ቤተ ክርስቲያን ታሪክ የጻፉት የኢትዮጵያ ቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊዎች የመንፈስ አባታቸውን የማርቲን ሉተር (ታላቁ) እንቅስቃሴ በታላቅ አድናቆት ሲተርኩ ከቆዩ በኋላ "...ከዓለም ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ወደ አገራችን መለስ ስንልም ልማዳዊ ከሆነው አካሔድ ወንጌላዊ ወደ ሆነው እምነት የተራመደ የጎላ እንቅስቃሴ የተከሰተበት ጊዜ ነበር።... ይህ እንቅስቃሴ 'ደቂቀ እስጢፋኖስ' ተሰኝቶ በጀማሪው እስጢፋኖስ ስም ተከታዮቹ ያወጡት መጠሪያ ነበር" ብለው የራሳቸው ያልሆነውን ታሪክ ለመውረስ ይፋጠናሉ።[16] በመቀጠልም "...እንግዲህ እስጢፋኖስ ከሞተ ከመቶ ዓመታት በኋላ ነበር የምዕራብ አውሮጳ ተሐድሶ የተጀመረውና ቀይቶም ወንጌላዊ

---

[16] ወንድዬ ዓሊ፣ "በመከራ ውስጥ ያበበች ቤተክርስቲያን፡ የኢትዮጵያ ቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን ታሪክ"፣ 1990 ዓ.ም.፡ገ.23



እምነት ወደ አገራችን እንደ ገና የገባው" በማለት አባ እስጢፋኖስ ከመነሣቱ በፊት ወንጌል እንዳልተሰበከ የሚያስመስል መመጻደቅ ያስነብቡናል።[19]

(5.2.3) ከላይ ፕ/ር ጌታቸው በጎዳግ ማስታወሻቸውና በመግቢያቸው ደቂቀ እስጢፋኖስን ከሉተራውያን ፕሮቴስታንቶች ጋር ለማዛመድ የሚቃጣቸው አገላለጾች ሳይገኙ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ ፕሮቴስታንት ጸሐፍት ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ የሚያነሡአቸውን የተሳሳቱ ነጥቦች ነካክቻቸዋለሁ። በተለይ ስለ ስግደቱ እና ስለ ሰሎሞናዊ ዘር ጉዳይ አልመለስበትም። የተቀሩትን በስሱ ልያቸው። ፕሮቴስታንቶች በዋናነት ደቂቀ እስጢፋኖስን "አባት" ለማድረግ የሚያነሡአቸው ነጥቦች ደቂቀ እስጢፋኖስ ልክ እንደ ፕሮቴስታንት፦

(1) ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያሉ አዋልድን አይቀበሉም/ አይጠቀሙም፣
(2) "መዳን በማመንና በምግባር ሳይሆን "በማመን በሚገኝ የእግዚአብሔር ጸጋ 'ብቻ' ነው" ብለው ያስተምሩ ነበር፣
(3) ታቦት አይቀበሉም፣
(4) አረማውያን ቤተ ክርስቲያን እንዲገቡ ይፈቅዳሉ፣
(5) በሞተ ሥጋ ለተለዩ ቅዱሳን አይጸልዩም የሚሉ ናቸው።

እንዲህ አድርገው ካመቻቹ በኋላ አባ እስጢፋኖስን "the first African Protestant" (አፍሪካዊ በኩረ ፕሮቴስታንት) እያሉ መፎከሪያ ያደርጉታል።[20] ሰዎቹ ያለ ሜዳቸው ገብተው በማይገባ ተርጉመዋል። ፕ/ር ጥቂት ቢያስቀይሙኝም ስለ ትርጉማቸው የማያቋርጥ ምስጋናዬን እየቸርኩ ከገድላተ ደቂቀ እስጢፋኖስ የሚመዘዙ የመልስ መልሶችን እንደሚከተለው ለመሰንዘር እሞክራለሁ።

## 5.2.4. እውን ደቂቀ እስጢፋኖስ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ባዮች ነበሩን?

(5.2.4.1) በአዋልድ አጠቃቀም ረገድ ጥንቱን ደቂቀ እስጢፋኖስ እንደ ፕሮቴስታንት መጽሐፍ ቅዱሳቸው 66 ብቻ አይደለም። ለማንያ አሐዱ

---

[19] ዝኒ ከማሁ፡ገ.28
[20] Dictionary of African Christian Biography, http://www.dacb.org/stories/ethiopia/estifanos_.html (2005) : October 11,2016

ነው፡፡[21] በአቡነ እስጢፋኖስ ገድል በገጽ 66 መጽሐፈ ሲራክ፣ በገጽ 77 እና 82 መጽሐፈ ሲኖዶስ፣ በገጽ 78 መጽሐፈ ሄኖክ ተጠቅሰው እናገኛለን፡፡ አባ እስጢፋኖስ በገጽ 93 ስለ ሳጥናኤል ከክብሩ መውረድ ለማስረዳትና የአባ ሲኖዳን የምንኩስና ኪዳን ሹሪነት ለማሳየት ተአምረ ኢየሱስን ይጠቅሳል፡፡ ፕሮቴስታንት ጸሐፍት አባ እስጢፋኖስ "Bible Alone" የሚል ነው ሲሉ በሌለ ተዛምዶ ሲዛመዱ ሲንትቱት ደግሞ "የአበው መጽሐፍ ለመነኮሲ ሞትንና ስቅለትን ተስፋ ከማድረግ የሚበልጥበት የለም ያለውን አልሰማህምን?" ይላቸዋል፡፡[22] ፕሮቴስታንቶች "የአበውን መጽሐፍ አያውቁምና መስማታቸውን እንጃ! ባይሆን በስጊዱ ያለንን ተዐቅቦ ጠብቀን እኛው እንስማው!

(5.2.4.2) እኔ ያነበብኳቸው ሁሉም ፕሮቴስታንታዊ ጽሑፎች በደምሳሳው ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ቢተርኩም ብዙ ጊዜ ከገድለ እስጢፋኖስ ተራምደው አይሔዱም፤ በጣም ኀዘዝ ነን ያሉት ወይም ዘርዓ ያዕቆብን በቀጣቱ መሪርነት ለበብ ለማጣጣል ብቻ አልመው የሚነሡት ደግሞ ከገድለ አበው ወአኃው አልፈው አያነቡም፡፡ የአባ አበከረዙንን፤ የአባ ዕዝራንና ያልታተሙትን ሌሎች ገድላት እንደ መስመርም አያነሷቸውም፡፡ ቢያነሷቸውም ስለ ይዘታቸው ትንፍሽ አይሉም፡፡ ገድላቱ በፍጹም ኦርቶዶክሳዊ አስተምህሮዎች ስለ ተሞሉ ለቁንጸላ አይመቹማ! ሁለቱን ገድላት ሊደፍሩአቸው የሚሞክሩት አይሁዳውያን ጸሐፍት ናቸው፡፡

አባ አበከረዙንን 'ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ መጽሐፍ ያስፈልጋል?' ብለው ምስክርነት ቢጠሩት ከአቤል ጀምሮ እስከ ጌታችን የተነሡ የታላላቅ አበውን ዜና መጽሐፈ ኩፋሌን እያጣቀሰ ሲዘክር ይቆይና "...'ከጌታችንም በኋላ... ጴጥሮስ ተሾመ፤ ከእርሱ ቀጥሎ ቀሌምንጦስ... ከጳውሎስ በኋላ ጢሞቴዎስ... ከእነርሱ በኋላ ሊቃውንትና የቤተ ክርስቲያን መምህራን ተነሡ፡፡[23] ጽድቅ እንደዚህ በየትውልዱ ከጻድቃን ወደ ጻድቃን ነፍስ ትሸጋገራለች፡፡ የእግዚአብሔር ነፍስ ለትውልደ ትውልድ ነች እንጂ የአንድ

[21] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ ገ.282 እና 296
[22] ገዚ ከማሁ፡ገ.102
[23] 1ቆሮ 12፡28



ጊዜ ብቻ አይደለችም፡፡[24] ከእነርሱ በኋላ ደግሞ በዘመናችን በትግላችን ጊዜ ረዳት እንዲሆነን እግዚአብሔር አቡነ እስጢፋኖስን አስነሣልን፡፡' ይኸንን ካለ በኋላ ገበራቸውን ያኖሃው ጻድቃን ያሉባቸውን መጻሕፍት እንብቡ እለ' ይላቸዋል፡፡[25] ፕሮቴስታንት ወንድም-እኅቶቻችን "የጻድቃን ዝክር ያለባቸውን መጻሕፍት" ማንበብ የሚያበረታታ አባት "Bible Alone" ብለው ሲቀበሉ አይተንም ሰምተንም አናውቅም፡፡

(5.2.4.3) በአባ አበከረዙን ገድል ገጽ 273 ከፊልክስዩስ ገጽ 219 የተወሰዱ 3 የነፍስ በረከት የሚያስገኙ ተጋድሎዎች ተጠቅሰዋል፤ ምንኵስና፣ ስሟዕትነት እና ጾምና! በገጽ 276 የአባ መቃርስ ሕይወት ለማስተማሪያነት ሲያገለግል እናነባለን፡፡ በገጽ 264 ስለ ሥርዓተ-ምንኵስና "የሥርዓታችሁ መጀመሪያ፡- [1] ነፍስን መጣል፤ [2] ፍላጎትን መተው፤ [3] ገንዘብን አለማከማቸት እንደ ሆነ ታውቃላችሁ፡፡ እነዚህ ሦስቱ የነፍስ ሕንጻ መሠረቶች ናቸው" ይላል አባ አበከረዙን፡፡ በፕሮቴስታንቶች ዘንድ ሥርዓትና ወግ የሚሉ ቃላት ብዙም ቦታ ያላቸው አይመስለኝም፡፡ በስድሳ ስድስቱ መጽሐፍ ቅዱስ ያልተጻፈ ሁሉ "ተረት ነው" ለማት ሲፋጠኑ ነዋ የምናያቸው!

አባ አበከረዙን ከላይ የተገለጸውን ስብከት የወሰደው በኢትዮጵያ ገዳማዊ ሕይወት ከግብጻውያን ይልቅ እጅግ የበረታ አሻራ አላቸው ተብሎ ከሚገመቱት የሶርያ ጽኑዓን/ ጽኑዓት ማኅበረ መነኰሳት ነው ብለን መከራከር ይቻላል፡፡ ምክንያቱም እነርሱም ልክ አባ በአከረዙን እንዳለው ቃል በቃል 'The pius monk seeks to achieve this by observing three vows, which he makes publicly by his own free will. These vows are the following:- (1) Absolute obedience to his spiritual superior. (2) Voluntary poverty, signifying that he may take nothing from the

[24] ምእመን መቃረቡን ሲነግራቸው ድንጋጤ ላይ ለለወደቁ ለማጽናናት ጌታ በማቴ.28፡20 የተናገረውንን "እስከ ዓለም ፍጻሜ ከእናንተ ጋር ነኝ" የሚል ቃል እየተረጐመላቸው ነው - ቃሉ ለእሱ ብቻ ሳይሆን ከእሱ በኋላም ለሚተካው አበምኔት እንደሚሠራ በመናገር፡፡ በነዳማቸው የተገኘው ግእዝ በግእዝ የሚተረጐም እንድምታ ቃሉን፡- "እስከ ሀልቀተ ዓለም እስመ ኢይደሉ ዘንተ ቃለ ለባሕቲቶሙ (ለሐዋርያት)፤ አላ ለኵሎሙ መሃይምናን እለ ሀለው እስከ ኀልቀተ ዓለም - እስከ ዓለም ፍጻሜ ሲልም ለእነሱ (ለሐዋርያት) ብቻ አይደለም፤ እስከ ዓለም ፍጻሜ ለሚነሱ አማንያን ሁሉ እንጂ" ይላል፡፡
[25] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.271

world as his personal property. (3) Chastity, enjoining him never to marry and to remain chaste. These vows are faithful promises that the monk must keep to the end of his life" እንደሚሉ ከፎረ ገጻቸው (ዌብሳይታቸው)[26] ያነበብን ሲሆን ስለ በን ተጽዕኖአቸው ደግሞ የኢትዮጵያን ምንኩስና ያጠኑ ሁሉ ተናግረዋል::[27] ፊልክስዩስም አመጣጡ ከሶርያ ነው::[28] ፕሮቴስታንቶች ይህን የመሳሰለ የመጽሐፈ መነኮሳት አጠቃቀስ ካላቸው ደስታ መሞታችን ነው! ግን አይመስለኝም!

ለተጨማሪ መረጃ ቅድስተ አርሴማን የሚያነሣሳውን የንግሥተ ማርያም ተጋድሎ ከገጽ 127፣ የፃ ሐራ ስማይን ተጋድሎ ከገጽ 144፣ የእንጸኪያን፣ የአርመንያን፣ የናግራንን ሰማዕታት የሚያዘክሩባቸውን ምንባባት ከገጽ 213፣ እንዲሁም ሕጻኑን ቅዱስ ቂርቆስን አርአያ አድርገው ገድላቸውን በጥብዐት ለመፈጸም የተዘጋጁትን እኃው ምንባባት ከገጽ 199 ጋብዘን እንለፍ:: ምንባባቱ ደቂቀ እስጢፋኖስ ገድለ ሰማዕታትን እንደ ዘመነኞቹ ተሐድሶ/ ፕሮቴስታንቶች እንደማያነውሩ ማሳያ ናቸው::

## 5.3.5. ደቂቀ እስጢፋኖስ ስለ መዳን ትምህርት ምን ይላሉ?

(5.3.5.1) Wikipedia ንብረትነቱ የኢትዮጵያ ቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን የሆነው የEthiopian Graduate School of Theology (EGST) ለዎች የሰጡትን መረጃ ይዞ[29] "ደቂቀ እስጢፋኖስ ስለ ነገረ ድኅነት ሲያስተምሩ መዳን የሚገኘው በእግዚአብሔር ጸጋ/ እምነት ብቻ እንጂ በምግባረ ሠናይ

---

[26] http://www.suryoyo.uni-goettingen.de/library/monastic.html :revisited 2016-10-26

[27] የኢትዮጵያን ምንኩስና ሥርዓት ያጠናው ብላሰዊዝ "Ethiopian monasticism is not a faithful image of the style of living of Egyptian eremites, for it has reached Ethiopia through Syrian and Greek monks - ምንኩስናው (ብህትውናው) የመጣው በሶርያና በግሪክ አድርጎ ስለሆነ [የግብጻውያን ተጽዕኖ ባይከድም] የኢትዮጵያ የምንኩስና ሥርዓት የግብጻውያንን ገዳማዊ ሥርዓት አጥብቆ የሚያንጸባርቅ አይደለም" ይላል:: (Blasewicz, p.35.) የምንኩስና (ብህትውና) ሥርዓታችን ከግብፅ በላይ የጠበቀና የጠነከረ ሥርዓት የሚከተልና ከሶርያ የተዛመደ መሆኑ ይነገራል::

[28] የፊልክስዩስ መቅድም::

[29] Mesfin Shuge, "Biography of 'Hadege Anbesa' (Abba Stephanos) of the Orthodox Church," term paper, Ethiopian Graduate School of Theology (EGST), Addis Ababa (May 2001)



እንዳልሆነ ይናገሩ ስለ ነበር "sola gratia - መዳን በጸጋ/ እምነት ብቻ - ከሚለው ፕሮቴስታንታዊ አስተምህሮ ጋር ይዛመዳሉ" ሲል ባልዋሉበት አውሏቸዋል:: ሀቁ ከዚህ በተቃራኒ ነው:: አባ እስጢፋኖስ አፈንጋጭ ኦርቶዶክሳዊ ነው ብንልም እንደ ፕሮቴስታንት "መዳን በጸጋ/ እምነት ብቻ"[30] ባይ ላለመሆኑ አኗኗሩና ንግግሩ ይመሰክራል:: እርሱ ስለ መንኖ ጥሪት "ወፎች ሲያባርሯቸው በቀላል ይበራሉ፤ ምክንያቱም የሸክም ክብደት የለባቸውም:: እናንተም እንደዚሁ... ሳታከማቹ ኑሩ" እያለ ይሰብክ ነበር::[31] እንጂ "አምኛለሁ፤ ጸድቂያለሁ" ብሎ ምንኩስናና ጾም አላስተሐቀረም::

(5.3.5.2) በእርሱ እምነት'ማ ለመዳን ማመን ብቻ ሳይሆን መታዘዝም ግድ ነው:: አባ እስጢፋኖስ እንዲህ ያለ ስሙ ስም ሰጥተው በስሙ ስለሚነግዱ አስተማሪዎች የተናገረው የሚመስለኝ ስብከት አለው:: እስኪ እንስማው:- "እነርሱ ራሳቸውን <u>ለእግዚአብሔር ትእዛዝ</u> ለማስገዛት ካልፈለጉ ሌላው ለእግዚአብሔር እንዳይጠመድ ለምን ይከለክላሉ? 'ልጆቻችን ናቸው' የሚሉት <u>የእግዚአብሔርን ትእዛዝ</u> ሳያስተምሩአቸውና <u>ከኃጢአት የመዳኛ ጸጋ</u>[32] ሳይሰጡዋቸው እንዴት ልጆቻቸው ሆኑ? <u>እነርሱስ ቢሆኑ ራሳቸውን ለቅዱሳን ሐዋርያትና ለተከታዮቻቸው ለመነኮሳት አባቶች ለእንጦንዮስና ለመቃርስ ትእዛዝ ሳያስገዙ የአባትነትን ስም እንዴት ወሰዱ?</u>" ይላል::[33] እንዲያው ዘመዶቻችን ገድል ጠቅሰው ለመጻፍ ሲጥሩ ለምን አናግዛቸውም ብለን እንጂ ነገሩ'ማ "ሃይማኖት ያለ ምግባር ያድናል" ብሎ ቢያምን ኖሮ ዱር ለዱር ምን አደከመው?! "ልጆቼ ከወጣላቸው ቀናና ጋራ ልባቸው

---

[30] "በእምነት መዳን" እና "በእምነት 'ብቻ' መዳን" እጅግ የተለያዩ አነጋገሮች ናቸው:: ያለ ምግባርና ያለ ምሥጢራት ቤተ ክርስቲያን እንዲያው "በእምነት 'ብቻ' መዳን" የሚል ጠባብ ትርጓሜ ማርቲን ሉተር ያመጣው ፕሮቴስታንታዊ ብሒል ነው:: (ያሬጋል አበጋዝ (ዲያቆን)፣ መድሎተ ጽድቅ፣ 2007 ዓ.ም.፣ ገ.188-191::)

[31] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.77

[32] "ከኃጢአት የመዳኛ ጸጋ" የሚለውን ሐረግ ብቻ ቆንጽሎ በመውሰድ ለመከኸት ይሞክራል:: ነገር ግን ይህ ሐረግ:- (1) ጸጋውን "ብቸኛው" የመዳኛ ጸጋ አይለውም:: (2) ከኂሳና ከሥራ ትእዛዛትን ስለመጠበቅና፣ የእንጦንስና የመቃርስን ፈለግ ስለ መከተል ተጽፏል:: የእንጦንስና የመቃርስ በምግባርና በተጋድሎ ያጌጠ እምነት ደግሞ "በጸጋ 'ብቻ' መዳን" በሚል የቅምጥልነት ሕይወት የታጀበ አይደለም:: (3) የተለመደ የሰገድ ተዕቅራችንን ጠብቀን የምናነበው የአባ እስጢፋኖስ ሕይወት በመመጻደቅ ይታማ እንደ ሆነ እንጂ ምግባርን ችላ ያለ አልነበረም:: ስለዚህ ታሪኩ ከነ "በጸጋው 'ብቻ' መዳን" ትረካ ጋር በፍጹም ኅብረት ሊኖረው አይችልም:: አባ እስጢፋኖስ የመዳኛ ጸጋ ሲል እምነቱን ከነትሩፋቱ/ ምግባሩ ነው::

[33] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.81

በሚዛን ላይ እኩል እስኪሆን ድረስ ኑሮአቸው በቃልም በምግባርም ትክክል እንዲሆን" በመንበርነት ለምን ደከመ?![34]

(5.3.5.3) ደቂቀ እስጢፋኖሳዊው አባ እበከረዙን "...ዕውቀት ብቻውን ሰውን አይጠቅመውም፤ ምግባርም ያለ መዓዛ [ፍቅር] አይጠቅምም። ዕውቀት በምግባር ሲጣፍጥ ብዙዎች በመዓዛዋ ይሰበሰባሉ። የክርስቶስ መንጋዎች ልብ ስላላቸው መዓዛ ያለውን እረኛ ይከተላሉ። አሁንም በመጀመሪያ መዓዛችሁን አሳዩ፤ አለዚያ በከንቱ አትድከሙ፤ ለሰውም ዕንቅፋት አትሁኑ፤ የጽድቅ ሥርዓት በሥራ እንጂ በነገር አይታነጽም።.... መጀመሪያ ስለ ሃይማኖት ስለ ምግባር ስለ መፈታቀር አስቡ። ሃይማኖት ትረዳለች፤ ምግባር ታስችላለች፤ ፍቅር ፍጹም ታደርጋለች"[35]፤[36] አክሎም ስለ ምንኩስና ሥርዓት ሲናገር "ለመነኩሴ በሥርዓቱ እንዳለ ከመሞት የሚሻለው የለም። ሥርዓት ለሚሞትላት ነች"[37] ይለናል።[38] እዚህ ላይ ከቶ ምን እንጨምራለን! እርሱ እንዳለው "የጽድቅ ሥርዓት በሥራ እንጂ በነገር አይታነጽም፤ ሥርዓትም ለሚሞትላት ነች"ና ነገር አናበዛም። ምግባር፣ ምንኩስና፣ ሥርዓት የሚሉ ቃላት ከእምነት ጋር በተዋሕዶ ሲቀርቡ ለዘመዶቻችን የቅምጥል ሕይወት አይመቹምና አናደክማቸውም።

(5.3.5.4) በ"ኩኩሐ ሃይማኖት" መጽሐፋቸው መልአከ ብርሃን አድማሱ እንደ ተናገሩት (ከመነሻቸው መጠነኛ አፈንጋጭነት ቢኖራቸውም) እነ አባ እበከረዙን ክርስቶስን የተከተሉት "በእግር" አይደለም፤ "በግብር" እንጂ! "ስሙ" ይላልና እስኪ እንስማው፦ " መነኮሲዎችም ሆናችሁ መነኮሲቶች በመንፈሳዊ አባታችሁ ሥርዓት እንዳላችሁ ብትሞቱ ይሻላችኋል። መጽሐፍ ካብ የሚንድን እባብ ይነክሰዋል[39] ይላል። እንደዚሁ አሁንም ወደ ፈተና

[34] ገዚ ከማሁ፡ገ.96

[35] ገዚ ከማሁ፡ገ.264

[36] አበከረዙንና ዕገዚ የቅዱስ ያሬድን ዜማ ያጣጣሙ ሊቃውንት ሆነው ይታዩኛል። እዚህ ላይ አባ አበከረዙን ስለ ሃይማኖት፣ ምግባርና ተፋቅሮ ያስቀመጠው ቃል ቀጥታ ከቅ/ያሬድ የዘወረደ ለኆ ጾመ ድጓ የተወሰደ ነው። "እስመ ሃይማኖት ትርድዕ፤ ... ወምግባር ታሠልጥ! ... ተፋቅሮ ለዝሉፋ ኢያኃሥር ወኢያወድቅ" ይላል። (ጾመ ድጓ፤1988 ዓ.ም፡ገ.24።)

[37] ዕብ.9:17 "ሥርዓቱሰ ለዘይመውት ጸንአት ይእቲ"

[38] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.266።

[39] መክ.10:8 "ወዘይነሥት ጸቈነ ይነስኮ አርዌ ምድር"



እንዳትገቡና የመንፈሳዊ አባታችሁን ሥርዓት እንዳትንዱ።"[40] በዚህ ቃለ ምዕዳን ላይ ሌላ ነገር መጨመር ድፍረት ሆኖ ይታየኛል። የእሱን ቃል ለማጽናት አንዲት የትግርኛ አባባል ልጥቀስ፦ "ሃይማኖት ብዘይ ግብሪ፤ ጸሎት ብዘይ ፍቕሪ፤ አይፈቱን ፈጣሪ - ሃይማኖት ያለ ምግባር፣ ጸሎት ያለ ፍቅር፣ አይወደውም እግዜር!" አባባሏን በአንድ ጥንታዊ የግእዝ መወድስ እናትማት። ሊቁ ይቀጥሉ...

**መወድስ!**

ጠፈረ ምሳሌ ሰማይ እምከመ ርኢኩ፤
ኢያጸድቅ ለሰብእ ጸሎት እንበለ ፍቅር፣
ወኢይበቍዖ እሚን እመ ኀበ አልቦ ምግባር፤
ዓዲ ኢይደልዎ፤
ትዕቢት ፀሩ ለክርስቶስ በዙር፤
ፍና ትሕትና ዘየሐውር፤
እስመ ኀበ ሀሎ ትዕቢት ህየ ሀሎ ኀሣር፤
እኃውየሂ ከመ ታእምሩ ምሳሌ ዝንቱ ነገር፤
እእዳው ኢይበቍዑ እንበለ አፃብዕ ወአጽፋር፤
ወኢየሜንዩ ምንተ በኀበ ኩሉ ፍጡር፤
እሥናን ባሕቲቶሙ እምኀበ አልቦሙ ከንፈር።

**የቅኔው ትርጉም፦** "ከሰማይ ጠፈር በታች ባለ ምሳሌ (ሁሉ) እንዳየሁት ጸሎት ያለ ፍቅር ሰውን አያጸድቀውም። እምነት ያለ ምግባርም አይበቃም። በትሕትና ጎዳና የሚሔድ የበኩር ክርስቶስ ተጻራሪ የሚሆን ትዕቢትም (ለሰው) አይገባም። ትዕቢት ባለበት ኀሣር አለና። ወንድሞቼ ሆይ! የዚህን ምሳሌ ትረዱት ዘንድ እጆች ያለ ጣትና ያለ ጥፍር አይበቁም/ አይጠቅሙም። በፍጡራን ሁሉ (እንደሚታየው) ከንፈር ካልከለላቸው በቀር ጥርሶች ለብቻቸው አያምሩም!" የሚል ነው። የቅኔውን ምሥጢር ለመረዳት፦ "ሃይማኖት እንበለ ምግባር ምውት ይእቲ - ሃይማኖት ያለ ምግባር ሙት ነው!" የሚለውን የያዕቆብ መልእክት ምዕራፍ 2 ከቍ. 17 ጀምሮ መገለጥ! ወዳጆቻችን በዚያ ሲዘልቁ እኛ ደግሞ በዚህ ታቦታችንን ለማንገሥ እንገባ!

## 5.3.6. ደቂቀ እስጢፋኖስ የኪዳኑን ታቦት አይቀበሉምን?

[40] ገዚ ከማሁ፡ገ.268

(5.3.6.1) ይህን ርእስ ቤተ ክርስቲያን በሰማናት ገጠመኝ እንጀምረው፡፡ ተማሪው ጀማሪ ነው፡፡ አትሮንስ ተዘርግቶ ለንባብ ቀረበ፡፡ ጀመረ፡፡ "ወአውሰአ ኢየሱስ - ኢየሱስም ተናገረ" የሚለውን ንባብ "ወአውሰበ፡ ኢየሱስ - ኢየሱስም አገባ" ብሎት ዐረፈ፡፡ መምህሩ ጮኸ ብለው "ኧረረረ! በዚህስ አይሁድም አላሙት" አሉት ይባላል፡፡ አይሁድ ጌታን ምን ቢከሱት ከዝሙት ጋራ በተያያዘ ስሙን እንዳሥተውት አያውቁም![41] ወደ ቀደመ ነገራችን እንመለስ! አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ደቂቀ እስጢፋኖስን "ታቦት አይቀበሉም" ብሎ ሲከስ አልሰማንም፡፡ በዚህ እርሱም አላማቸው! አፄ ዘርዓ ያዕቆብ አባ እስጢፋኖስን ስለ ታቦት ክብር ሲናገር ሰምቶ በደስታ "ዝስ ሠናይ ውእቱ - ይህስ መልካም ነው!" ከማለት በቀር 'ታቦት አቃለልክ' ብሎ ነቀፌታ አልሰነዘረበትም፡፡[42] እርግጥ እርሱ ካለፈ በኋላ በኢየሩሳሌም የነበሩ ኢትዮጵያውያን መነኮሳት ይህን ዓይነት ክስ አቅርበውባቸው ነበር፡፡ ለክሱ የአባ ዕዝራ መልስ፡- "ታቦት የላቸውም ስለሚሉት ቅድስት ኦሪት የምትለውን ስማ 'ከማይነቅዝ ዕንጨት ቁመቱ አንድ ክንድ ተኩል፣ ወርዱ አንድ ክሩብ የሚሆን ታቦት ሥራ' (ዘጸ.25፡23)፡፡ ታቦት የሁላችን መመኪያ፣ የመላእክትም መመኪያ ማርያም ነች" ይላል "ታቦት በወርቅ ልቡጥ እምኵለሄ ዘግቡር እምዕጽ ዘኢይኔቅዝ" የሚለውን የቅዱስ ኤፍሬም የእሑድ ውዳሴ ማርያም ሁለተኛ ምስጋና እያሰበ፡፡[43] ይህን'ማ ስለ እመቤታችን ለመግለጽ ነው የተናገረው እንዳይባል በገጽ 308 በአባ ዕዝራ ጥረት ግዝት ተነሥቶ ሰላም ከወረደ በኋላ ደቂቀ እስጢፋኖስ ጳጳሱ ፊት ቀርበው 80 ታቦታትን እንዳስባርኩ እና አባ ዕዝራ ለታቦቱ እጅ እንደ ነሳ ተጽፎ እናነባለን፡፡ ገድሉ ገና ያልታተመው አባ ይስሐቅ ዘክስዋ[44] እንዲሁ "ዕቀቡ ታቦታተ እግዚአብሔር ማኅፀንተክሙ - የእግዚአብሔርን ታቦታት በመጠጊያዎቻችሁ ጠብቁ" ይል ነበር፡፡

(5.3.6.2) አባ ዕዝራ አፈንግጦ ነው ይኸን ያደረገው እንዳይባል አባ እስጢፋኖስ በገጽ 100 "ታቦት የሚሆነውም ቅዱስ ሜሮን የተቀባ ዕንጨት ነው፤" ሲል እናገኘዋለን፡፡ በገድለ አበው ወአኃው እንዲሁ ስለ ታቦት እንዲህ የሚል ንባብ አለ፡- "ሲመሽ መልእክተኛ መጣና ካህናቱን ዲያቆናቱን

[41] "ዋሺንጊ ኮድ" የተሰኘ መጽሐፍ የጻፈ ፈረንጅ ግን በክፋቱ አይሁድን በልጦ ተገኘ መሰል!
[42] አባ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዲ፡ገ.134፡፡
[43] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.290
[44] ክስዋ = ጕንዳጕንዲ = ደብረ ገሪዛን



ታቦቶቹን አምጡ' አለ፡፡ 'አንሰጥህም' አሉት፡፡ ታቦታቸውንና ቅዱሳት ዕቃቸውን ነጥቋቸው ሔደ"[45] ደቂቀ እስጢፋኖሳዊው አባ አበከረዙን ለደቀ መዛሙርቱ ከሚሰጣቸው ምክሮች አንዱ "በደረሳችሁበት ሁሉ የእግዚአብሔርን ታቦቶች ሳትይዙ አትሒዱ፡፡ እናንተም በጉዞአችሁ ሁሉ የእግዚአብሔር ኃይል ይረዳችኋል" የሚል ነበር፡፡[46] T/C ጌታቸው በተረጐሟቸው ዐራቱም ገድላት ደቂቀ እስጢፋኖስ ስለ ታቦት ተቃውሞ ሳይሆን ፍቅርና ስገድ ሲያደርጉ ነው በተደጋጋሚ የምናየው፡፡ ብቻ የቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን ሰዎች እኛ ያላገኘነው የደቂቀ እስጢፋኖስ ገድል ያገበኑ ይመስላሉ፡፡ ወይም "ወይመስሎሙ ወልደ የሴፍ" የተባለውን የወንጌል ቃል በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ ለመተርጎም እየታተሩ ነው መሰል፤ "He denied the presence of the Ark of the Covenant in Ethiopia and conducted worship services without the presence of a Tabot (a replica of the Ark of the Covenant) which is mandatory in every Orthodox Church - የቃል ኪዳኑን ታቦት በኢትዮጵያ መኖር አያምንም፤ አምልኮ የሚፈጽመውም በእያንዳንዱ የኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ሊኖር ግድ የሆነው ታቦት በሌለበት ሁኔታ ነበር፤" እያሉ ስንገሰሮቻቸውን ያስደስታሉ - ያልተጻፈ እያነበቡ፤ ያልተባለ እየተረጎሙ!

(5.3.6.3) በዚሁ ገጽ "Abba Estifanos objected to the worldly authority of the monks - አባ እስጢፋኖስ መነኮሳት ያላቸውን ዓለማዊ ሥልጣን ይቃወም ነበር" ይላሉ፡፡ ጥሩ! የመነኮሳትን ዓለማዊ ሥልጣን አያበረታታም ለማለት ከሆነ ጥሩ! በመናዝዝ (የማሰርና የመፍታት) ሥልጣን አያምንም ለማለት ከሆነ ግን ተለያየን፡፡ እንላለን - 'በእይቴ ሐሲፊኪ ድግ ተምህርኪ?" - እንላለን! "አባ" የሚለው መዓርግ ከየት ተገኘ?

ከዚህ ሁሉ ገድሉን በጽሞና ብናነበው፡- አባ እስጢፋኖስን በገጽ 59 ለካህን ሲናዘዝ፤ በገጽ 72 ቅስና ሲቀበል፤ ልጆቹን በሚመለከት አባ ገብረ ክርስቶስ ከአባ ተወልደ መድኅን (ሁለቱም ገድል አላቸው) ንስሐ ሲቀበል በገጽ 121፤ በገጽ 129 ቃል በቃል በጳጳስ እንደሚያምኑ ሲናገሩ፤ ስለ በዓላት እና ሰንበታት አከባበር በገጽ 77፤ የቅዱሳን አባቶችን ገድላት መጻፍ፣ ማስጻፍ፣ ማንበብ፣ መስማት ስለሚያስገኘው ጸጋና በረከት ገጽ 115 እና እንዲሁም በገጽ 213 እና አባላቸው ያረፈበትን ኢጋጣሚ በገለጹበት የንባብ ክፍል ሁሉ፣ ስለ ለሙታን ተዝካር ስለ ለሙታን ቍርባን ስለ ማስቆረብ በገጽ 133፤

[45] ዝኒ ከማሁ፡ገ.150
[46] ዝኒ ከማሁ፡ገ.257

ማውጣትና ስለ ጸሉተ ፍትሐት በገጽ 131ና 132፣ ስለ ማዕተብ፣ ቆብና ጥምጥም አጠባበቅ ሥርዓታቸው በገጽ 153፣ 200ና 203፣ ወዘተ... በስፋው ስላለ ደቂቀ እስጢፋኖስን ከፕሮቴስታንታውያን ደምሮ ማሰብን ሕሊናዬ አሺ ብሎኝ አያውቅም" ወንድሞቻችን ግን የእኛን ቤተ ክርስቲያን ታሪክ ለመጻፍ ሲሉ ደከሙብን! ላይ ቤትና፣ ታች ቤት ተራወጡ! ለድካማቸው እንዲት ተረትና ምሳሌ እናበርክት፡- "ሁለት ዛፍ ላይ ያረፈች ወፍ፣ ሁለት ክንፏን ትነደፍ!" ጓዶች ተሰብሰቡ! መቀላወጥ ነውር ነው!

## 5.3.7. ደቂቀ እስጢፋኖስ ያልተጠመቁ አረማውያንን ቤተ ክርስቲያን ያስገቡ ነበርን?

"ወይመስሉሙ ወልደ ዮሴፍ" የምትለዋ ፋላሲ (ማደናገሪያ) ሐደቷን ቀጥላለች። ዘመዶቻችን በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ በተቀዋሚዎቻቸው የተሰነዘረውን ክስ እንዳለ እየወሰዱ ስም መስጠቱን ቀጥለውበታል። "ደቂቀ እስጢፋኖስ ያልተጠመቁ አረማውያንን ቤተ ክርስቲያን ያስገቡ ነበር" ይሉናል ከላይ የጠቀስናቸው ምንጮች። ይኼንን ጥያቄ አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ነበር በክስ መልክ ለአባ እስጢፋኖስ ያቀረበለት። ጥያቄውንና መልሱን ከገድሉ ገጽ 100 እንደ ወረደ እናቅርብ፤ "አረማውያን ከቤተ ክርስቲያን እንደምታስገባ ሰማሁ... እውነት ነው ወይስ ውሸት?" ብሎ ንጉሡ ጠይቆት አባ እስጢፋኖስ ሲመልስ "አረሚ ቀርቶ በአፋቸው ክርስቲያን ነን የሚሉትን እንኳን በሕገ ፊስግ ካልሔዱ ከምሥዋዕችን [ከቁርባናችን] አናካፍልም" ነው ያለው።[47] ይህ

[47] ያልተጠመቁ አረማውያን ቤተ ክርስቲያን እንዳይገቡ ክልከላ ማድረግ የተለመደ ይመስላል። (ገድለ አቡነ ዜና ማርቆስ፡ገ.290።) መጽሐፈ ሲኖዶስ (መንበረ ፓትርያርክ ቤተ መጻሕፍት ውስጥ የሚገኝ) በአንቀጽ 12 "ወአንተ ከመ ኢይትወከፉ መነሂ እምአረሚ በቤተ ክርስቲያን - በቤተ ክርስቲያን ማንንም ቢሆን ከአረሚ እንዳይቀበሉ" ይላል። አፄ ዘርዓ ያዕቆብ በመጽሐፈ ብርሃን "ዘየሐውር ኀበ አምልኮ ባዕድ ... ኢይባእ ውስተ ቤተ ክርስቲያን፤ ወኢይምጻእ ውስተ መካነ ትምህርት ዘእንበለ ያፍትን ርእሶ ለካህን፤ <u>እስመ እምኮኑ ኃጢአት የአኪ አምልኮ ጣዖት</u> - ወደ ባዕድ አምልኮ የሚሄድ ... ቤተ ክርስቲያን ውስጥ አይግባ፤ ራሱን ለካህን ካላስመረመር በቀር ትምህርት ወደሚሰጥበት ጉባኤም አይምጣ፤ <u>ከኃጢአት ሁሉ የጣዖት አምልኮ ይከፋልና፤</u>" ይላል። (ከላይ በተጠቀሰው ቤተ መጻሕፍት የሚገኝ መጽሐፈ ብርሃን፡ብራና ቅጠል 48)። ያም ሆኖ የአረሚው አመጣጥ ሥርዓተ ቤተ ክርስቲያን አፍቅሮና ለመቀበል ተዘጋጅቶ ከሆነ ተቀብሎ ማስተማር እንደሚገባ ዘርዓ ያዕቆብ ይገልጻል፤ "ለአረሚኒ <u>ለእመ መጽአ አፍቂሮ</u> ይባእ ውስተ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ... <u>ወኢይቤልዎ ኢንትወከፈከ፤ እስ ይሜህርዎ ፈጣሪሃ እግዚአብሔር አምላክ</u> - አረሚም ቢሆን ወደ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ይገባ ዘንድ ወድዶ ከመጣ አንቀበልህም አይበሉት፤ ፈጣሪ እግዚአብሔር አምላክ መሆኑን ያስተምሩት እንጂ፤" ይላል። (መጽሐፈ ብርሃን፡ብራና ቅጠል 77።) የዚህ ድንጋጌ መጽሐፋዊ መነሻው 2ኛ ዮሐ ቁ.9-10 ላይ ያለው "ለሚወጣ ኹሉ <u>በክርስቶስም ትምህርት ለማይኖር ሰው አምላክ</u>



በፕሮቴስታንት ወንድሞቻችን የእንግሊዝኛ አንድምታ ሲተረጎም "He allowed heathens to enter the church building (እሱ - አባ እስጢፋኖስ - አረማውያን ወደ ሕንጻ ቤተ ክርስቲያን እንዲገቡ ይፈቅድ ነበር።" ገድሉ የሚለው ግን "ከምሥዋዕችን አናካፍልም" እንጂ "ይፈቅድ ነበር" አይደለም። <u>"አናካፍልም - allowed"</u> ተብሎ በተቃርኖ ከተተረጎመ ትርጉም በእንብርክ ሔደች!

## 5.3.8 ደቂቀ እስጢፋኖስ (ባረፉ) ቅዱሳን ስም አይማጸኑምን?

(5.3.8.1) ይህቺን ጥያቄ መልሶ በጥያቄ መመለስ ይቻላል። ባረፉ ቅዱሳን ስም ካልተማጸኑ ገድሎቻቸው በሙሉ ለምን "አባ እስሌ መሥዋዕትንትን ተቀበለ፤ እማሆይ እከሊት፤ ዐረፈች በረከት ረድኤታቸው ይደርብን!" ይላሉ? ገድላቱ ከሜፍ እስከ ሜፍ በዚህ ዓይነት መደምደሚያዎች የተሞሉ ናቸው። ያነባቸው ይፍረደኝ! የታተመ ማስረጃ ግድ ከተባለ ግን በገጽ 140 <u>"...የአምላክ እናት ማርያም ሆይ! እነሆ ከምሕረትሽ ጥላ ሥር ተደግፈናል፤ በጭንቀታችን ጊዜ ልመናችንን አትናቂ..."</u> ተብላ የለፈረችውን ንባብ እንጠቅሳለን። እርሱ ተደጋገመ ከተባለም በአባ እስጢፋኖስ ገድል ገጽ 113 ከመቃብሩ ፈውስ መገኘቱን የሚገልጸው ክፍልና አባ ዕዝራ ሲያርፍ "መመኪያ እንዲሆነን ሥጋውን ስጡን!" የሚል የገጽ 313 ንባብ ደቂቀ እስጢፋኖስ ባረፉ ቅዱሳን በክርስቶስ ሕያው መሆንና ከእኛ ከምድራውያኑ ጋር ኅብረታቸው አለመቋረጡን ማመን ንሉህ ማሳያ ነበር። ያም ሆኖ ፕሮቴስታንት ፀሐፍት ከአባ እስጢፋኖስ ትምህርቶች አንዱ "Rejection of prayer to dead saints and angelic beings - ባረፉ ቅዱሳንና በመላእክት መማጸንን አለመቀበል ነበር፤" ይሉናል! ደግነቱ ሁሉም የደቂቀ

<u>የለውም</u>፤ በክርስቶስ ትምህርት ለሚኖር አብና ወልድ አሉት። ማንም ወደ እናንተ ቢመጣ ይህንም ትምህርት ባያመጣ <u>በቤታችኹ አትቀበሉት</u> ሰላምም አትበሉት።" የሚለው ቃል ነው። እንደ ቅዳሴው ሥርዓት ከአረማዊነት ተመልሰው የተጠመቁትም እስከቡቶ ድረስ በቅዳሴ ኢንግሊዝ (ፍሬ ቅዳሴ ከመጀመሩ በፊት) "ጻዑ ንኡሰ ክርስቲያን" ሲባል እየወጡ ነን ሰንን ትምህርትና ቀኖናቸውን ሲጨርሱ ሙሉ ለሙሉ ይቀላቀላሉ። የአባ እስጢፋኖስ አካሳጽ እስጢፋኖሳውያን በሥርዓተ ቅዳሴና ቁርባን አፈጻጸም ረገድ ከነባሩ የቤተ ክርስቲያን ትውፊት የተለየ አስተምህሮ እንደሌላቸው ያሳያል። ከአባ እስጢፋኖስ ህልፈት በኋላም ተከታዮቹ በሐዋርያት ሥርዓት ለማይሄድ ሰው ከቁርባናችን አናካፍልም የሚል አቋማቸውን ቀጥለዋል። (ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ገ.151።) ኢምስጣቴዎሳውያንም እስከ 1459 ዓ.ም. በሰንበት አይሁድ/ ቀዳሚት ሰንበት/ ከርክር የተነሣ እንደ አይሁድ ተቆጥረው ከቁርባን ይለዩ ነበር። (የቤተ ክርስቲያን መዝገብ ቃላት፤ ቅጽ 9፡ገ.161።) ይኼኛው መለያየት "ወንድሞች ሆይ፥ ከእኛ እንደ ተቀበሉት ወግ ሳይኾን <u>ያለ ሥርዐት ከሚኼድ ወንድም ኹሉ ትለዩ ዘንድ በጌ ታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እናዛችኋለን።"</u> የሚለውን የ2ኛ ተሰ.3፡6 ቃል መሠረት ያደረገ ይመስላል።

እስጢፋኖስ ገዳማት በእመቤታችን ስም ናቸው።[48] የአባ ዕዝራ እናት ባሏ ከሞተ በኋላ የተጸናናቸውም በቅዱስ ሚካኤል ቤተ ክርስቲያን መሆኑ በገድሉ ተገልጹዋል።[49]

(5.3.8.2) ብቻ ለዘመዶቻችንን ዝንጋኄ ዘለፋ እንዲሆን በሚመስል መልኩ የገድለ አበው ወእኃው ጸሐፊ የእመቤታችንን፣ የመላእክትን፣ የቅዱሳንና እና ሰማዕታትን አማላጅነት እየተማጸነ በአራኀራኂ ቃል ገድሉን ባሳረገበት ሐረግ ልደመድመው፤ "በደብ ፀር ዘመን... ሰማዕትነታቸውን በመልካም ሰማዕትነትና በመንፈሳዊ ገድል ከፈጸሙት ውስጥ ቍጥራቸውን ያወቅነው የቅዱስ ብፁዕ እስጢፋኖስ ወንድና ሴት ልጆች ሰማዕታትና ጻድቃን ጠቅላላ ድምር 1004 ነው። የማናውቀውን እርሱ ንብረቱን ይሰብስብ።... ይኸንን ለእኛና ከእኛ በኋላ ለሚመጡ ማስታወሻ እንዲሆን እንዳገኘነው ጻፍነው። <u>በእምላክ እናት በቅድስት ድንግል ማርያም ልመና፣ በትጉሃን መላእክት ሁሉ ጸሎት፣ በቅዱሳንና በሰማዕታት ሁሉ ጸሎት እግዚአብሔር የረድኤታቸውን በረከት ይስጠን</u>፣ አሜን፣ አሜን፣ አሜን"[50]

**ደቂቀ እስጢፋኖስ በየዘመናቱ ያንጸባረቁትን አቋም ከተሐድሶ/ ፕሮቴስታንትና ጸንቶ ከኖረው የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ትውፊት ጋር ለማነጻጸር የሚረዳ ሰንጠረዥ**

| | ፕሮቴስታንት | ተሐድሶ | አባ እስጢፋኖስ | አበው ወእኀው | አባ ዕዝራ | የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. |
|---|---|---|---|---|---|---|
| የሰማያ አንዱን መጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና መቀበል | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ሁሉም ካህን ነው | √ | √ | X | X | X | X |
| ለሥዕለ ማርያምና ለመስቀል መስገድ | X | X | X | ከጊዜ በኋላ በጳጳሱ አቡነ ገብርኤል ምዕዳን/ ምክር ሰገዱ | √ | √ |
| በዘብረ ድንግልና አማላጅነት ማመን | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ጸሎተ ፍትሐትና ተገቢር | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ቍርባን (ሥጋ ወደሙ) | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ታቦት ላይ ቀድሶ መሥዋዕት ማሳረግ | X | X | √ | √ | √ | √ |
| መዳን በእምነት "ብቻ" | √ | √ | "ብቻ" አይደለም X | X | X | X |
| ባረፉ ቅዱሳን አማላጅነት ማመን | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ሰንበትንና በዓላትን ማክበር | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ቅዱሳት መካናትን መሳለም | X | X | ግልጽ አይደለም | √ | √ | √ |
| በጾምና በጸሎት ድንጋኄ ማመን | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ማማተብና ማዕተብ ማድረግ | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ውዳሴ ማርያምን መድገም | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ቤተ ክርስቲያን በእመቤታችን ስም መሰየም | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ገድላትን የመጻፍና የመቀበል ትውፊት | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ምንኩስናን ከነ ድንጋጌው መቀበል | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ዶግማና ቀኖና ማክበር | X | X | √ | √ | √ | √ |
| የተጻፈ ሥርዓተ ቅዳሴ | X | X | √ | √ | √ | √ |
| ጥሬ ቃልን ብቻ ሳይሆን ትርጓሜን መከተል | X | X | የጸጋ ስግደት ላይ ብቻ ፈደላዊ የሆነ ይመስላል | በጸጋ ስግደት ላይ ፈደላዊ የነበሩ ቢሆንም ኋላ ተስተካክሏል | √ | √ |

√ ይቀበላሉ X አይቀበሉም

[48] በተደጋጋሚ ከሚጠቀሱት የእስጢፋኖሳውያን ገዳማት ውስጥ ጕንደጕንዶ ማርያም፣ ዲቦ ማርያምና አሲራ መቲራ ማርያም ገዳም ይገኙባቸዋል። (ካሕሳይ፡ገ.53።) በለሙን ሁማማት ስግደት ወቅት የገዳሙን የስግደ ሥርዓት በመቅረጽ ፕሮቴስታንታዊ ለማስመሰል በሚቃጣው ሙከራ እንኳ ገዳማውያኑ በሁማማት ሰሞታ ውስጥ ያለውን በአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ የተደረሰ እመቤታችን የተመለከተ ሰሞታ ሲያደርሱ ይታያሉ፣ ይሰማሉ።

[49] ደቂቀ እስጢፋኖስ፡ ገ.281

[50] ይህ ሐረግ የአብዛኞቹ እስጢፋኖሳውያን ገድላት ማሳረጊያ ነው።

# ምዕራፍ ስድስት

# መደምደሚያና አስተያየት

6.1. የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ ቢነቀፍም ቢወደስም የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ታሪክ ነው ብዬ አምናለሁ! ስለ ሆነም ታሪኩን አይሁዳዊ ወይም ፕሮቴስታንታዊ ገጽታ መስጠት ፍጹም በደል ነው እላለሁ! በእኔ በኩል አቡነ ጳውሎስ እንደ ሠየሙት እንቅስቃሴው "አፈንጋጭ ኦርቶዶክስ /heterodox/" ቢባል እመርጣለሁ። ታሪኩን ያለ ቅጥ ገፍቶ፣ ከቅጽራችን አስወጥቶ ለውጹአን መጠቀሚያ ማድረግ ያሳምመኛል! የቀሰቀሰኝም ይኼው ሕማም ነው!

6.2. እርግጥ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከ1421 - 1492 ዓ.ም. ለሰባ አንድ ዓመታት ለእመቤታችንና ለመስቀል መስገድን ይቃወሙ እንደ ነበር በብዙኃኑ የታሪካቸው አጥኚዎች አልተካደም! በመሆኑም ቀደም ሲል ውግዘት ተላልፎ ነበር የሚለውን አመለካከት እቀበላለሁ፤ እናገራለሁ!

6.3. ነገር ግን ውግዘቱ በሊቀ ጳጳሳችን አቡነ ይስሐቅ በአፄ ናዖድ ዘመን ጥር 21 ቀን 1492 ዓ.ም. ከተፈታ በኋላ ምዕመኑና ካህኑ ውስጥ የሠረፀው እነሱን በጥርጣሬ የመመልከት ሁኔታ ሙሉ ለሙሉ ባይቀረፍም ደቂቀ እስጢፋኖስ በሒደት በፍጹምነት ለኦርቶዶክሳዊት እምነት ቆመዋል፤ ይህንንም በግራኝ ዘመን ካህናተ ደብተራን ሳይቀር በትግራይ ተራሮች ጉያ በተመሠረቱ የእመቤታችን ገዳማቶቻቸው በማስጠለል ከቀደመ ጎዳናቸው መመለሳቸውን አሳይተዋል ብዬ አምናለሁ!

6.4. ለሰባ ዓመታት አካባቢ የቆየውን ውግዘት መቀበሌ እንዳለ ሆኖ ንጉሥ ዘርዓ ያዕቆብ ስመ መንግሥቱ ቆስጠንጢኖስ ሆኖ ሳለ ታላቁ ቆስጠንጢኖስ አርዮስን በመሰለ መናፍቅ ላይ ያላደረገውን እጅግ መራር ቅጣት በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ መፈጸሙ በቅዱሳት መጻሕፍት አንጻር ተገቢ ነው ለማለት ይከብደኛል። በመንፈሳዊ ጉዳዮች ላይ ኃይል የተቀላቀለበት ቅጽርን የመጋፋት ሁኔታ እስካልተከሰተ ድረስ ከውግዘት ባለፈ የሚፈጸምን አካላዊ ቅጣት አለመቃወም ድርጊቱ ዛሬም ቢፈጸም ሲበረታታ እንደሚችል ጠቋሚ አድርጌ አየዋለሁ!

6.5. የዘመናችው አገራዊ ብሔርተኝነት በኦርቶዶክሳዊ ቃና መቀሬቶ የሚያሳድረው ተጽዕኖ ሳይዘነጋ ቀደምት አባቶቻችን ቢችሉ የቀደመ ዘመናትን የውግዘት ሒደቶች አብነት በማድረግ የዘርዓ ያዕቆብ ን ድርጊት



ከውግዘት ወዲያ አካላዊ ቅጣት የለም ሲሉ ቢቃወሙ፣[1] ተተኪዎችም በአካል ባይደርሱበትም ታሪኩን በሙገሳ ከማጉላት ከፉውን ከበጎ ለይተው ቢተቹት ኖሮ በአፄ ሱስንዮስ[2]ና በ1870 ዓ.ም. በቦሩ ሜዳ ጉባኤ በነ ዘርዓያዕቢ እንገዳ ላይ በአፄ ዮሐንስ አራተኛ[3] አማካይነት የታየው ምሳስ የመቁረጥ ድርጊት አይፈጸምም ነበር ብዬ ስለምገምት በአባቶች እርምጃ[4] ቅር ይለኛል!

---

[1] እርግጥ አባ ተክለ ሐዋርያት በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ የተፈጸመውን ገደብ የተላለፈ ቅጣት ስለ መቃወማቸው ተጽፏል (ዲ.ን. ዳንኤል ክብረት፣ የቤተ ክርስቲያን መረጃዎች፣ገ.70።)

[2] አፄ ሱስንዮስም አፍንጫና ጆሮ ይቆርጥ ነበር (የአፄ ሱስንዮስ ዜና መዋዕል፣ገ.171።)

[3] በአፄ ዘርዓ ያዕቆብና አፄ ዮሐንስ አራተኛ መካከል የሚገርሙ መመሳሰሎች አሉ። (1) ሁለቱም በተወለዱ በ35 ዓመታቸው የተረከቧት ኢትዮጵያ ማዕከላዊ አስተዳደሯ መሰነጣጠቁ የጀመረ ገና ያልተጠናከረች፣ የሃይማኖት ክርክር የበዛባት፣ ክርስቲያኑ ክፍል በሙስሊም ኃይሎች እንዋጣለን ብሎ የሚሰጋባት ኢትዮጵያ ነበረች። (2) የሁለቱም ሚስቶች በጥምቀት ወደ ክርስትና የመጡ ሙስሊሞች ናቸው። የዘርዓ ያዕቆብ ሚስት ንግሥት ዕሌኒ ከሀዲያ ሙስሊም ገዥ መደብ ናት፤ የአፄ ዮሐንስ ሚስት ዳቶ ሃሊማ (Dato Halima) ወይም በክርስትና ስሟ ጥበበ ሥላሴ ከአፋር የእብንአላ ጎሣ የተገኙት ጥንተ-ሙስሊም ናት። እርግጥ አፄ ዮሐንስ እንደ ዘርዓ ያዕቆብ ዕቁባት በማብዛት ሲታሙ አላየሁም። (3) ሁለቱም ነገሥታት በአመራራቸው የኦርቶዶክሳዊ ክርስትና ሃይማኖታዊ ብሔርተኝነት የተጫናቸው ሆነው ይታያሉ። (4) ሃይማኖትን በጉባኤ የማስወሰንና በሒደቱም ከሌሎች ነገሥታት በተለየ ጉዳ ተሳትፎ የማድረግ አካሄድ ተከትለዋል። (5) በሃይማኖታዊ ውሳኔ ከውግዘት ባለፈ አፍንጫን የመፎነን፣ ምላስን የመቁረጥና ከንፈርን በስለት የመሸርከፍ እርምጃ ወስደዋል። (6) በአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዘመን ትምባሆ ስለ ማጨስ ክርክር እንደ ነበር ሊቀ መዘምራን ሞገስ ዕቁበ ጊዮርጊስ ጽፈዋል። በአፄ ዮሐንስ ዘመን እንዲሁ ትምባሆ ማጨስ ከንፈር የሚያስቆርጥ ወንጀል ሆኗል። (7) ሁለቱም ለስብከተ ወንጌል ካላቸው ቀናኢነት የተነሣ ከአንድ በላይ ገዳማት አስመጥተዋል። አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ሁለት ሲያስመጡ፣ አፄ ዮሐንስ በዘመናቸው በራት ጳጳሳትን ከግብጽ አስመጥተዋል። (8) ከኢየሩሳሌም የኢትዮጵያ ገዳማት ጋር ጠንካራ ግንኙነት አላቸው። (9) ምርኮዎቻቸውን በብዕዕት ለቤተ ክርስቲያን ይሰጣሉ። አፄ ዘርዓ ያዕቆብ ከሀዲያው ገራድ የማረኩውን ለየገዳማቱ ያድል ነበር። አፄ ዮሐንስም ከግብጾች የማረኩትን ወርቅ ለኢየሩሳሌሟ ደብረ ገነት ኪዳነ ምሕረት ማስሰሪያ አበርክተዋል። ሁለቱም በየዘመናቸው የደብረ ሊባኖስን ገዳም እንደ አዲስ ሠርተውታል።(10) ማዕከላዊው የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ሲኖዶስ ከጥልቅ አክብሮት (አክብሮቱ የሁላችንም ነው!) ውጭ በይፋ የሰጠው ቅድስና ባይኖርም ለቤተ ክርስቲያን ያበረከቷቸውን አስተዋጽኦዎች በማየት አፄ ዘርዓ ያዕቆብን በጻድቅነት፣ አፄ ዮሐንስን በሰማዕትነት ሲደመው በተናጠል (ወዲታን ለመግለጽ) እንደ ቅዱሳን የሚጠሩዋቸው ሰዎች አሉ።

[4] ጉዳት ከደረሰ በኋላ ቢሆንም አፄ ዮሐንስ በቦሩ ሜዳ ጉባኤ ላይ የወሰዱትን እርምጃ ሰዉን ቲዎፍሎስ "በእንተ ርትዕት ሃይማኖትነ ኢይደሉ ንክዐው ደመ ካልእነ፤ አላ ንክዐው ደመ ዚአነ - ስለ ቀናች ሃይማኖት የሌሎችን ደም ማፍሰስ አይገባንም፤ የኛን ደም እናፍስስ እንጂ" ብለው አስቁመዋል። (ሥርግው፣ እሚ.መዝ.ቃላት ቅጽ 4፣ገ.185)። መሪር እስከወልድም የአፄ ዮሐንስን በወሎ ሙስሊሞች ላይ የተሰነዘረ ዘመቻ አስቁመው በምትኩ "መማር ይቅደም" ብለው በወሎ ሙስሊሞች ላይ በሐዋርያነት ተሹመዋል። (አለቃ ተክለ ኢየሱስ፣ የኢትዮጵያ ታሪክ፣ 2ኛ እትም፣ 2008 ዓ.ም.፣ገ.262)።

6.6. ከዚሁም ባሻገር አባቶቻችን ታሪኩን ከግራ ቀኝ አጣርተው ከመጻፍ ይልቅ በአንድ አቅጣጫ ብቻ ያለውን እየሰሙ ሲተርኩ መኖራቸው፣ እንዲሁም ከሙ አሰጣጥ ላይ ሳይጠነቀቁ ደቂቀ እስጢፋኖስ ለእመቤታችንና ለመስቀል ለመስገድ እምቢተኛ ስለ ሆኑ ብቻ "አይሁዳውያን" እና "ፕሮቴስታንት" እንደ ዘበሩ አድርገው ባገኙትና ስማቸውን ያከፋልናል ባሉት ስም ሁሉ ለመጥራት መቁጠናቸው[8] የኋላ ኋላ እነዚህ ሁለት ኃይላት ታሪኩን እንዳሻቸው ያለ ሀይ ባይ እንዲቀነጸጽሉት በር ከፍቷል ብዬ አምናለሁ!

6.7. በዚህ ረገድ ምንም እንኳ በመግቢያቸውና በአንዳንድ የጎዳ ማስታወሻዎቻቸው የገድላቱን መንፈስ ፕሮቴስታንታዊ ቃና በማላበስ አረዳድ አዛብተዋል የሚል ቅሬታ ቢኖረኝም አረጋዊው ፕሮፌሰር ጌታቸው ኃይሌ ገድላቱን በመተርጎም ግራ ቀኝ አይተን ታሪኩን በባለቤትነት መንፈስ ለመረዳትና ለመተረክ በማመቻቸት ታላቅ ውለታ[7] ሠርተዋል እላለሁ! ድርሻቸውን ተወጥተዋል! ከንፈታችን የተቆረጠውን ዛፍ የማስመለስ ኃላፊነት የእኛ የአዳዲሶቹ ውሉድ እና አዋልድ ይሆናል!

6.8. የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ በቤተ ክርስቲያናችን በባለቤትነት ስሜት አልተጠናም። በመሆኑም ከአንዳንድ የቤተ ክርስቲያን የቅርብ ሰዎች እንዲህ ዓይነት ጹሑፍት ሲወጡ ገዢ ትችት ሳይዘነጋ ቢበረታታ የተገባ ይሆናል። ታላላቅ የሚባሉ እንደ አቡነ መልከ ጼዴቅ (የአሜሪካው) ዓይነት አበው

[5] ጉዳዩ ከዓለማዊ ሕግ ጋር ቢያያዝም እንደ አገር በአፄ ኃይለሥላሴ ዘመን፣ በ1949 ዓ.ም. በወጣው የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ አንቀጽ 120 እና 128 በቅደም ተከተል "ግርፋት"ና "ሽት ግዞት" ከወንጀለኛ መቅጫ መንገዶች ውስጥ ነበሩ። ሰውን በስቅላት መቅጣም አንዱ የወንጀል ቅጣት ማስፈጸሚያ መንገድ ነበር። በዚህ ዐይን ከታየ ስለአፄ ዘርዓ ያዕቆብና ለአፄ የሐንስ! ለሌሎችም የቀደሙ ነገሥታት የምሕረት አተያይ ይኖረናል። ስነገሩ አሁንም ቢሆን የተጠርጣሪና የአስረኛ መብት ይዞታችን የሚያኩራራ አይደለም።

[6] ከተዋሕዶ ያላቸው የምሥጢረ ሥጋዌ ትርጉሜ፣ የበዐላትና የአጽዋማት ድንጋጌ ልዩነት እንደ ተጠበቀ ሆኖ የየት መጣ ታሪኩ ቢያጨቃጭቅም በትውፊት ፍጹም ከካቶሊክ የሚለዩትን፣ ሁለት ዓለርይ ባለማለትና መንፈስ ቅዱስ ከወልድም ሠረፀ ባለማለት ከካቶሊካውያን የማይመሳሰሉትንና እንዲያውም ልዩነን አጥብቀው የሚያወግዙትን ቅብዐቶችና ጸጋዎች እንዲሁ ካቶሊክ ብለን ለመፈረጅ እንቻኮላለን። በዚህ የተነካ ካቶሊካውያን የጸጋዎችና የቅብዐቶች ደጋፊ መሰለው ነቀፋ በመሰንዘራቸው መ/ብ እድማሱ በመድሎተ አሚን መጽሐፋቸው ካቶሊክ ከቅብዐትና ጸጋ የሚለይበትን ለማንጠርና ለቁንጸላ በር ሳለመከፈት ብዙ ደክመዋል። ስም አወጣጥ ላይ ጠንቃቆች የሆንን አይመስለኝም። ከብሒላችን ያልገጠመ ሰው ሲገጥመን ሁሉንም የጉፋቄ ስም ማሸከም ራሳችን ላይ የተጻራሪዎች ግንባር ማደራጀት ነውና እናስብበት፣ ደቂቀ እስጢፋኖስ ለፕሮቴስታንት አስተምህሮ እጅግ ሩቅ ናቸው!

[7] የፕ/ር ትርጉም በቅዱሳት መጻሕፍት ቁርኝት ረገድ ከገዳሙም ትርጉም የላቀና የሰፋ ነው። ሆነ ተብሎ ይሁን በአጋጣሚ ባላውቅም የገዳሙ ጉትመት የእስጢፋኖሳውያንን ንግግሮች ከትክክለኛ የአዋልድ ምንጮቻቸው በማቁረኘት ረገድ ደክሞብኛል።



ፕሮፌሰር ጌታቸውን[8] እንዲሁም የተወሰኑ ሰዎች ዲያን ዳንኤል ክብረትን የመሰከሰኛው ዘመን ቅዱሳንን ገድላት ሲተረጉሙ "የነገሥታቱን ስም አጥፍተዋል" የሚል ክስ እናነባለን። አልስማማበትም፣ ቅዱስ ዳዊትንና ንጉሥ ሰሎሞንን ያከል ታላላቅ ነገሥታትም ከጠንካራ ጎናቸው ጎን ለጎን ደካማ ታሪካቸው ሰፍሯል። በመጻፉ ተምረንበታል። የእኛ ነገሥታትም ታሪክ በዚያ መልኩ በጎና ጸያፍ ተግባራቸው መጻፍ አለበት ብዬ አምናለሁ። ታሪኩን ከሚያነቡና ከሚሰሙ ሰዎችም በተቻለ መጠን ታሪኩን ግራ ቀኙን ለማገናዘብ ቢሞክር ደስ ይለኛል። እንደማየው ታሪኩ በሁሉም ጽንፍ ያለው አቀራረብ ሕሊናን የሚፈታተን ነውና በተቻለ መጠን የተገናዘበ አመለካከት ቢኖረን!

6.9. ታሪኩ መንፈሳዊ ይዘቱ እስኪጠፋ ድረስ እጅግ ፖለቲካዊ እንዲሆን መደረጉ ከቶም አያስደስተኝ! ለእመቤታችን፣ ለመስቀልና ለቅዱሳት ሥዕላት የሚደረግ የጸጋ አክብሮትና ስግደት ከፕሮቴስታንቱ ክፍል ውጭ በብዙኃኑ የዓለም ክርስትና ክፍል የሚሰጠው ቦታ ላቅ ያለ መሆኑ እየታወቀ በነ አባ እስጢፋኖስ የተነሣውን የ'እንስግድም' ሃይማኖታዊ አመጻ በቅጣቱ መሪርነት ሽፋፍኖ ፖለቲካውን፣ የአስተዳር ሥርዓቱን ድክመትና አምባ ገነንነት ብቻ የማጉላት አካሄድ ይስተዋላል። ምናልባት የደቂቀ እስጢፋኖስ ገድላት ተርጓሚው የፕ/ር ጌታቸውና እንቅስቃሴውን ያጠኑት ሌላኛው ምሁር ፕ/ር ታደሰ ታምራት ምሁራዊ ቁመና ከፍ ማለት የእነሱ፦ "እስመግባቱ የተፈጠረው እስጢፋኖሳውያን የዘመኑን መነኮሳት በነገሥታት አደባባይ የመታደም አካሄድ ስለ ተቹና ለአፄ ዘርዓ ያዕቆብ 'አምባገነናዊ' አገዛዝ ስላልተመቹ ብቻ ነው" የሚመስል ግላዊና ደምዳሚ አመለካከት ዓለማዊ ምሁራንን ታሪኩን ገደብ ባለፈ መልኩ እጅግ ፖለቲካዊ እንዲያደርጉት የገፋፋ ይመስለኛል። የቅዱሳት ሥዕላት ጉዳይ በ7ኛውና በ8ኛው ክፍለ ዘመን በቢዛንታይን ግዛት ብዙ ያወዛገበ ቀኖና እንደ መሆኑ መጠን በኛ አገርም የ'እንስግድም' አመጻው በራሱ ሊፈጥረው የሚችለው ውዥንብር ባይዘነጋና ቸል ባይባል ደስ ይለኛል።

::::::::::::: ተፈጠመ :::::::::::::

[8] ጌታቸው ኃይሌ፣ እንዳፍታ ላውጋችሁ፣ገ.280።

# ዋቢ መጻሕፍት


ሀ. በአማርኛ የተጻፉ መጻሕፍት

1. ሉሌ መላኩ (ሬ/T/C)፣ "የቤተክርስቲያን ታሪክ"፣ 1986 ዓ.ም.፣ ንግድ ማተሚያ ቤት። አዲስ አበባ።
2. "መጽሐፈ ቀሌምንጦስ ዘሮም"፣ ትርጉም በገ/ዮሐንስ ገ/ማርያም፣ 2000 ዓ.ም.። አዲስ አበባ።
3. "መጽሐፈ ጤፉት"፣ ትርጉም፣ በመሪጌታ የማነ ብርሃን ደሴ፣ የግሸን ደብረ ከርቤ ቅድስት ድንግል ማርያም ደብር ሰበካ ጉባኤ፣ መጋቢት 2006 ዓ.ም። አዲስ አበባ።
4. "መጽሐፈ ቅዳሴ"፣ በግእዝና አማርኛ ከነ ምልክቱ፣ ሁለተኛ ኅትመት፣ 1998 ዓ.ም.፣ ዘአንተም ገብረ ሥላሴ ብርሃኑ ዘብሔረ አክሱም። አዲስ አበባ።
5. "መጽሐፈ ቅዳሴ"፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1988 ዓ.ም.፣ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት። አዲስ አበባ።
6. ሰሎሞን ዮሐንስ (ዲያቆን)፣ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ወርቃማ ዘመናት"፣ 2001 ዓ.ም.።
7. ሥርግው ሀብተ ሥላሴ (ዶ/ር)፣ "አማርኛ የቤተ ክርስቲያን መዝገበ ቃላት"፣ ቅጽ 3፣ 4፣ 5፣ 6፣ 9፣10፣ 11ና 12። (ያልታተመ)።
8. በአቡነ ገሪማና ሌሎችም፣ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን ከልደተ ክርስቶስ እስከ ፳፻ (2000 ዓ.ም.)"፣ 2000 ዓ.ም.፣ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት። አዲስ አበባ።
9. "ተአምረ ማርያም"፣ 1987 ዓ.ም.፣ ተስፋ ገብረ ሥላሴ ማተሚያ ድርጅት። አዲስ አበባ።
10. ተክለ ኢሱስ ዋቅጂራ(አለቃ)፣ ሐተታ በዶ/ር ስርግው ገላው፣ የኢትዮጵያ ታሪክ፣ 2000ዓ.ም.፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ድርጅት
11. አሰባቸው ኬሪሚሶ እና ሳሙኤል ሀንዳሞ፣ "የሐዲያ ሕዝብ ታሪክና ባህል"፣ ሐምሌ 2002 ዓ.ም.። አዲስ አበባ።
12. አቡነ እስጢፋኖስ ዘጕንዳጕንዶ፣ 1996 ዓ.ም.፣ ዘአንተም መምህር ወማኅበር ዘጕንዳጕንዶ ደብረ ገሪዛን ማኅበር።
13. እንዳዓለም ዳግማዊ (መምህር)፣ "ወላዲተ አምላክ በነገረ ድኅነት"፣ 1998 ዓ.ም። አዲስ አበባ።
14. እድማሱ ጀንበሬ (መልአከ ብርሃን)፣ "ኵሎሐ ሃይማኖት"፣ 1949 ዓ.ም። አዲስ አበባ።
15. ኪዳነ ወልድ ክፍሌ (አለቃ)፣ መጽሐፈ ሰዋስው ወግስ፣ 1948 ዓ.ም፣ አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት፣ አሳታሚ ደስታ ተክለወልድ። አዲስ አበባ።
16. ካሕሳይ ገብረእግዚአብሔር፣ "ምንኩስና በኢትዮጵያ ዛሬና ትናንትና"፣ 2000 ዓ.ም.። አዲስ አበባ





17. "ገብረ ነገሥት"፣ ግእዝና አማርኛ፣ ትርጉምና አርትዖት በስርግው ገላው (ዶ/ር)፣ 1994፣ አ/አ/ዩ. የኢትዮጵያ ቋንቋዎች ጥናትና ምርምር ማዕከል። አዲስ አበባ።
18. ወንድዩ ዓሊ፣ "በመከራ ውስጥ ያበበች ቤተክርስቲያን፡ የኢትዮጵያ ቃለ ሕይወት ቤተ ክርስቲያን ታሪክ"፣ 1990 ዓ.ም.፣ የኢ/ቃ/ሕ/ቤ.ክ. የሥነ ጽሑፍ አገልግሎት። አዲስ አበባ።
19. ዓለሙ ኃይሌ፣ "የአፄ ዘርዓ ያዕቆብ ዜና መዋዕል (1418 - 1452)"፣ 2007 ዓ.ም.፣ ሲራክ አሳታሚ ድርጅት።
    - "የአፄ ሱስንዮስ ዜና መዋዕል (1597 — 1625)"፣ 2005 ዓ.ም.
20. የግዕዝ ቅኔያት፣ 1ኛ መጽሐፍ፣ 1980 ዓ.ም፣ አዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ ቋንቋዎች አካዳሚ። አዲስ አበባ
21. ያሬጋል አበጋዝ (ዲያቆን)፣ መድሎተ ጽድቅ፣ 2007 ዓ.ም.
22. ይልማ ደሬሳ፣ "የኢትዮጵያ ታሪክ በ16ኛው ክፍለ ዘመን"፣ 3ኛ እትም፣ 2007 ዓ.ም.።
23. ዳንኤል ክብረት (ዲያቆን)፣ "ዐራቱ ኃያላን"፣ 2006፣ አግዮስ ኅትመት። አዲስ አበባ።
    - የቤተ ክርስቲያን መረጃዎች፣ 1999 ዓ.ም.፣ አሳታሚ ማኅበረ ቅዱሳን፣ ሜጋ ማተሚያ ቤት። አዲስ አበባ።
    - ውዳሴ መስቀል ዘአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ 2006፣ አግዮስ ኅትመት። አዲስ አበባ።
24. "ድጓ"፣1988 ዓ.ም.፣ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት።
25. ዶናልድ ሌቪን (ትርጉም በሚሊዮን ነቅንቅ)፣ "ትልቋ ኢትዮጵያ"፣ 2007 ዓ.ም.፣ አዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ ፕሬስ። አዲስ አበባ።
26. ገብረ ሥላሴ ወልደ አረጋይ (ጸሐፌ ትእዛዝ) ፣ "ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ"፣ 22008 ዓ.ም.፣ አሳታሚውና ማተሚያ ቤቱ ያልተጠቀሰ።
27. ገ/ዮሐንስ ገ/ማርያም፣ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ታሪክ፣ በ16ኛው ክፍለ ዘመን"፣ 1992 ዓ.ም.።
28. "ገድለ አባ ተክለ ሐዋርያት"፣ አሳታሚ የዐጋት መድኃኒ ዓለም የአባቶችና የእናቶች አንድነት ገዳም፣ ጢስ ዓባይ ማተሚያ ቤት።
29. "ገድለ አቡነ ዜና ማርቆስ"፣ 2ኛ እትም፣ 2005 ዓ.ም.፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት። አዲስ አበባ።
30. "ገድለ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ እና ገድለ አባ በጸሎተ ሚካኤል"፣ ትርጉም ኃይለ እግዚእ አሰፋ (መ/ሐ) እና ሌሎች፣ 2004 ዓ.ም.፣ አሳታሚ ማኅበረ ቅዱሳን። አዲስ አበባ።
31. ጌታቸው ኃይሌ (T/C)፣ በግል ሕይወቴ ከደረሰውና ካጋጠመኝ፡ እንዳፍታ ላውጋችሁ፣ 2ኛ ዕትም፣ 2006 ዓ.ም. ግራፊክ አታሚዎች። አዲስ አበባ።
    - "ባሕረ ሐሳብ፡ የዘመን ቆጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋር"፣ 1993 ዓ.ም.፣ ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ)።


CamScanner

- "ደቂቀ እስጢፋኖስ በሕግ አምላክ"፣ መጀመሪያ ዕትም፣ 1996 ዓ.ም.፣ ሁለተኛ ዕትም፣ 2007 ዓ.ም. ኮሌጅ ቪል ሚኒሶታ፣ አሳዬ ፕሬስ።
32. ጎርጎርዮስ (ብፁዕ አቡነ)፣ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን ታሪክ"፣1986 ዓ.ም.፣ 2ኛ እትም፣ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት።
33. "ጸሎተ ድጓ"፣ 1988፣ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት።
34. ፍስሐ ያዜ፣ "የኢትዮጵያ የ5ሺህ ዓመት ታሪክ"፣2004 ዓ.ም.። አ.አ።

ለ. የእንግሊዝኛ ጽሑፎች

1. Encyclopedia Aethiopica, Volume 2, 2007, Harrassowitz.Wiesbaden
2. Encyclopedia Aethiopica, Volume 3, 2007, Harrassowitz.Wiesbaden
3. Encyclopedia Aethiopica, Volume 4, 2010, Harrassowitz.Wiesbaden
4. Encyclopedia Aethiopica, Volume 5, 2014, Harrassowitz.Wiesbaden
5. Encyclopedia of Christian Theology, 2005, New York, London
6. Encyclopedia of Eastern Orthodox Christianity Edited by John Anthony McGuckin , 2011
7. Gawdat Gabra , et'al, The A to Z of the Coptic Church, The Scarecrow Press, Inc. Lanham • Toronto • Plymouth, UK 2009.
8. Taddesse Tamrat, "Some Notes on the Fifteenth Century Stephenite 'Heresy' in the Ethiopian Church," 22 (1966.), Addis Ababa University, IES Library.pp.103-115

ሐ. ከድረ ገጽ (መጀመሪያ እ.ኤ.አ. መስከረምና ጥቅምት 2015 ዓ.ም.፣ በመቀጠል እ.ኤ.አ አሁንም መስከረምና ጥቅምት 2016) ከተገኙ (ስለ ሶፍት ኮፒ) ማጣቀሻዎች ውስጥ ዋና ዋናዎቹ

1. Ephraim Issac, A New Text-Critical Introduction to Mashafa Berhān with a Translation of Book I. Leiden: E. J. Brill, Netherland, 1973
2. Denis nosnitsin, New Branches of the Stephanite Monastic Network? Cases of Some Under-Explored Sites, Hamburg University, 2013, pp.57-83
3. Getachew Haile, Aethiopica 14 (2011), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, Praises of the Cross, Wedase Masqal, by Aba Giyorgis of Gasecca ውዳሴ፡መስቀል, pp.47-120
_ Bulletin of the School of Oriental and African Studies, University of London, Vol.43,No.2(1980)., pp.207-234



_ "The Cause of [E]stifanosites: A Fundamentalist Sect in the Church of Ethiopia", Paideuma, Bd 29(1983),pp.193-119.
4. John of Damascenus (ዮሐንስ ዘደማስቆ), Apologia Against Those Who Decry Holy Images, http://www.documentacatholicaomnia.eu/03d/0675-0749,_Joannes_Damascenus,_Apologia_Against_Those_Who_Decry_Holy_Images,_EN.pdf
5. Krzysztof Piotr Blasewicz, Ethiopian Monasticism,1999,Institute of Oriental Studies Warsaw University, Pp.31-46
6. Maimire Mennasemay (Hagos G), The Dekike Estifanos: Towards an Ethiopian Critical theory January 22, 2013 ethiopiawinote https://ethiopiawinote.wordpress.com/2013/01/22/the-dekike-estifanos-towards-an-ethiopian-critical-theory/
7. Paulos (Aba), Filsata: The Feast of the Assumption of the Virgin Mary and the Mariological tradition of the Ethiopian Orthodox Tewahido Church, 1988, unpublished, Princeton Theological Seminary
8. Steven Kaplan, Indigeenous Categories and The Study of World Religion in Ethiopia: The Case of The Beta Israel (Falasha),1992, (The Hebrew University, Jerusalem)
https://oca.org/reflections/fr.-steven-kostoff/before-thy-cross-we-bow-down-in-worship
_ "The Falasha and the Stephanite: An Episode from 'Gadla Gabra Masih'", Bulletin the School of Oriental and African Studies, University of London, Vol.48, No.2 (1985),pp.278-282.
9. Stanisaw Chojnack, Aethiopica 5 (2002), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, "Notes on a Lessor Known Marian Iconography in 13th and 14th Century Ethiopian Painting", p.42-66
10. Veronika Six, Aethiopica 2 (1999), International Journal of Ethiopian and Eritrean Studies, "Water — The Nile — And Taamra Maryam, Miracles of Virgin Mary in the Ethiopian Version" pp.53-68
11. https://mesfinwoldemariam.wordpress.com/2012/04/02/2-april-2012-1855/
12. https://en.wikipedia.org/wiki/Abba_Estifanos_of_Gwendagwende
13. http://www.dacb.org/stories/ethiopia/estifanos_.html http://www.suryoyo.uni-goettingen.de/library/monastic.html
14. https://tezetaethiopia.wordpress.com/2005/06/01/the-chronicle-of-the-emperor-zara-yaqob-1434-1468/

15. http://www.newadvent.org/cathen/07664a.htm
http://www.antiochian.org/content/no-graven-image-icons-and-their-proper-use

16. UTSC Library, Digital Scholarship Unit, Gunda Gunde Manuscripts, Hill Museum & Manuscripts Library (HMML)
http://digitalscholarship.utsc.utoronto.ca/projects/islandora/object/gundagunde%3Apublic?f[0]=mods_subject_topic_ms%3A%22Ethiopian%5C%20Manuscripts%5C%20from%5C%20the%5C%20Monastery%5C%20Gunda%5C%20Gunde%22&f[1]=RELS_EXT_isMemberOfCollection_uri_ms%3A%22info%5C%3Afedora%5C/gundagunde%5C%3Apublic%22

# ክፍል ፮

## ጥንተ አብሶ ከነጓዙ - "አንጽሐ" ወይስ "ዐቀባ"? ከሚለው የሊቃውንት ክርክር ጋር

*"… ስለ ተሰጣትም የእግዚአብሔር ጸጋ የሔዋን መርገም በእርሷ ላይ ተቋረጠ፡፡ እንዲህ ያለ ስጦታ ለአዳምና ለዘሩ እስከ ዘላለም ለሌላ አልተሰጠም"*
*አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ መጽሐፈ ምሥጢር፣ ገጽ 163*

# መግቢያ

ይህቺ ጽሑፍ ከብዥታና ቅሬታ ተወለደች፡፡ ዕድለኛ ነኝ፡፡ በቅርቤ የዕድሜ ታላላቅና የዕድሜ እኩያ የትርጉሜ መጻሕፍት መምህራን ወዳጆች አሉኝ፡፡ ብዥታዬን ነገርኋቸው፡፡ አስረዱኝ፡፡ ነገሩኝ፡፡ ንግግራቸው ባያጠግበኝም ፍንጭ ሰጡኝ፡፡ የሰጡኝን ፍንጭ ተከትዬ ጠብሰቅ ያለችውን የአባቴን የመደርደሪያ ውርስ (ሼልፍ) ዳሰስኩ፡፡ ድረ ገጾችን ፈተሽኩ፡፡ ማስታወሻዬ ተጠራቀመ፡፡ አቀናጀሁት፡፡ ሲቀናጅ ጓዝ ብዙ ሆነ፡፡ ጓዙ አላስጨነቀኝም፡፡ ያስጨነቀኝ በግራ ቀኝ ክርክር ዘለፋ ጋር ተቀላቅሎ የሚሰነዘሩ ቁም ነገሮችን ለይቶ ማውጣት ነው፡፡ ያስጨነቀኝ የራሴን ሽራፊና ቀዳሚ አተያይ ገድቤ የተከራካሪዎችን ነጥቦች በንጹሕ ልቡና ለመረዳት መሞከር ነው፡፡ ሞከርኩ፡፡ የግል አቋሜን በተቻለኝ መጠን ከስሜታዊነት ድምጸት ራቅ አደረግሁ፤ አቋሜን መግለጼ ግን አልቀረም፡፡ ስገልጽ በጨበጣ አይደለም፡፡ ያገኘሁትን ማስረጃና አመክንዮ ተጠቅሜያለሁ፤ አስቀምጫለሁ፡፡ ከድረ ገጽ የተገኙ ምንጮችን አካትቼ በአካል አግኝቼ የዳሰስኳቸውን መጻሕፍትንም በጽሑፉ ግርጌ ዘርዝሬያለሁ፡፡ የድረ ገጽ የመረጃ ገጸ በረከቶችን ያልዘረዘርኩ ወትሮም የተለጠጠውን ጽሑፍ ይብሱ አስፍተው በጉዞዬ ጓዜን እንዳያበዙት ነው፡፡ ጉዞዬ ስለ ጥንተ አብሶ ለማወቅ የምትቃትት አንዲት ኦርቶዶክሳዊት ነፍስ ጉዞ ተደርጎ ይወሰድልኝ፡፡

ጓዜን በአምስት አርእስት ለመሸከፍ ሞክሬያለሁ፡፡ ጽሑፉ ዘለግ ስለሚል በየአርእስቱ የሚነሡ ነጥቦች በተቻለ መጠን ለብቻቸው ቢነበቡም ስሜት እንዲሰጡ ለማድረግ ደክሜያለሁ፡፡ አርእስቱ፦

1. ጥንተ መርገምን ለመረዳት፤ ጥንተ ነፍስን ማወቅ፤

2. የጥንተ አብሶ ትርጓሜ፤ ምንነት፤ ውጤትና ድምሳሴ፤

3. የእንጽሐ ቡድን፦ እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት፤ የጠፋላት በበሥራቷ ጊዜ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነው፤

4. የዐቀባ ቡድን፦ ስትፀነስ ጀምሮ መንፈስ ቅዱስ በጥንተ አብሶ ምክንያት ከመጣው መርገም ጠብቋታል፤ አበሳው አልነካትም፤



5. በእንጽሐ እና በዐቀባ የእርስ በእርስ ክርክር መካከል የሚሰነዘሩ ያልተስማሙኝ አባባሎች፤

ከላይ በቀረቡት አርእስት ዙሪያ ብሔራውያንና የውጭ አገር በተለይም ካቶሊካውያን፣ ግሪካውያን/ ምሥራቃውያንና የኦሪየንታል ክርስቲያናት በተለያየ ማዕረግ የሚገኙ ሊቃውንት የጻፏቸውን አብዛኛ ይዘታቸውን[1] ሳላዛባ ለማቅረብ እሞክራለሁ፡፡ ደጋግሜ እንደምለው በሒደቱ ራሴን የዳኛ ተመልካች አላደርግም፡፡ ያቅሜን ተሳትፎ አደርጋለሁ፡፡ ቢያንስ የሚስማማኝን አሳብ እየመረጥኩ እሰለፋለሁ፡፡ መንገዴ እንዲያምርልኝ የፈጣሪዬን አጋዥነት የወላዲቷን ልመና ተስፋ አደርጋለሁ፡፡ ቀጠልኩ…

[1] ጥንተ አብሶ፦ (1) ቃል በቃል በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ስላልተጠቀሰና በቀጥታውያን ዓለም አቀፍ የሊቃውንት ጉባኤያትም ስላልተወሰነ ለግላዊ ትንተና - speculation - የተጋለጠ ነው፡፡ (2) ከጠባብ መነሻ - ከሮሜ. 5:12 - ተነስቶ በትርጓሜና በሐተታ ስለሚሰፋ ከሱ ይልቅ አናቱ እየከበደ የሚሄድ ርእስ ነው፤ ሐረጉን በዕውቀት ቁጥር ይዞ የሚመጣው ግዝ ብዙ ነው፡፡ (3) ብዙኃኑ የምሥራቅም ሆነ የምዕራብ ጸሀፍት ከራሳቸው ነባር ትውፊትና የአሁኑ የግል አስተሳሰብ እየተነሡ ስለሚጽፉት (በአንድ ጥልቅ አንባቢ ታላቅ ወንድሜ አነጋገር - ሰውን እንዳልጠቅስ "ቢቃስ መሆኑንም ገዝቻለሁ" ስላለኝ ነው - "ሁሉም በራሱ ነባር እርሾ ላይ ርእሱን ስለሚያቦካው") ከኦርቶዶክሳዊው የተዋሕዶ ክበበ ገሪና ሳንወጣ እስከተቻለን ድረስ በሰፊ ልቡናና በተለያየ አንጻር ማየት የተገባ ነው፡፡

# ምዕራፍ አንድ

# ጥንተ መርገምን ለመረዳት፣ ጥንተ ነፍስን ማወቅ

ሰው ማለት "ተሰብአ" ('ብ' ይጠብቃል) "ሰባት ሆነ" ከሚለው ግስ የወጣ ስም ነው፤ ምሥጢራዊ ትርጉሙም "ሰባት ባሕርያትን የያዘ" ማለት ነው ብለው ይተረጉሙታል ሊቃውንት።[1] ሰባቱ ባሕርያት የተባሉ፡- የሥጋ ዐራቱ ባሕርያት ማለትም (1) መሬት፣ (2) ውኃ፣ (3) እሳትና (4) ነፋስ፤ የነፍስ ሦስቱ ባሕርያት (1) ነባቢነት (ቋንቋ)፣ (2) ለባዊነት (ማገናዘብ) እና (3) ሕያውነት (ዘለዓለማዊነት) ናቸው። ሰው ከሌሎች ግዑዛን እና ደመ ነፍሳውያን ፍጥረታት የሚለየውና በእግዚአብሔር አምሳል ተፈጥሯል የሚባለው በዋነኛነት በእነዚህ የኋለኞቹ የነፍስ ባሕርያቱ መሆኑ ሲነገር የኖረ ነው። ከሰው በቀር ቋንቋ ያለው፣ በጥልቀት የሚያገናዝብ ሕያው ፍጥረት በምድር ላይ የለም። እንዲያ ቢባልም ግብራቸው ሁሉ በተዋሕዶ ነው፤ ነፍስ ያለ ሥጋ ለብቻዋ የምትሠራው ምድራዊ ሐኬትም ሆነ ትሩፋት የለም። "ዘእንበለ ሥጋ፡ ኢትቀውም፡ ነፍስ" እንዲሉ አበው።

ይህ ከሆነ የነፍስ አፈጣጠር እንዴት ነው? ነፍስና ሥጋ ተዋሕደው ሰውን "ሰው" የሚያሰኙት መቼ ነው? የሚሉ ጥያቄዎችን ማየት ግድ ይሆናል። ቅድመ ቀራንዮ (ዓለም በክርስቶስ ቤዛነት ሳይድን) ሰው ሲፀነስ/ ሲወለድ ነፍሱ ከአዳም መርገም የተነሣ ጸጋ ጎድሏት ትገኝ ነበር ካልን አስቀድሞ አፈጣጠሯን ማወቅ አይከፋም። የወሊድ መቆጣጠሪያ ዘዴዎችንና ጽንስ ማቋረጥን ከሃይማኖት አንጻር ለመበየንም የነፍስን አፈጣጠር ማወቅ ቁልፍ ነው። ያለተራክቦ ዘር በማፍሰስ ዙሪያ ለሚነሡ ጥያቄዎች ምላሽ ለመስጠት እንዲሁ የነፍስን አፈጣጠር ማወቅ ያስፈልጋል። ይሁን እንጂ የእኔ ትኩረት ጥንተ አብሶን ብቻ ማዕከል ያደረገ በመሆኑ የነፍስን አፈጣጠርም ከርእሱ ጋር በተገናኘ ብቻ ለማየት ነው። በዚህ ርእስ ዙሪያ የተብራራ ግን የተለየ

[1] አክሲማሮስ ዘኤጲፋንዮስ (1999 ዓ.ም.)፣ የዓርብ፡ ገ.151



ትረካ ባቀረቡልን የአገራችን ኦርቶዶክሳውያን ሊቃውንትና መጻሕፍት እተኩራለሁ።

## 1.1. "እንደ ሥጋችን ነፍሳችንም ከአባትና እናት ትገኛለች"

(1.1.1) አባ መልከጼዴቅ ካበረከቱልን መጻሕፍት ውስጥ በ1994 ዓ.ም. አሜሪካ ከሔዱ በኋላ የጻፉት "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን እምነትና ትምህርት" የሚል መጽሐፍ ይጠቀሳል። በዚህ መጽሐፍ ከገጽ 131 - 141 ስለ ሰው አፈጣጠር በጠቅላላው በተለይ ደግሞ ስለ ነፍስ አፈጣጠር ሰፋ ያለና የጠለቀ ትንታኔ "መዝገበ ሃይማኖት" የተሰኘውን መጽሐፍ ዋቢ በማድረግ ያቀርባሉ። እርሳቸው በመጽሐፋቸው እንዳሰፈሩት ስለ ነፍስ አፈጣጠር ሦስት ዓይነት አመለካከቶች ይስተዋላሉ፡-

1ኛው አመለካከት፡- "ነፍስ ቀድሞ የነበረች ናት፤ መዝገበ ነፍሳት [የነፍሳት ግምጃ ቤት - warehouse of souls] አለ፤ በዚያ ትኖራለች። አንድ ሰው በተወለደ ጊዜ ግን አንድ ነፍስ ይሰጠዋል" የሚል ነው።

2ኛው አመለካከት፡- "ነፍስ በየጊዜው ትፈጠራለች፤ አንድ ሰው ሲወለድ አዲስ ነፍስ ይፈጠርለታል፤" የሚል ሲሆን

3ኛውና እሳቸው ኦርቶዶክሳዊ ብለው እንድንከተለው የሚመክሩን አመለካከት ደግሞ "ነፍስ አንድ ጊዜ የተፈጠረች በሥጋም ያደረች ናት።... ነፍስ አንድ ጊዜ ተፈጥራለች፤ ከዚያ በኋላ ግን ትራባለች፣ ትባዛለች እንጂ አስቀድማ ተፈጥራ የቆየች በኋላም በሥጋ የምታድር አይደለችም። ከሥጋ ጋር እንደ ሥጋ ትራባለች። እንደ ሥጋችን ነፍሳችንም ከአባትና እናት ዘር ይገኛል።..." የሚለው ነው።[2]

መልአከ ብርሃን አድማሱ ጀንበሬ በተመሳሳይ፡- "ከአዳም ዘርዕ፣ ከሔዋን ደም ሲከፈል ነፍስም አብራ ተከፈለች፤ ደምና ዘርዕ ተቀላቅለው ተዋሕደው ቀስ በቀስ ሥጋ፣ አጥንት፣ ጅማት፣ ጠጕር ወደ መሆን ሲራመዱ ነፍስም በበኩሏ

[2] አባ መልከ ጼዴቅ፣ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን እምነትና ትምህርት፣ 1994 ዓ.ም.፡ ገ፣135

ቀስ በቀስ ሥጋዊ አካል ወይም ገላ ወደ መሆን መራመድ የጀመረውን ጽንስ በማንቀሳቀስ የሕይወትነት ሥራዋን ትሠራለች" ይላሉ።[3]

(1.1.2) የነፍስን የእድገትና ከትውልድ ወደ ትውልድ የመራባት ሁኔታ አቡነ መልከ ጼዴቅ በምሳሌ ሲያብራሩ፦ "ዛፍ ፍሬውን ወስደው ቢተክሉት ... ያንኑ የመጀመሪያውን ዛፍ መስሎ እንዲገኝ ነፍስና ሥጋም በአንድ ጊዜ ከአባትም ከእናትም በሔደው ዘር አብረው ይሔዳሉ፤ ከዚያ በኋላ ያንኑ የመጀመሪያውን ሰው [አዳምን?] መስሎ ሥጋው ተቀርጾ አካል ለይቶ ሰው ሆኖ ሲገኝ ነፍሱም አብራ ታድጋለች ማለት ዕውቀቱ ይዳብራል፤ አእምሮው ይሰፋል። ጥንታዊ በደልን ከአባቱና ከእናቱ በዘር ይወርሳል የሚባለው ስለዚህ ነው፤ ... የኃጢአትም ቁራኝነት ከነፍሱ ጋር አብሮ ስለሚወርድ..' ይሉናል።[4] አባ መልከ ጼዴቅ "ነፍስ አስቀድማ በመዝገበ ነፍሳት ነበረች፤"[5] የሚለውን አመለካከት ሁሉም ፍጡር በዘመን ጥላ ሥር ጊዜ ተሰፍሮና ተቈጥሮለት ስለ ተፈጠረ "አስቀድሞ ተፈጠረ" የሚባል ፍጥረት የለም ሲሉ ይሞግቱታል።[6] "ሰው በተወለደ (በተፀነሰ) ቁጥር አዲስ ነፍስ ይፈጠርለታል፤" የሚለው አመለካከትም "እግዚአብሔርን በየጊዜው የሚፈጥርና ፍጥረት በስድስት ቀናት ተጠቃሎ እንዳላበቃ የሚያስመስል ነው፤" ሲሉ ይተቹታል - "ወፈጸመ እግዚአብሔር ግብሮ ዘገብረ" የምትለዋን የዘፍ.2፡2 ጥቅስ እያጣቀሱ! መልአከ ብርሃን በበኩላቸው ይህ ብሒል በቅዱሳት መጻሕፍት ማስረጃ የሌለው ነው ሲሉ ይነቅፉታል።[7]

(1.1.3) የመጻሕፍቱን ትርጓሜ - ከሁለቱ አበው አባባል ጋር የሚስማሙትን - እንመልከት። በኦሪት ዘፍጥረት 2፡7 "ወነፍሐ በገጹ መንፈሰ ሕይወት ወኮነ እጓለ እመሕያው በመንፈሰ ሕይወት - ሕይወት የምትሆን ነፍስን አሳደረበት፤ አንድም የጸጋ ሕይወት የሚሆን መንፈስ ቅዱስ አሳደረበት፤ አዳም ሕይወት በምትሆን ነፍስ ባለ አእምሮ ሆነ፤" በሚል አዳም ሕይወት (ነፍስ) ያገኘበት መንገድ በሊቃውንት ተብራርቶ ተገልጿል። ይህን ቃል እንደምታው ገፋ አድርጎ በሐተታ ሲያብራራው "ነፍሐ በገጹ [እፍ ብሎ ነፍስን በንፍሐት /በእፍታ/ አሳደረበት] ማለቱ፦ አሁን ዛሬ ሰው ትተራውን በፊት ሠርቶ በኋላ እህል እንዲያኖርበት፤ በፊት ሥጋን ፈጥሮ ኋላ ነፍስን አምጥቶ አሳደረበት ማለት አይደለም፤ ሥጋን ከዐራቱ ባሕርያት፣ ነፍስንም እምኀበ አልቦ [ከምንም /ካለመኖር/ - out of nothing] አምጥቶ ሲፈጥር ሲያዋሕድ አንድ ጊዜ ነው፤ የነፍስና የሥጋ ተዋሕዶ በተፀቅቦ [የየራሳቸውን ተፈጥሮአዊ ባሕርይ ሳይለቁ፤ አንዱ በአንዱ ሳይዋጥ መዋሐድ] ነውና ነፍሐ በገጹ [ነፍስን በንፍሐት አሳደረበት] አለ እንጂ፤" ይላል።[8] ትርጓሜው በግልጽ እንዳስቀመጠው ሥጋ ከዐራቱ ባሕርያት ተነሥቶ፤ ነፍስ እምኀበ አልቦ መጥታ የተዋሐዱበት ቅጽበት አንድ ጊዜ ነው። በንግግር የሥጋና ነፍስ ተፈጥሮ መቀዳደም ያለበት መምሰሉ መገኛቸውን ለመናገር በተደረገ ሒደት የተከሰተ ነው፤ እንጂ የአዳም ሥጋና ነፍስ ተፈጥሮና ውኀደት አንድ ጊዜ ነው።[9]

(1.1.4) ስለ ሔዋን ተፈጥሮ ሲነገር ከአዳም ጎን መገኘቷን ከመግለጽ ውጭ ለእርሷ ተብሎ አዲስ ነፍስ ስለ መፍጠሩ ወይም ከነፍሳት መዝገብ የተፈለቀቀች ነፍስ ከአዳም በተከፈለው የሔዋን ሥጋ ላይ ስለ ማደሯ በዘፍ.2፡22 አለመጻፉም "ነፍስም እንደ ሥጋ ከተገኘችበት አካል እየተከፈለች ስለምትሔድ የሔዋን ነፍስ ከአዳም ከነሳችው ሥጋ ጋር አብራ እንደ ተከፈለች ታሳቢ ተደርጎ ነው፤' በማለት የአባ መልከ ጼዴቅንና የመልአከ ብርሃንን መከራከሪያ አጠናክሮ መያዝ ይቻላል። ከአዳም በቀር እግዚአብሔር እፍ ብሎ ነፍሱን ከሥጋው ያዋሐደው ሰው ስለ መኖሩ በመጽሐፍ ቅዱስ ስላልሰፈረ "ነፍሳት ሁሉ ከአዳም ዘር ተከፍለዋል" ብንል እውነት አለን። ስላሚገርስ ነፍስን ከሥጋ ሳይለይና ሳያቀዳድም "ብዙ፤ ተባዙ" ነው ያለው። አለቃ... ሥጋው ስለ አዳም ተፈጥሮ ሲገልጹ፦ "አዳም በአካለ ነፍሱና በአካለ ሥጋው መቀዳደም መከታተል አለበትን? ቢሉ የለበትም። በአካለ ሥጋውና በአካለ ነፍሱስ መቀዳደም መከታተል ቢኖርበት ንግበር፡ ሥጋ፡ [ሥጋን እንፍጠር]

[3] መልአከ ብርሃን አድማሱ ጀንበሬ፤ መድሎተ አሚን፡ ገ.358
[4] አባ መልከጼዴቅ፡ገ.135
[5] በእኛ ድርሳናት ውስጥም አልፎ አልፎ ይህ አስተምህሮ ብልጭ ይላል። ለምሳሌ፦ በድርሳነ ዑራኤል ገጽ 119፦ "ነፍስ ዕፀብት እንዘ ኢተጋድር ውስተ ሥጋ ነበረት ውስተ ሕይወት - ነፍስ በሥጋ ከመዋሐዷ በፊት አስደናቂ በሚሆን ሕይወት ውስጥ ነበረች።" ይላል።
[6] ይህ አስተምህሮ በአገራችን ተነስቶ በአፄ ገላውዴዎስ ዘመን ተወግዟል። (ሐለቃ ተክለ ኢየሱስ፤ የኢትዮጵያ ታሪክ፤ 2ኛዕትም፤ 2008 ዓ.ም.፡ገ.145።)
[7] አድማሱ ጀንበሬ፤ መድሎተ አሚን፡ገ.360-361

[8] የመጻሕፍተ ብሉያት ክልኤቱ አንድምታ፤ 1999 ዓ.ም.፡ 122
[9] ዝኒ ከማሁ፡ገ.22

ወንግበር፡ ነፍስ፡ [ነፍስንም እንፍጠር] ባሉ ነበር፤" በማለት የሥጋና ነፍስ አፈጣጠር አንድ ላይ በተመሳሳይ ቅጽበት የተከናወነ እንደ ሆነ ይተርካል።[10] ሔዋንም እንዲሁ ከአዳም ሥጋ፣ አጥንት እና ነፍስ ተከፍሎ ስለ መፈጠሯ ይገልጻል።[11] አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ በጌና ስብከት ምንባብ ቍጥር 24 "ለአዲስ ጽንስ ሁሉ አዲስ ነፍስ ይፈጠራል" የሚለውን ካቶሊካዊ ብሒል ሲነቅፍ "ዳግመኛም በአዳም ላይ እንደሆነው በሕጻናት አካል ውስጥ ከእግዚአብሔር እስትንፋስ እፍታ የሕይወት እስትንፋስን መቀበል እንደሚደረግ የሚናገሩ አሉ። እኛ ግን የነፍስና ሥጋ መውጣት ከወንድ [ወገብ] በመዋለጃ ዘር ወጥቶ በሴቲቱ ማኅፀን ይፀነሳል፤ ከእርሷም በእግዚአብሔር ትእዛዝ የሚሆን የወንድና የሴት ፈቃድ የጠባይ መቀላቀል ይሆናል፤ ወንድም ቢሆን ሴትም ቢሆን ይሳላል [ሕዋሳት /የሰውነት አካላት/ ያወጣል] እንላለን። /ዘፍ.2፡7/ ይላል።

(1.1.5) አባ ጊዮርጊስ የፋሲካ ረቡዕን ምንባብ ሙሉ ለሙሉ በሚባል መልኩ ስለ ነፍስ አፈጣጠር ለመተረክ ነው ያዋለው። ምንባቡን "ለሕፃን ከአባቱና ከእናቱ ባሕርይ የሚሰጠውን የሕይወት እስትንፋስን መቀበልን የሚክዱትን በተገናኙም በአርባ ቀን እግዚአብሔር በሕፃኑ ፊት ላይ የሕይወትን እስትንፋስ እፍ ይልበታል፤ በእግዚአብሔርም እጅ ይፈጠራል የሚሉትን ሰዎች ተግሣጽ እንናገር..." ሲል ይጀምራል።[12] የነፍስን አፈጣጠር ሒደት ማብራራቱን ሲቀጥልም፥ "...የወንድ ባሕርይ [ዘር] ከእርሷ [ከሴቷ] የመዋለጃ ዘር ጋር ተቀላቅሎ በሴቲቱ ማኅፀን ውስጥ በሚፀነስ የዘር ጠብታ ከጭት ይፈስሳል፤ በእግዚአብሔርም ፈቃድ ሕፃን ይሆናል። [እንደ ሔዋን] በመሠራት አይደለም፤ [እንደ አዳም] በሕይወት እስትንፋስም እፍታ አይደለም።..." ይላል።[13] አባ ጊዮርጊስ ስለ ሰው ነፍስ አፈጣጠር ሦስት መንገዶች እንዳሉ ነው የሚነግረን። መንገዶቹ፡- (1) ንፍሐት፣ (2) መሠራትና (3) ተከፍሎ ሊባሉ ይችላሉ። የአዳም ነፍስ አፈጣጠር 'በንፍሐት' ነው። የሔዋን አፈጣጠር ያለእናት 'በመሠራት' ሆኖ ነፍሷና አጥንቷ ከአዳም ተገኝቷዋል። የቃየል ሥጋና ነፍስ ግን 'በተከፍሎ' ነው፤

[10] አክሲማሮስ፡ ገ.150
[11] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.181
[12] አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ፣ መጽሐፈ ምሥጢር፣ 2001 ዓ.ም.፡ ገ.237
[13] ዝኒ ከማሁ፡ገ.239



እንደ አዳም መፈጠር፣ እንደ ሔዋን መሠራት የለበትም። በአባ ጊዮርጊስ እንደበት፡- "...የሕይወት እስትንፋስን መቀበል በእናታችን በሔዋን ተቋርጧል፤ የአዳም [አንድ ጊዜ] የሕይወት እስትንፋስን መቀበል [ለሁሉም] በቅቷልና፤ በእጅ መሠራትን ግን ተሠራች ትወለድ ዘንድ እናት የለቻትምና። በቃየል ግን በእጅ መሠራትም የሕይወት እስትንፋስን ከእግዚአብሔር መቀበልም ተቋርጧል፤ የአባቱና የእናቱ የሕይወት እስትንፋስ በቅቶታልና፤" ተብሏል።[14] አባ ጊዮርጊስ ይህን መጽሐፍ ቅዱሳዊ ሐቅ ያልተቀበሉ ሰዎችን ይዘልፋቸዋል፤ ሆኖም በምሣሌ ላይ ከፉ ነገር ለማለትና አይፈግማቸውም።[15]

(1.1.6) በቤተ ክርስቲያን ያለውን ትውፊት፣ የአንድምታ ትርጓሜዎችና አዋልድ መጻሕፍትን ስናነብ የጌታ ከእመቤታችን ሰው መሆን የሚገለጽበት ቃል፣ "ከሥጋዋ ሥጋ፣ ከነፍሷ ነፍስ ነሣ፤" የሚል ነው። ለማስረጃ ከሃይማኖተ አበው ጥቂት ምንባባትን እንጥቀስ። ቅዱስ አትናቴዎስ፡- "ከእመቤታችን ... ከቅድስት ድንግል ማርያም ... ከሥጋዋ ሥጋን፣ ከነፍሷ ነፍስን ነስቶ ሰው እንደ ሆነ እናምናለን፤" ሲል ነፍስና ሥጋ ከወላጅ እንደሚከፈል ያመላክታል።[16] ቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሳርያም በተመሳሳይ ስለ ጌታ ሰው መሆን ሲተርክ፡- "ከእርሷ ሥጋን፣ ነፍስን ነስቶ ሰው እንደ ሆነ እናምናለን፤" በማለት በማኅፀን ውስጥ የፅንሱ አካል በአጸባፊተ መንፈስ ቅዱስ (በመንፈስ ቅዱስ ጣቶች) ሲቀረጽ በተመሳሳይ ቅጽበት ነፍስ አብሮ እንደ ተቀረጸች ያስረዳል።[17] ዮሐንስ አፈወርቅ እንዲሁ፡- "... ከድንግል የምትናገር የምታውቅ ነፍስ ያለችውን ሥጋ ነሣ ..." ይላል።[18] አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ "በእናቱም ላይ ካለው በቀር ሌላ የሕይወት እስትንፋስ አልተዋሐደም"[19] ብሏል። በውዳሴ ማርያም ትርጉም ውስጥ፡- "ተሰብአ፣ ተሠገወ፣ ኮነ ሰብአ፣ አማኑኤል፣ ኀደረ ላዕሌነ፤" የሚሉ ቃላት በተተረጎሙበት አጋጣሚ ሁሉ የጌታ ሥጋን ብቻ ሳይሆን ነፍስንም

[14] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.239
[15] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.244
[16] ሃይማኖተ አበው ዘአትናቴዎስ፡ ገ.76፣79፣85
[17] ሃይማኖተ አበው፡ ገ.421
[18] መጽሐፈ ቅዳሴ ዘዮሐንስ አፈወርቅ፡ ገ.240
[19] መጽሐፈ ምስጢር፡ገ.242

ከእመቤታችን መንሳት ተተርጊል።[20] በወንጌል ትርጓሜም ተመሳሳይ ነው። ለአብነት ትርጓሜ ወንጌል በዮሐንስ 1፥14 ላይ "ወውእቱ፡ ቃል፡ ሥጋ፡ ኮነ፤ ወንደረ፡ ላዕሌነ...ላዕሌነ /ውስቴትነ/ አለ ነፍስን እንደ ተዋሐደ ለማጠየቅ የሚለውን ገጸ ንባብ እንድምታ ማየት ይቻላል።[21] በሐዋርያት ሥራ ምዕ.17፥25 እንድምታ እንዲሁ "ወውእቱ፡ ይሁብ፡ ለኩሉ፡ ሰብእ፡ ነፍሰ፡ ወሕይወተ፡ ኵሎ፡ ገብረ፡ ኀቡረ" የሚለው ቃል "ለሰው ሁሉ ደመ ነፍስን፣ ነባቢት ነፍስን የፈጠረ፤ ሥጋና ነፍስን አዋሕዶ የፈጠረ፤" ተብሎ የነፍስና ሥጋ አፈጣጠር መቀዳደም የሌለበት በተዋሕዶ (ነፍስና ሥጋ አንድ ላይ) የተከናወነ የጌታ ሥራ መሆኑ ተመልክቷል። በየመጻሕፍቱ ጌታችን ሰው ሲሆን ነፍስና ሥጋን ከእመቤታችን ሰውነት መንሳቱ በግልጽ ሰፍሯል፤ 'አዲስ ነፍስ እምነበ እልቦ አምጥቶ ለራሱ ፈጠረ፤' ወይም 'ከመዝገበ ነፍሳት የድርሻውን ነፍስ ወሰደ፤' የሚል የለም።

(1.1.7) በአጠቃላይ የሁለቱ አበው ኦርቶዶክሳዊ አቋም፦ "ነፍስ ከሥጋ ጋር በፈጣሪ እፍታ አዳም ሲፈጠር ተፈጠረች፤ ከዚያ በኋላ ሰው በተፈጥሮአዊ መንገድ በተራክቦ እየበዛና እየተባዛ ሲሔድ ነፍሱም እንዲሁ ከአባት ዘር፤ ከእናት ደም ተከፍሎ ሥጋ (ፅንስ) ሲፈጠር አብራ ከወላጅ አብራክ እየተከፈለች ከሥጋ ጋር በተዋሕዶ ሆና ነገር ግን ነፍሳዊ ባሕሪዋን ሳትለቅ፤ በሥጋ ባሕርይ ሳትዋጥ (በተፀቅቦ) ትራባለች የሚል ነው፤" ብንል አሳባቸውን መጠቅለል የሚቻለን ይመስለኛል።

በተንዳኝ የፈረንጆቹን ተቀራራቢ ትረካዎች ከየድረ ገጹ (ዌብሳይቱ) ማየት የፈለገ፤ ስለ ነፍስና ሥጋ ተዋሕዶ "Ensoulment" የሚለውን ቃል ለድረ ገጽ የመረጃ ማሰሻዎች በማቀበል የሚመጡለትን፦

(1) Pre-existentialism (ነፍስ ሥጋ ሳይፈጠር በመዝገበ ነፍሳት ነበረች)፤

(2) Traducianism (ነፍስ ከሥጋ ጋር ከአባትና እናት ተከፍላ ወደ ልጅ ታልፋለች)፤

[20] ውዳሴ ማርያም፤ ንባቡና ትርጓሜው፤ 1990 ዓ.ም. ፡ ገ.19፤70፤72፤76፤100፤105፤...

[21] ወንጌል ቅዱስ፤ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.379



(3) Creatianism[22] (የእያንዳንዱ ሰው ሥጋው ሲፈጠር አዲስ ነፍስ ትፈጠርለታለች) የሚለውን ሃይማኖታዊ አተያይ ተመልክቶ ከእኛ ሊቃውንት አመለካከት ጋር ማነጻጸር ይችላል።

(1.1.8) የሌሎች አብያተ ክርስቲያናትን አቋም ስናይ ካቶሊኮች "Every spiritual soul is created immediately by God - it is not 'produced' by the parents.... እያንዳንዷ መንፈሳዊት ነፍስ ወዲያዉኑ (በጽንስ ጊዜ) በእግዚአብሔር ትፈጠራለች - ከአባትና እናት አትከፈልም፤" በማለት ያስተምራሉ።[23] የምሥራቅ ኦርቶዶክሳውያን ስለ ነፍስ አፈጣጠር ማዕከላዊ ሊባል የሚችል አቋም እንደ ሌላቸው በመግለጽ ነገር ግን ከካቶሊካውያኑ የተዛመደ አስተምህሮ ያንፀባርቃሉ።[24] አስተምህሮው ለእያንዳንዱ ሥጋ አዲስ ነፍስ ይፈጠራል (Creatianism) የሚባለው አስተምህሮ መሆኑ ነው። ከቀደምት ኦርቶዶክሳውያን አበው ጎርጎርዮስ ዘኑሲስ "In relation to the formation of the human body, when does the soul have its origin? Three options arise, namely a) after the formation of the body, b) before the formation of the body, and c) together with the formation of the body. Option A is dismissed immediately since soulless bodies neither move nor grow. Option B is rejected due to the apparent absurdities and impieties which arise, namely those which arise from the concept of transmigration of souls. This leaves option C which is finally accepted - ከግዜፈ ሥጋ አፈጣጠር ጋር በተገናኘ የነፍስ ሕላዌ መቼ ይጀመራል? (ለሚለው) ጥያቄ ሦስት አማራጮች ይነሣሉ። እነርሱም፦ (ሀ) ቅድመ ተፈጥሮ ሥጋ፤ (ለ) ድኅረ ተፈጥሮ ሥጋና (ሐ) ጊዜ ተፈጥሮ ሥጋ ማለትም የሥጋ ሕላዌ ሲጀመር፤ አንድ ላይ። አማራጭ 'ሀ' እንበለ ነፍስ የሆነ ሥጋ መንቀሳቀስና ማደግ አይችልምና ውድቅ ተደርጓል። አማራጭ 'ለ'

[22] Creatianism እና Creationism ልዩነት አላቸው

[23] catholic encyclopedia/ http://www.vatican.va/archive/ENG0015/__P1B.HTM#-CR ወይም በዚህ http://www.vatican.va/archive/ccc_css/archive/catechism/p1s2c1p6.htm አድራሻቸው ቀኖና ቁጥር 366'ን ማየት ይቻላል።

[24] http://orthodoxwayoflife.blogspot.com/2009/07/nature-of-soul-mind-brain-and-heart.html : October 27, 2016

ነፍስ ተላላፊ (እንዱ ሲሞት ከሟች ግዘፈ ሥጋ ወጥታ በአዲስ ጽንስ እያደረች፣ ከሰው ወደ ሰው ወይም ከሌሎች ፍጥረታት ወደ ሰው በዳግም ሕላዌ ተላላፊ) ናት ማለትን ፈጥሮ ርኵሰትና ምስቅልቅል ስለሚፈጥር ተቀባይነት አላገኘም። ይህም አማራጭ 'ሐ' ተቀባይነት እንዲያገኝ አድርጎታል" እንደሚል ሥራውን ያጠኑ ምሁራን ይገልጻሉ።[25] የግብጽ ኦፕቲክ ቤተ ክርስቲያን በበኩሏ "The soul comes into existence as soon as the sperm and the egg unite - የወንዱ ዘርና የሴቷ እንቁላል እንደ ተገናኙ የነፍስ ሕላዌ ይጀምራል" የምትል መሆኗን እንባበናል።[26] የማብጻውያኑ ብሒል ከእኛ ጋር የሚገጥም ይመስላል። ከመልአከ ብርሃን ምሳሌ ተውሰን (ጥቂት በማሻሻል) ክብሪትን ምሳሌ እናድርጋት፡- የወንዱ ዘር የክብሪት ዕንጨት ነው፤ ሴቷ የክብሪቱ ማጎደር። የክብሪቷ ዕንጨት የማጎደሩን ቀፎ ከጎኑ ሲጭረው እሳት ይፈጠራል። ነፍስም እንዲያ ናት . እንደ እሳቱ። ክብሪቱ በሰበታ ሲጫር ብቻ እሳት ይኖራል፤ ነፍስም ሕላዌዋ ከወንድና ሴት ተራክቦ ነው። እኛ እንዲያ እናምናለን። የፕሮቴስታንታውያን አቋም የተለያየ በመሆኑና በጉዳዩ ላይ እምብዛም አትኩሮት የመስጠት ዝንባሌ ስለሌለ ይህ ነው ለማለት ይከብዳል። ይልቅስ የተለየ አቋም ወደሚያራምዱት የራሳችን ሊቅ እንለፍ፡-

## 1.2. "ነፍስ ከአባትና እናት በተከፈለው ዘር እምኀበ አልቦ መጥታ ታድራለች እንጂ እርሷ አትከፈልም!"

(1.2.1) አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ በመጽሐፈ ሰዋስው ወግስ ስለ ነፍስ ተፈጥሮ ሲገልጹ፡- "... ነፍስም እንደ አዳም ነፍስ ከፈጣሪ እፍታ በንጽሐ ጠባይዕ ተገኝታ ከአባት ከእናት በተከፈለው በዘርና በደም ታድራለች እንጂ እርሷ አትከፈልም ... ስትፈጠር እንደ መላእክት ነጻነትና ዕውቀት ሥልጣን ያላት፣ የወደደችውን ማድረግ የምትችል፣ ነባቢት፣ ለባዊት፣ ፍጽምተ አካል ናት እንጂ፤ ከሥጋ ጋር እንደ ሥጋ ከአባት ከእናት ስላልተከፈለች በየጥቂቱ

[25] *Saint Gregory of Nyssa On the Soul and the Resurrection*, Presented by: Brian Ephrem Fitzgerald, Ph.D. At St. Philip's Antiochian Orthodox Church, Souderton, PA 2, 9, 16, & 23 May 2004, p:12

[26] http://www.suscopts.org/q&a/index.php?qid=1233&catid=348



ማደግ የለባትም። ... ግዙፉ መሣሪያዋ ሥጋዋ እስኪያድግና እስኪፀና ድረስ በራሷ በገንዘቧ መሥራት ትችላለች፤ በር(ቅ)ቀቷ የምትሠራውን ግን ከፈጣሪ በቀር የሚያውቅላትና የሚያውቅባት የለም፤" ይላሉ።[27]

(1.2.2) አለቃ በማስረጃነት የቅዱሳት መጻሕፍትን ጥቅሶች፣ መቅድመ ወንጌል ፣ አዋልድና ማሳያ ቅዱሳንን በተዋረድ ይጠቅሳሉ። ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ፡- "ሰማያትን የፈጠረ፣ የዘረጋቸውም፤ ምድርንና በውስጡዋ ያለውን ያፀና፣ በእርስዋ ላይ ለሚኖሩ ሕዝብ እስትንፋስን፣ ለሚሄዱባትም መንፈስን የሚሰጥ ... " በሚለው የኢሳይያስ 42:5 ንባብ ውስጥ "ለሚሔዱባትም መንፈስን የሚሰጥ - ወነፍሰ፡ ለእለ፡ ይነብሩ፡ ዲቤሃ" የሚለውን ንባብ "ነፍስ ቀጥታ ከፈጣሪ የምትሰጥ እንጂ ከአባትና እናት የማትከፈል" ለመሆኗ ማሳያ አድርገው ያቀርቡታል። በተመሳሳይ ኤር.1:5፣ ዘካ.12:1 እና መዝ.21:10 ስለ ነፍስ ራሷን ችላ መናገር፣ ማምለክና ማወቅ መቻል ለአባባላቸው በማስረጃነት ቀርበዋል። ሆኖም የጥቅሶቹ አንድምታ ተርጓሚዎች ምንባባቱን የፈጣሪን አስቀድሞ ዐዋቂነት፣ የሰውን አእምሮ (ማገናዘብ) ለመግለጽ፣ የነፍስና ሥጋ ውሕደትን እና የጌታን ከማኅፀን ጀምሮ ጠባቂነት ለማሳየት የተጻፉ አድርገው ነው የሚተረጉሙዋቸው። ለምሳሌ፡- "ለሚሔዱባትም መንፈስን የሚሰጥ - ወነፍሰ፡ ለእለ፡ ይነብሩ፡ ዲቤሃ..." የሚለው የኢሳይያስ ንባብ ሲተረጎም "ከእርሷ ለሚኖሩ ሰዎች ነባቢት ነፍስን የሚያዋሕድ..." ተብሎ ነው።[28] "ነፍስን የሚሰጥ"[29] የሚለው ቃል ምሥጢራዊ ትርጉም "ነፍስን የሚያዋሕድ" ተብሎ ተቃንቷል።

(1.2.3) የዘካርያስ 12:1 "የሰውን መንፈስ የሠራ - ወይፈጥር፡ ነፍሰ፡ ላዕለ ሰብእ" የሚል ንባብም በአንድምታው "አእምሮን (ዕውቀትን) በሰው

[27] አለቃ ኪዳነ ወልድ፣ መጽሐፈ ሰዋስው ወግስ፣ 1948 ዓ.ም ፡ ገ.26

[28] መጽሐፈ ኢሳይያስ ፣ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997 ዓ.ም.፡ ገ.279

[29] "የሚሰጥ" ማለትም፡- አእምሮን የሚሰጥ፣ አካልን የሚሰጥ ... እንደ ማለት እንጂ የተለየች ስንዱ (ቀድማ ለብቻዋ የተዘጋጀች) ነፍስን፣ ከተለየ ቦታዋ አምጥቶ የሚሰጥ ማለት ሊሆን አይችልም። ጌታ ሀብተ ክህነትን አንድ ጊዜ ለሐዋርያት እፍ ብሎ ሰጥቷቸው እነሱ በተራቸው ለሊቃውንት፣ ሊቃውንት መልሰው በየዘመኑ ለተነሱ ተተኪዎቻቸው እስከኛ ድረስ አንድ ጊዜ ከጌታ የተሰጠውን ሀብት በንፍሐት የሚያስተላልፉበትን ሥርዓት የመሰለ ነው የነፍስ ከወላጅ ወደ ልጅ ከሥጋ ጋር በጽንስ ጊዜ እየተከፈለች መሄድ። (መጽሐፈ ምስጢር፡ገ.242።)

የሚያሳድር" ተብሎ ነው የተተረጎመው።[30] መዝ.21፡10 እንዲሁ "ከማኅፀን ጀምሮ በአንተ ተጣልሁ" የሚለው ቃል "በአንተ ፈቃድ ሰው ሆንሁ፤ ተገኘሁ/ ተጣልኩ' ማለቱ ከአባት ዘር፣ ከእናት ደም ይከፈላልና ከማኅፀን በቀር እየንዳንዱ ሰው ሲፈጠር ነፍሱ ከሥጋው በፊት ስለ መኖሯ ወይም ልክ እንደ መጀመሪያዋ የአዳም ነፍስ ወዲያውኑ በእፍታ ስለ መፈጠሯ አይገልጽም።[31] በአጠቃላይ ጥቅሶቹ አለቃ እንደሚሉት የነፍስን ከወላጆች አለመከፈል አያሳዩም፤ የነፍስን ባሕርይ መገለጫዎችና የፈጣሪን አምላካዊ ጥበቃ ብቻ ያሳያሉ እንጂ።

(1.2.4) በዚህ አጋጣሚ "ነፍስ" እና "መንፈስ" የሚሉት ቃላት በአነጋገር የተለያዩ መስለው ቢቀርቡም ያላቸው ትርጉም አንድ መሆኑን መረዳት ይገባል።[32] ግብጻውያን[33] ግን ነፍስና መንፈስ የተለያዩ እንደ ሆኑ ይናገራሉ[34]፤ የእኛ ሊቃውንት በተቃራኒው አንድነታቸውን ያስምሩበታል። ጥቂት ማስረጃ እናምጣ! የዮሐንስ አፈወርቅን ድርሳን በአንድምታ ሲተረጉሙት "እስመ ይዕቲ ነፍስ … ወካዕበ ትሠመይ መንፈስ በብዙኅ መካን - ነፍስ ትባላለችና … ዳግመኛም … በብዙ አንቀጽ መንፈስ ትባላለች፤" ሲሉ የግእዙን መዝ.50፡10 እና 77፡39 ጠቅሰው የነፍስና የመንፈስ ምሥጢራዊ አንድነትን ያብራራሉ።[35] ቅዱስ ያሬድ በስቅለት ጾመ ድጓ ማቴዎስ 27፡50 ላይ ተመሥርቶ "ጊዜ ተሰዓቱ ሰዓት ገዐረ ኢየሱስ በቃሉ ወወጽአት 'መንፈሱ' ሶቤሃ" ማለቱ ነፍሱን ተወ ለማለት ነው። የኪዳን ወልድ ክፍሌ መዝገበ ቃላት እንዲሁ የነፍስንና የመንፈስን መመሳሰል

---

[30] ዳንኤልና 12ቱ ደቂቅ ነቢያት፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1999 ዓ.ም.፡ገ.399

[31] መዝሙረ ዳዊት፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997 ዓ.ም.፡ ገ.136

[32] እርግጥ በመጽሐፍ ልማድ የአንዱን ለአንዱ ሰጥቶ መናገር፣ በግእዙ "መንፈስ" ያለውን በአማርኛው "ነፍስ" ማለት፣ የአማርኛውን "ነፍስ" በግእዙ "መንፈስ" ማለት፣ አንዳንድ ጊዜም ነፍስ፣ መንፈስ፣ ሥጋ ብሎ ለያይቶ መጥራት፣ ከዚያም አልፎ በነፍስ ባሕርይ ስለ ሥጋ፣ በሥጋ ባሕርይ ስለ ነፍስ መናገር፣ ደመ ነፍስን (እስትንፋስ ሕይወትን)ና ሕያዊት ነፍስን ቀላቅሎ መናገር የተለመደ ነው። "እስመ ክልኤቱ ነፍሳት ሀለዋ ውስተ ሰብእ [1] ወአሐቲ መንፈስ ሕይወት .. ወኢትመውትሂ። [2] ወአሐቲ ደመ ነፍስ … ወይእቲሰ ትመውት" እንዲል አባ ጊዮርጊስ በአርጋኖን ዘቀዳሚት። ደመ ነፍስ ደግሞ ከመላእክት በቀር ሁሉም ፍጥረት አለው ተብሎ ይታመናል። አክሲማሮስ፡ገ.149

[33] ብዙ ጊዜ በልማድ "ግብጻውያን፣ ፈረንጆች፣ ምዕራብውያን፣ ካቶሊካውያን፣ ፕሮቴስታንታውያን" እያልኩ ለሳቤን በጥቅል ስገልጽ በፀናው / ባመዘነው/ መናገሬ እንጂ ሁሉም እኔ እንደምለው ያለ ተመሳሳይ አቋም አላቸው ማለቴ አይደለም።

[34] H.H.Pope Shenouda III, "What is Man?", 2nd print, June, 2004, Egyptian Printing, ወይም http://www.suscopts.org/q&a/index.php?qid=578&catid=348

[35] ድርሳን ዘዮሐንስ አፈወርቅ፣ 1987 ዓ.ም. ምዕራፍ 2፡199-201፣ ገ.57፣



ይናገራል።[36] የመጽሐፈ ቅዳሴ ትርጓሜ በ"እመ ብእሲ" ትርጓሜ "ንሥእ ሥጋ ወመንፈስ" የሚለውን ቃል "ነፍስና ሥጋ ፈጥሮ የሚገዛ ሲል በትርጓሜው መንፈስን እንደ ነፍስ ቈጥሮ አብራርቶታል።[37] በዘመኑ መልክ ጸደት መጽሐፍና በመጽሐፍ ቅዱስ መዝገበ ቃላት በተመሳሳይ ገጽ 137 ነፍስና መንፈስ በመጽሐፍ ልማድ ለየብቻ ቢጠቀሱም ምሥጢራዊ ትርጉማቸው አንድ መሆኑ' ተገልጿል።

(1.2.5) ወደ ነፍስ አፈጣጠር ትረካችን እንመለስ! አለቃ ኪዳን ወልድ "ሕጻን ከአባቱ ወገብ አውጥተህ ወደ ሴት ማኅፀን የምትልከው ሆይ! በረቂቅ የምታረገው፣ የሕይወት መንፈስንም እፍ ትልበታለህ። በሆነ ሆኖ በአርባ ቀን ትሸመዋለህ (ታድለዋለህ) ባለጸጋ ለመሆን ለመደኸየትም ቢሆን ለመጽደቅም ለመኰነንም ቢሆን …" የሚለውን የአትናቴዎስ ቅዳሴ ቍጥር 113 ጠቅሰው "ነፍስ ከአባትና እናት በተከፈለው ዘር ታድራለች እንጂ እርሷ አትከፈልም፤" የሚለውን ጽኑ አቋማቸውን ያጠናክራሉ።[38] ነገር ግን ይህን ንባብ አበው የሚተረጕሙት ለነፍስ አፈጣጠር ሳይሆን "እስከ አርባ ቀን ፅንሱ ውኃ ሆኖ ይሰነብታል። አይታወቅም። በአርባ ቀን እንደ ጭራ ሆኖ ይታያል። ጥር የሚከብርበት፣ ቢታከይ [ቢታበይ] የሚቸገርበት፣ በጎ ቢሠራ የሚጸድቅበት፣ ክፉ ቢሠራ የሚኰነንበት ሕዋሳት በአርባ ቀን ይፈጸማልና እንዲህ አለ፤" በማለት ንባቡ ተሥዕሎተ መልክዕ የሚያገኝበትና ሕዋሳት የሚሟሉበትን ቀንና ሁኔታ ለማመልከት እንደ ሆነ በማተኮር ነው።[39] ተመሳሳይ አባባ በዘጸአት የምዕራፍ 21፡22 ትርጓሜም ስለ ተሥዕሎተ መልክዕ ቀርቧል።[40]

(1.2.6) ተዛማጅ መጣጥፍ ያዘጋጁ ወንድሞቻችን ንባቡ እንዳለ በደረቁ ከተወሰደ ከነፍስ አፈጣጠር በተጨማሪ የሰው የጽድቅና ኵነኔ ዕጣ ፈንታ አስቀድሞ በአርባ ቀን ዕድል የተወሰነ (predestination) ስለሚያስመስል ንባቡ ትርጓሜውን ማገናዘብ እንዳለበት አመላክተዋል።[41] በተጨማሪም

---

[36] ኪዳን ወልድ ክፍሌ.፡ገ.647

[37] መጽሐ ቅዳሴ፣ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.42

[38] አለቃ ኪዳን ወልድ፡ ገ.25

[39] መጽሐፈ ቅዳሴ፣ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.327

[40] መጻሕፍ ብሉያት ክልኤቱ፡ ገ.131

[41] ዲ/ን ብርሃኑ አድማስ፣ ጥር፣ 2001፣ ሐመር መጽሔት፣ ገ.27-28

የጽንሱ ሕዋሳት ረግተው ቅርጽ የሚይዙት ከአርባ ቀን ወይም ከስድስተኛው ሳምንት ጀምሮ መሆኑ በሳይንሱም እንደሚታመንበት ዲ/ን ብርሃኑ የገለጹ ሲሆን በአይሁዳውያን እምነት ደግሞ አርባኛው ቀን ነፍስ ከጽንሱ የምትዋሐደበት ተደርጎ እንደሚቈጠር ከጽንስ ማቋረጥ ጋር የየሃይማኖቶቹን አስተምህሮ የዳሰሱት የሕግ ምሁሩ ፀሐይ ወዳ ጽፈዋል::[42] በእኛ እንዲያ አይደለም:: አርባ ቀን የአዳም ነፍስ ማግኘት ሳይሆን ወደ ገነት መግባት ነው የሚተረከበት! ይህም ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ለማግኘቱ ማሳያ ነው (ኩፋ.4:9፤ ዘሌ.12:4-7፤ ሉቃ.2:22-25)::[43] ነፍሱ'ማ ከጅምሩ ከሥጋው ጋር ተዋሕዳ ነው የተፈጠረችው!

(1.2.7) በመቅድመ ትርጓሜ ወንጌል ገጽ 15 ስለ ነፍስ ባሕርይና አፈጣጠር "፺ ይእቲ አርአያ ገጹ ለእግዚአብሔር ወአምሳሊሁ - ይህቺውም የእግዚአብሔር መታወቂያ ናት፤ ምሳሌውም ናት:: … ግብር እምግብር ያልተፈጠረች ናት:: … ሀላዊት… ነባሪት ናት:: የሚገዛት፣ የሚያዝዛት ሳይኖር የወደደችውን እንደ ወደደች ታደርግ ዘንድ አእምሮ ጠባይዕን ሳለባት፤ በጎነቷም ክፋቷም በፈቃዷ ይሆን ዘንድ" ይላል:: ይህን ንባብ አለቃ ኪዳነ ወልድ፦ "ነፍስ ፍጹም ሆና ከፈጣሪዋ እፍታ ስለ ተገኘች በየጊዜው ማደግ የለባትም፤" ለማለት ጠቅሰውታል:: ይሁን እንጂ የነፍሳት ባሕርያት ተብለው ከተጠቀሱት ነባቢነት (ቃል)፣ ለባዊነት (ልብ) እና ሕያውነት ውስጥ የአእምሮ ሥራ የሆኑት ነባቢነትና ለባዊነት (የንግግርና የማገናዘብ ችሎታ) ከግዘፈ ሥጋ ጋራ አብረው እያደጉና እየጎለመሱ ሲሔዱ ስለምናይ ከአለቃ ይልቅ "ሥጋው ተቀርጾ አካል ለይቶ ሰው ሆኖ ሲገኝ ነፍሱም አብራ ታድጋለች ማለት ዕውቀቱ ይዳብራል፤ አእምሮው ይሰፋል፤" የሚለው የአባ መልከ ጼዴቅ አተያይ የተሻለ አሳማኝ የሚሆን ይመስለኛል:: የአቡነ ጎርጎርዮስ አቋምም፦ "እያንዳንዱ ሰው በሚወለድበት ጊዜ እያደገ በሔደ ቍጥር ነፍስም አብራ ታድጋለች" የሚል ነው::[44] ስለ ሆነም የመቅድመ ወንጌሉ አሳብ ስለ መጀመሪያው ሰው ስለ አዳም ነፍስ አፈጣጠር እንጂ አለቃ እንዳሉት ስለ እያንዳንዳችን ነፍስ አፈጣጠር የሚናገር አይደለም:: ነፍስ "ግብርት እምግብር"

---

[42] Tsehai Wada,2008,Mizan Law Review,p.8

[43] አስሊማርስ፡ ገ.157

[44] አባ ጎርጎርዮስ፣ የቤተክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ፣ 1978 ዓ.ም.፡ ገ.54



አይደለችም መባሏ ለሁላችን ሳይሆን ከአዳም ሥጋ ተፈጥሮ አንጻር ብቻ ነው:: ምክንያቱም የአዳም ሥጋና ነፍስ የተፈጠሩት በአንድ ጊዜ፣ በተዋሕዶ ቢሆንም መገኛቸው ለየቅል ነው:: የአዳም ሥጋ እምንበ አልቦ አይደለም የተፈጠረው፤ ግብር እምግብር ነው - ከመሬት፣ ውኃ፣ ነፋስ፣ እሳት:: በአንጻሩ የአዳም ነፍስ እምንበ አልቦ ናት፤ ከእርሱ በኋላ ያለነው ሰብአውያን ፍጡራን ነፍስ ግን ከወላጅ የምትከፈል (ግብርት እምግብር) ናት:: ነፍስ የእግዚአብሔር እፍታ ናት'[45] የሚለውንም አቡነ መልከ ጼዴቅ "እግዚአብሔር ጥበበኛ ፈጣሪ እንደ መሆኑ ነፍስን ፈጥሮ በሰው ሥጋ ውስጥ አደረጋት እንጂ ከአምላክነቱ ጋር ምንም ግንኙነት (የእግዚአብሔር አካልነት) የሌላት ፍጥረት ናት፤" በማለት ነፍስን የመለኮት አካል አድርገን እንዳንወስዳት ያስጠነቅቁናል::[46]

(1.2.8) አቡነ ጎርጎርዮስ "የሰው ነፍስ እንደ እሳት ከፋይ ከመለኮት ባሕርይ እየተከፈለች የምትመጣ ናት፤" የሚለው አነጋገር ግኖስቲካዊ ኑፋቄ እንደ ሆነ ይጠቁሙናል::[47] አንድ የሐዲስ ኪዳን ሊቅ በዚህ ርእስ ዙሪያ ጠይቄ በቀዳሚ ሠለስቱ ምዕት ቍጥር 63 "ወእምእሐቲ መዝገብ ዘእምስትንፋስ እሙሁ ይሰርጸ ወያሕመለምላ ነፍሳት እለ ይትወለዱ ውስተ ዓለም … በዓለም የሚወለዱ ነፍሳት ከአፉ እስትንፋስ ከተገኘች ከአንዲት መዝገብ ይወጣሉ፤ ይለመልማሉም፤" እንደሚል በመጥቀስ ነፍስ የፈጣሪ እስትንፋስ ክፋይ ናት ብለውኝ ነበር:: የቅዳሴው አንድምታ ትርጓሜ ግን ይህን ንባብ "አንድ ከአዳም 'ብዝሁ ወተባዝኁ' ባለው በባሕርዩ ሥልጣን በዚህ ዓለም የሚፈጠሩ ነፍሳት ይከፈላሉ፤" በማለት ነፍሳት በሰው የመዋለድ ሒደት በተከፍሎ የሚበዙና የሚባዙ መሆናቸውን በማረጋገጥ የሊቁን አባባል ውድቅ አድርጎ

---

[45] ጥቅሱ ለትምህርት ሃይማኖት የሚበቃ ባይሆንም በተለምዶ ፈላስፋው ዘርዓ ያዕቆብ የምንለው ሰው ደቀ መዝሙር የሚሆን ወልደ ወልደ ሕይወት እንዲፈንዊ 'ወልደናዊ ለነፍስን ማዕዘረ ብርሃን ውእቱ ዘወጽአ እምገላዌ እግዚአብሔር ፈጣሬ … ወበመ ወጽአት ብርሀተ እምሕጽን ፈጣሪሃ ከማሁ ትገብእ ኀቤሁ እምድኅረ ዝንቱ ኀዘረት - የነፍስ ልብናዊ … ብፁህ ናት (ማስተዋል) ከ… እግዚአብሔር አነዋወር የወጣ የብርሃን ፍንጣቂ ነው … ከፈጣሪዋ አትቅፍ እንደ ወጣች ከዚህኛው (ዓለም) ኑሮረት (ኑሮ) በኋላ እንዲሁ ወደ እሱ ትመለሳለች::" ይላል:: (ሐተታ ገብረ ሕይወት (በግእዝ):ገ.33::)

[46] አባ መልከ ጼዴቅ:ገ.140

[47] አባ ጎርጎርዮስ፡ ገ.57

አቃንቶ ተርጉሞታል።[48] ለተፀነሰው ጽንስ ሁሉ ከእናትና አባቱ የምትከፈል "ግብር እምግብር" የሆነች ነፍስ እንጂ "እምነበ አልቦ" አዲስ ነፍስ አትፈጠርም። ሕያዊት ነፍስ እንደ ጧፍ ብርሃን በወንድና ሴት ተራክቦ እየተለኰሰች ከወላጅ ሳትጎድል በተከፍሎ ለልጅ ታልፋለች፤ ትበዛለች።

(1.2.9) ወደ አለቃ ኪዳን ወልድ ስንመለስ እርሳቸው ስለ ነፍስ ከላይ የሰፈረውን ሐተታ የሚያቀርቡት "ነፍስ ከወላጅ ወደ ልጅ ስለማትተላለፍ እመቤታችንና ጌታ ብቻ ሳይሆኑ አዳምን መስለው በፈጣሪያቸው ላይ በደል ያልሠሩ ሁሉ ጥንተ አብሶ አይመለከታቸውም፤" ለማለት ነው። የአለቃ አቋም ጥንተ አብሶን በሚተነትኑ የባሕር ማዶ ሊቃውንት "Imitation" ይባላል፤ ይዘቱ የአዳም ርግማን መስሎ ለሚሠራ እንጂ በተወላጁ ሁሉ (by propagation) አይተላለፍም የሚል ሲሆን ብሒሉ በምሥራቁም ሆነ በምዕራቡ ውጉዝ ነው። ለጊዜው ስለ ነፍስ አፈጣጠር ከሊቃውንት የሚቀርበውን የተለያየ አመለካከት ከገለጽን ይህን በዋናነት ትንቢተ ሕዝቅኤል ምዕራፍ 18:4 እና 20 ላይ የተመረኮዘ የአለቃ አባባል ወረድ ብለን እንመለስበት። ብቻ አንድ ጭብጥ እንያዝ፡፡ በአለቃ ኪዳን ወልድ "ነፍስ ከወላጅ ሳትከፈል እምነበ አልቦ ትፈጠራለች" የሚል አቋም ከተራመድን ጥንተ አብሶ የሚባል ነገር አይኖርም። ምክንያቱም ነፍስ ከወላጅ ስለማትከፈል የአዳም መርገም ለልጆቹ በነፍስ የመከፈል ሒደት አይወረስም፤ አይተላለፍም። ስለዚህ በአለቃ ኪዳን ወልድ አሳብ ከተመራን ርእሱ እዚሁ ይቆማል። እንደ እነ አቡነ መልከ ጼዴቅና መልአከ ብርሃን አድማሱ "ነፍስ ከወላጅ ወደ ልጅ በዘር የመከፈል ሒደት ትራባለች፤" ካልን ብቻ ነው ስለ ጥንተ አብሶ መነጋገር የምንችለው። በእኔ በኩል (በኦሪት ዘመን ሰው በመርገም ስር ሆኖ ይወለዳል እንጂ ኃጢአትን ወርሶ አይወለድም ብዬ ባምንም) ከነፍስ አፈጣጠር አንጻር የጊለኞችን ትንታኔ ስለ ተቀበልኩ ወደ ቀጣዩ ርእስ እሻገራለሁ። ቆይ…

(1.2.10) ጥንተ ነፍስን ከመቋጨቴ በፊት ስለ ነፍስ መገኛ ጥቂት ልበል። ነፍስ በሰው የሰውነት ሕዋሳት ውስጥ የት ቦታ እንደምትገኝ የተለያዩ አመለካከቶች አሉ። በሕግ ትምህርት ቤት ስንማር "አንድ ሰው በአንድ ጊዜ በተተከሉ ሁለት ጥይቶች ልቡ እና ጭንቅላቱ ቢመታ ቀድማ የገደለችው

[48] መጽሐፈ ቅዳሴ፤ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.292



ጥይት የትኛዋ ናት? ገዳዩስ ልቡን የመታው ሰው ወይስ ጭንቅላቱን? የሚል ክርክር እንደ ነበር አስታውሳለሁ። ልቡን የመታው ነው ቀድሞ የገደለው ካልን ነፍስ ያለችው ልብ ላይ ነው ማለት ነው፤ ቀድሞ የመታው ነው ካልን ጭንቅላት የነፍስ መኖሪያ ነው ማለት ነው። ጭንቅላቱን ከተጠያቂነት እንደማያመልጡ ብንስማማም ገዳዩን ጥይት ሳንለይ ክርክሩ በአንጥልጥል መቅረቱን አስታውሳለሁ። ወደ መጻሕፍቶቻችን ስንመለስ ዘሌ.17:14 "የሥጋ ሁሉ ሕይወት ደሙ ነውና የሥጋውን ሁሉ ደም አትብሉ፤ የሚበላውም ሁሉ ተለይቶ ይጥፋ አልኋቸው፤" በማለት ሕይወትንና ደምን ያቀራኝዋል። ኦሪት ዘፍጥረት ምዕራፍ 9:4 እንዲሁ "ነገር ግን ነፍሱ ደሙ ያለችበትን ሥጋ አትብሉ፤" ይላል። አባቶች ይህን ንባብ ሲያብራሩት "እስመ ደም ነፍስትክሙ ውእቱ። ደም ነፍሳችሁ ነውና።… የበሉት የጠጡት ደም ይሆናል፤ በዚያው ላይ ነፍስ ታድራለችና ነፍስከሙ አለ፤ 'እስመ ነፍስ ተኃድር በደም' እንዲል ዘሌ 17:14"[49] ቅዱስ አትናቴዎስ ነፍስን ከልብ ጋር ያያይዘዋል። "ወልቡ፡ ለብእሲ መንፈሱ ውእቱ ወውእቱ አሐዱ ምስለ ነፍሱ እንተ ሀለወት በሥጋሁ … የሰው ልቡ ሕይወቱ ነው፤ ይኸውም ሥጋውን ከተዋሐደች ከነፍሱ ጋር አንድ ነው"[50] አባ ጊዮርጊስ በመጽሐፈ ሰዓታት እመቤታችንን ሲያወድስ፦

ለአዕፅምትኪ ዙሉ፤
ባሕርያተ ሰማይ ዘላዕሉ፤
በእምትንት ወሥርው እለ ተሰንሰሉ፤
ወለደም ነፍስተ እሉ፤
ሰላም ለኪ።

ይላታል። ትርጓሜው፦ "በጅማትና በሥር ለተሰናሰሉ፤ ሰማያዊ ባሕርይ ላላቸው፤ ለአጥንቶቿ ሁሉ፤ 'የነዚህ ነፍስ ለሚሆን ደምሽም ሰላም እላለሁ፤' ማለት ነው። ቁልፉ ቃል "ወለደም ነፍስተ እሉ - የእነርሱ ነፍስ ለሚሆነው ደምሽም…" ነው። በአማርኛ አነጋገር የሰው ደም በግፍ የሚያፈስና በአርድ ጊዜ የእንስሳት ደም በገበታ አቁሮ ጠብሶ የሚበላ ሰው "ነፍስ በላ" መባሉ 'ደም የነፍስ ማደሪያ ነው' ተብሎ ስለሚታመን ነው።

[49] መጻሕፍተ ብሉያት ክልኤቱ፡ ገ.69
[50] ሃይማኖተ አበው ዘአትናቴዎስ ም.23:26፡ገ .76

# ምዕራፍ ሁለት

## ጥንተ አብሶ፡- ትርጓሜው፣ ምንነቱ፣ ውጤቱና ድምሳሴው፤ ከአንጻራዊ እይታ ጋር

### 2.1 ጥንተ አብሶ፡- የቃሉ ትርጉም፤

(2.1.1) ጥንተ አብሶ ስያሜው የሁለት ቃላት ጥምረት ውጤት ነው፡፡ "ጥንት" እና "አበሳ"፡፡ (1) ጥንት "ወጠነ" ከሚለው የግእዝ ቃል የወጣ ሲሆን ትርጉሙም "ጀመረ" ማለት ነው፡፡ ጥንት=መጀመሪያ፡፡ (2) "አበሳ" መነሻው "አበሰ" የሚለው የግእዝ ግስ ነው፤ ትርጓሜው "በደለ"፡፡ አበሳ=በደል፡፡ ሁለቱ ቃላት ሲጣመሩ "የመጀመሪያ በደል" = "ጥንተ አብሶ" የሚለውን ጥምር ቃል ያስገኛሉ፡፡ እንደ ቃልነቱስ "የመጀመሪያ በደል" ለማለኘት ግእዙ "አበሳ ጥንት" ቢሆን ቀና ይሆን ነበር፤ "ጥንተ አብሶ" ሲባል ዘይቤውን ጠብቀን እንተርጉም ካልን "የበደል መጀመሪያ" ነው የሚሆን፤ ቢሆንም "መጽሐፍ ምሥጢር እንጂ ዘይቤ አይጠነቅቅም" የሚለውን ብሒል ተንተርሰን ልማዳዊውን አካሔድ ተከትለናል - ጥንተ አብሶ=የመጀመሪያ በደል፡፡ የመጀመሪያ በደል የተባለው የመጀመሪያው ሰው የመጀመሪያ ሕግ አፍራሽነት ነው (ዘፍ.3:6)፡፡ በልማድ በደለኛው የአዳም ብቻ እንደ ሆነ ቢገለጽም ተሳላፊዎቹ ሁለቱም ናቸው፤ አዳምና ሔዋን፡፡ ለዚህ ነው ኦርቶዶክሳውያን ሊቃውንት "በጌጋየ አዳም ወሔዋን ሱራፊ ዘዐጸዋ" እያሉ የሁለቱንም በደል አዛርፈው/ አቀናጅተው የሚገልጹት፡፡[1] በደሉን (ጥንተ አብሶን) የሚገልጹ ቃላትን በመጠቀም ረገድ ግእዛችን "አበሳ"ንና "ጌጋይ"ን እያቀያየረ ይጠቀማል፤ አንዳንድ ጊዜ "ኃጢአት" የሚለው ቃልም ጥቅም ላይ ይውላል፡፡ መተርጉማን በበኩላቸው ሦስቱን ቃላት ለተለያየ ዓይነት የበደል መግለጫ የመጠቀም ባሕል ያላቸው ይመስላሉ፡፡ ለምሳሌ፡- ከማቴዎስ ወንጌል 6:12 ከተቀዳው የአቡነ ዘበሰማያት ጸሎት ውስጥ "ኅድግ ለነ፤ አበሳነ ወጌጋየነ" ተብሎ ሁለቱም ቃላት (አበሳ እና ጌጋይ) የሰፈሩበትን ንባብ ትርጓሜ "አበሳ የዓመት

[1] ማኅሌተ ፅጌ



በደል፤ ጌጋይ የዕለት በደል" ሲሉ ልዩነታቸውን ይጠቁማሉ፡፡[2] ሊቀ "አበሳ" ለከባድ በደልና ንስሐውም በከብደቱ መጠን ዓመታትን በሚወስድ ቀኖና ለሚገለጽ በደል የዋለ ስያሜ መሆኑን ይጠቁሙናል፡፡ "ጌጋይ" ግን ዕለቱን እርስ በእርስ ይቅር በመባባል የሚሰረይ ቀላል በደል መሆኑን ያመለክቱናል፡፡

(2.1.2) የ"ኃጢአት"ን እና የ"አበሳ"ን ልዩነት በሚመለከትም በመዝ. 31:4 ግእዙ "ኃጢአትየ ነገርኩ፤ ወአበሳየ ኢኀባዕኩ" ያለ ሲሆን መደበኛው አማርኛ መጽሐፍ ቅዱስ "ኃጢአቴን ለአንተ አስታወቅሁ፤ በደሌንም (ወአበሳየ) አልሸሸግሁም" ሲል ፈትቷል፡፡ ትርጓሜው ደግሞ "ጥቃቅኑን ኃጢአት ነገርሁ፤ ታላላቁን ኃጢአቴን (አበሳዬን) አልሰወርሁም፤" በማለት ኃጢአትንና አበሳን ታናሽና ታላቅ ወይም ጥቃቅንና ከባድ ለሚለው የበደል ዓይነት ለያይቶ ለመሰየም ይጠቀምባቸዋል፡፡[3] በተመሳሳይ "ኅጸበ ወአንጽሐኒ እምኃጢአትየ፤ ወእምአበሳየኒ አንጽሐኒ" የሚለውን የመዝሙረ ዳዊት 50:2 የተረጎሙ አበው ሲያብራሩ "ኅጢአት ታናሽ፣ አበሳ ታላቅ " እያሉ ደረጃ ሰጥተውታል፡፡[4] ስለዚህ የመጀመሪያው (የጥንቱ) አዳማዊ በደል "አበሳ" ቢባል የበደሉን ክብደት ለመግለጽ ቃሉ ብቃት አለው ማለት ነው፡፡ ፈረንጆችም ቃላቱን፡- Sin (ኃጢአት), Iniquity (አበሳ) እና Transgression (መተላለፍ) እያሉ የተለያዩ ስያሜዎችን በተለዋጭነት ይጠቀማሉ፡፡ ዞር ዞር ነው ሽንኩርት አንድ ራሱም ቢበሉ፤ ሁለት ራሱም ቢበሉ የአፍ መጣ እንደሚቀይር ኃጢአትም ታላቅ ታናሽ ቢባልም ሁሉም ከሲኦ ያድላል፤ ድቀት ያመጣል፤ ያሸማቅቃል፡፡ "መርገም" እና "ፍዳ" የሚሉት ቃላት ኃጢአትን/ አበሳን/ በደልን ተከትለው የሚመጡ ጊሎች መሆናቸውን መረዳት አይከፋም፤ መርገምና ፍዳ የኃጢአት ውጤቶች ናቸው፡፡ ፈደሪ- ከፈለ፡፡ "ፍዳ" የቅጣት ፍርድ ማለት ነው - ፍርደኛነት፤ መርገም የኃጢአተኛነት ውሳኔው ነው፡፡

(2.1.3) ከላይ ያለው የትርጉምና የቃል አመራረጥ ሒደት እንዳለ ሆኖ "ጥንተ አብሶ" የሚለው ስያሜ እንደ ወረደ ቃል በቃል በቀደምት ኢትዮጵያውያን አበው ወጥ እና የትርጉም ሥራዎች በዚህ መጠሪያ

[2] መ/ሐ ታመነ፤ የዘወትር ጸሎት ትርጓሜ፤ 2000 ዓ.ም፡ ገ.40
[3] መዝሙረ ዳዊት ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.179
[4] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.265

ተብራርቶና ተፍታቶ ስለ መታወቁ ማስረጃ ማቅረብ እንደሚቸግር መገለጹ የተገባ ነው። ከጥንተ አብሶ ይልቅ "ቁራኝነት" የሚል ቃል ይበረክታል። ምሳሌዎችን ሳስቀምጥ፦ (1) "የሰው ባሕርይ በዲያብሎስ በሠራዊቱ በቁራኝነት ተይዞ ይኖር ነበርና ... ይድን ዘንድ እግዚአብሔር የሰውን ባሕርይ አሰበ" (2) አዳምና ሔዋን ከድቀት በኋላ " ... ለብዙ ኃጢአት ወደ መገዛት ገቡ ... ለሰይጣናት ቁራኞች ሆኑ። ... በአዳም በልጆቹም ሁሉ [ሰይጣናት] በቁራኝነት የሠለጠኑ ሆኑ ... ምርኮ ማራኪ በምርኮኞቹ እንዲሠለጥን። ... የሞተውን ሥጋውን በመቃብር ነፍሱን በሲዖል በገሃነም ተቆራኝተው ይኖሩ ነበር። ... አዳም ከተፈጠረ ጀምሮ አምስት ሺሕ አምስት መቶ ዘመን እስኪፈጸም ድረስ ቁራኝነት ፈጽሞ ተደረገባቸው"[6] እንዲህ ሲባል ግን "ጥንተ አብሶ" ቃሉ ጭራሽ አይታወቅም ማለት አይደለም። ለምሳሌ፦ በሰኞ ውዳሴ ማርያም ትርጓሜ "ነበ ሀለወት ብዝኀት ኃጢአት በህየ ትበዝህ ጸጋ እግዚአብሔር" የሚለውን ቃል አበው ሲያብራሩ "ብዙ ኃጢአት ካለች ዘንድ ጸጋ እግዚአብሔር አለ ... አንድም ጌታ ሰው መሆኑ በምልአት ኃጢአት ነውና በጥንተ አብሶ (ምክንያት)ስ ሰው ሆኖ ቢሆን ለአዳምና ሔዋን ብሉ ሰው ሆነ እንጂ እኛስ በግዝረታችን በመሥዋዕታችን እንድናለን ባሉ ነበርና። ኀበሰ መጽአ በጥንተ አብሶ እምኢኮነ ሞቱ ለቤዛ ብዙኃን - አዳምና ሔዋን እንደ በደሉ በመጣስ ... ሞቱ የሁሉን ኃጢአት ለማስተሠረይ እንደ ሆነ ባልተጸፈም ነበር" እንዲል[7]" ሲሉ ለቃሉ እንግዳ አለመሆናቸውን ያሳዩናል።[8] ሆኖም እንደ ሌሎቹ አብያተ ክርስቲያናት ቃሉን አያጋንኑትም!

(2.1.4) ወደ ውጭ ጸሐፍት ስናማትር አሳቡ ጎርጎርዮስ ዘኑሲስ የመሳሰሉ አበውን ጨምሮ በቀደምት አበው ሲብላላ ቢኖርም ቃሉን "Original Sin" (ጥንተ አብሶ) ሲሉ የክርስትና ስም ያወጡለት ካቶሊካውያን ሳይሆኑ አይቀሩም። በተለይ በ5ኛው ክፍለ ዘመን የነበረው የምዕራባውያን ሊቅ አውግስጢኖስ ጽንሰ አሳቡን በማጎልበት ይጠቀሳል። የእንግሊዝኛ መዛግብት ለጥንተ አብሶ መገለጫ ተለዋዋጭ ቃላትን ይጠቀማሉ። አዳማዊ በደል (Adamic guilt)፣ የውርስ ኃጢአት (Hereditary Sin)፣ የቀደመ በደል

[5] ሃይማኖተ አበው ዘቄርሎስ፡ ገ.298
[6] መቅድመ ወንጌል፡ ገ.20
[7] ድርሳነ ዘዮሐንስ አፈወርቅ ምዕ.17.ቁ.50-51፡ገ.303
[8] ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.25



(Original Coruption)፣ የቀደምት ወላጆች ኃጢአት (Ancestral Sin) ከጥንተ አብሶ (Original Sin) በተጨማሪ የመጀመሪያውን በደል ለመግለጽ አገልግሎት ላይ የዋሉ የእንግሊዝኛ ቃላት ናቸው። ከየምንጮቻቸው እንደምንረዳው የምሥራቅ ኦርቶዶክሶች ጥንተ አብሶ (Original Sin) ከሚለው ቃል ይልቅ የቀደምት ወላጆች አበሳ (Ancestral Sin) ማለትን ይመርጣሉ። በደሉ የአያቶቻችን የአዳምና የሔዋን ብቻ ነው፣ እኛ ቅጣቱን (መርገሙን) እንጂ ኃጢአቱን አንወርስም ለማለት። የእኛ ሊቃውንት አዳማዊውን በደል "ጥንተ አብሶ"፣ ዕለታዊውን የየግላችንን በደልና መተላለፍ "ገጋይ/ ኃጢአት/ ምልአተ ኃጢአት" በማለት ለመለየት እንደሚሞክሩት ሁሉ የውጮቹ ደግሞ የቀደመውን የአዳምና ሔዋን በደል ጥንተ አብሶ (Original Sin)፣ የዘወትሩን በግለሰብ ደረጃ የሚሰራ በደል ምልአተ ኃጢአት (Actual Sin) ሲሉ ይለያዩአቸዋል።

## 2.2 ጥንተ አብሶ፡- ምሥጢራዊ (መጽሐፋዊ) ትርጉሙ

(2.2.1) ኦሪት ዘፍጥረት ምዕራፍ 3፡17 እንደ ነገረን አዳም የፈጣሪውን ትእዛዝ በመተላለፉ "ርግምተ ትኩን ምድር በተግባርከ - ምድር በሥራህ የተረገመች ትሁን" የሚል አምላካዊ ርግማን ደረሰበት። ርግማኑ በእርሱ ተወስኖ አልቀረም፤ "ምድር" የሚለው ቃል "በስመ ማኅደር ይጼዋዕ ኀዳሪ" እንዲሉ አበው በምድር ላይ ለሚኖሩ የአዳም ልጆች ማለትም "ዘዘር በሩካቤ ለተወለዱ ልጆቹ" ሁሉ ተረፈ።[9] መንፈስ ቅዱስ እፍ ያለበት አዳም ጸጋው ተገፈፈ፤ በረከቱ ተወሰደበት። የሰው ባሕርይ ማደፍ ጀመረ። "እግዚአብሔርም የሰው ክፋት በምድር ላይ እንደ በዛ፣ የልቡ አሳብ ምኞትም ሁልጊዜ ፈጽሞ ክፉ እንደ ሆነ አየ፤" (ዘፍ.6:15)። ጠቢቡ እና ነቢዩ ሁሉ ስለ ሰው ልጅ ለክፋት ተላልፎ መሰጠት ጻፉ፣ ተናገሩ (መክ.9:3፣ ኤር.17:9)። በአንድ በአዳም በደል የተነሣ ኃጢአት ወደ ዓለም ገባች፤ "ኃጢአት አዳም አሐዱ ብእሲ ቦአት ኃጢአት ውስተ ዓለም እንዳለው ሐዋርያው (ሮሜ.5:12)። ኃጢአቱን ተከትሎም በሰው ልጅ ላይ ሞት ነገሠ። "ኃጢአት ሰውን ሁሉ ኃጥእ አሰኘችው።"[10] አዳም ከመተላለፉ የተነሣ በዘፍጥረት 2፡17

[9] መጻሕፍተ ብሉያት ክልኤቱ፡ ገ.37
[10] የቅዱስ ጳውሎስ መጽሐፍ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1988 ዓ.ም.፡ ገ.52

ሞትን ትሞታለህ" የተባለው ድንጋጌ ተፈጸመበት። ከእግዚአብሔር ፊት ሸሸ፤ ወደ ታች ተጋዘ። አማናዊው ሞት እርሱ ነበር - ከእግዚአብሔር መራቁ፤ መራቆቱ፤ "ሞታ ለነፍስ ርኂቅ እምእግዚአብሔር" እንዲሉ መተርጉማን። ወይም "Death is being separated from God" እንዲሉ እነ ቅዱስ አትናቴዎስ እና እነ አቡነ ሺኖዳ። "ከመርገም በኋላ የመጣው ጸጋ አልባ ሁኔታ ኃጢአትን የሚጋብዝ፣ ለክፉ ነገር የተመቻቸ ነበር። ይህም ሁኔታ ለልጅ ልጆቹ የሚተላለፍ ሆኗል። ... ድርጊቱ ቀጥታ በዘር ተላለፈ ማለት ሳይሆን ጸጋ በሌለበት ጊዜና ቦታ የተፈጠረውን በኃጢአትና በመርገም የመጣውን የውስጥ የውጭ ሁኔታ መውረሳችንን መናገር ነው።"[11] "ሰይጣን በአዳም ላይ ኃይልን፣ መዊዕን ገንዘብ አደረገ፤ ምርኮው ሆነ። ... ልጆቹም ከሱ ጋር እንደሱ ተገዙ። ... በብዙ ነገር ለማሳ[ሳ]ት ሰይጣን ሠለጠነባቸው። ... መከራ ሠለጠነባቸው።"[12]

(2.2.2) በአዳም ላይ የመጡትን ቅጣቶች ብፁዕ አቡነ መልከ ጼዴቅ ሊቃውንትን ዋቢ አድርገው በሦስት ዋና ዋና ክፍሎች መድበዋቸዋል። (1) በጥንተ ፍጥረት የተሰጠው የእግዚአብሔር ልጅነቱ መወሰድ፣ (2) በመንፈስ ማርጀት (ብልየት ማግኘት)፣ (3) ከመንፈስ ቅዱስ ማኅደርነት መውጣት ናቸው። በተለይ በጎ ነገሮችን ሁሉ ለመሥራት አጋዥ የሆነው መንፈስ ቅዱስ እንደ መሆኑ ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ከሰው ልጆች መለየቱ ከባድ ቅጣት እንደ ሆነ ያስምሩበታል።[13] ሊቀ ጉባኤ አባ አበራ እንዲሁ ከአዳም በደል ተነሣ የሰው ልጆች ከዕውቀት መጉደላቸውን፣ የመወሰን ኃይላቸው መዳከሙን፣ በፍትወት (የሥጋ ምኞት) መሸነፋቸውን፣ በመከራ መፈተናቸውንና በራሳቸው ላይ ሞተ ሥጋና ሞተ ነፍስ ማምጣታቸውን አብራርተዋል።[14] የኤርትራ ኦርቶዶክሳውያን ወንድሞቻችን በጉዳዩ ላይ በጻፉት ሐተታ አዳምና ሔዋን ላይ የደረሰውን ቅጣት ሲገልጹ "ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ተገፈፈባቸው፤ ስመ ወልድና አጡ። ዕርቃን ሆኑ፤ ክብራቸውን ጣሉ። በዚህም ምክንያት በሞተ ሥጋ ላይ ሞተ ነፍስ፣ በመርገመ ሥጋ ላይ

[11] ሊቀ ጉባኤ አበራ በቀለ፣ ትምህርተ ሃይማኖትና ክርስቲያናዊ ሕይወት፣ 2ኛ ዕትም፣ 2006 ዓ.ም.፡ ገ.90
[12] መቅድመ ወንጌል፡ ገ.19
[13] አባ መልከጼ.ዑ.ኤ፡ ገ.144
[14] ሊቀ ጉባኤ አበራ በቀለ፡ ገ.97



መርገመ ነፍስ ተጨመረባቸው። ከእግዚአብሔር ኅብረት፣ አንድነት ተለዩ። ጸጋቸው ተገፈፈ። ነጻነት አጡ። ለፍላጎታቸው ተገዙ። ባሕርያቸው ደከመ። ፊላቸውን መግዛት ተሳናቸው። ኃጢአትን የሚያሸንፍ አእምሮአቸው በሰይጣን ፈተና የሚሸነፍ ሆነ፤" በሚል ድምጸት ጽፈውታል። ይህ ሁሉ የሆነው በጥንተ አብሶ የተነሣ ነው። ቃላቸውን እንደ ወረደ በጥቂቱ ልዋስ፣ "ዘሒ ድማ ብንፍሓት ንዘሓደርም ጸጋ (ሃብቲ) መንፈስ ቅዱስ ውሉድነት ምሳሴ (ሀብተ ውልድና) ተገፈፉ ዕርቃኖም ተረፉ ክብሪ ስኣኑ። በዚ ምኽንያት እዚ ኸኣ ኣብ ልዕሊ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ ተፈሪድዎም፤ ኣብ ልዕሊ መርገመ ሥጋን መርገመ ነፍስን ተቐሪናዎም፤ ካብ ሓድነት ብኣርዑት እግዚአብሔር ተፈልዩ። ስለዚ ጸጋኦም ተገፈፉ፤ ናጽነት ስኢኖም እኩያት ፍትወታት (ፍትወታተ ሥጋ) ሓየሎም፤ ባህርይኦም ደኺሙ፤ ንኃጢአት ዚስዕር ዝነበረ ኣእምሮኦም፤ ብፈተናታት ሰይጣን ብቐሊሉ ዝሰዓር ስለ ዝኾነ ኣብ ዝተረፈ (ብድሕሪኦም ዚመጽእ) ወለዶኦም ምፍራስ ሕጊ፣ ስሰዕቲ፣ ትዕቢት፣ ትህኪት፣ ክፍኣትን ድንቍርናን ነገሠ። እዚ ኹሉ ከኣ እቲ ናይ መጀመርታ ኃጢኣት (ጥንተ ኣብሶ) ዘምጽኦ ጸገም እዩ ነይሩ።"[15]

(2.2.3) የአበውን መጻሕፍት ስናይ "የኃጢአት መጀመሪያ በሆነች ከግእዛኑዋ በወጣች በፈቃዳችን ምክንያት በእኛ ፈጽማ ጸንታ በነበረች ታላቅ ኃጢአት ተጎድተን" እንደ ነበር ይነግሩናል።[16] አቡሊዲስ የተባለው ኦርቶዶክሳዊ አባት ከአዳም እንሥቶ እስከ ሙሴ፤ ከሙሴም በኋላ እስከ ክርስቶስ መሰቀል ድረስ ያሉ ደጋግ አበውን በአዳም አምሳል ሞት እንደ ገዛቸው ይተርካል።[17] የሞት ግዛት የተዘረጋው በበደሉ ብቻ ሳይሆን ባልበደሉም ላይ ነበርና የገነት በር ለፈያታዊ ዘየማን በክርስቶስ ደም ማኅተምነት እስከትከፈትለት ድረስ የአዳም ልጆቹ ሁሉ ጽድቃቸው መርገም ሆኖ በመንጸፈ ደይን ቆዩ፤ ወደ ሲዖል ተጋዙ (ኢሳ.64፡6። ሮሜ.5፡14)። ነቢዩ ዳዊት ለዚህ ነው "ወበአበሳ ወለደተኒ እምየ፤...ኃጢአት በሠለጠነበት ወራት ተወልጃለሁና" እያለ በመዝ.50፡3

[15] http://maeadot.blogspot.com/2012/08/blog-post_16.html : revisited Oct 26, 2016.
[16] ሃይማኖተ አበው ዘቄርሎስ፡ምዕ.70፡19፡ ገ.257
[17] ሃይማኖተ አበው ዘአቡሊዲስ፡ምዕ.42፡9-11፡ ገ.145

ጸጸቱን የሚናገር።[18] መጻሕፍቱ ከበደሉ ይልቅ የበደሉ ውጤት (consequence of sin) ላይ ማተኮራቸውን ማስተዋል ይገባል።

## 2.3. የጥንተ አብሶ ውጤት ምንድን ነው? የሚተላለፈው ርግማኑ ብቻ ነው ወይስ ኃጢአቱም? የኤርትራ፣ የግብጽ ኮፕቲክ፣ የካቶሊክ እና የምሥራቅ ኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያናት አመለካከት

(2.3.1) የጥንተ አብሶን ውጤት በሚመለከት በደሉን የሠራው አዳም ቢሆንም ቅጣቱ "በበደሉትም ባልበደሉትም" ላይ እንደ ሆነ ቅዱስ ጳውሎስ በግልጽ ተናግሯል (ሮሜ.12:14)። በደለኛ ለመባል የአዳም ልጅ መሆን በቂ ነበር። ምክንያቱም "እስመ ኵሉ፡ በአምሳለ አዳም ተፈጥረ - ሰው ሁሉ በአዳም አምሳል፣ እንደ አዳም ደክሞ ኃጢአት ሠርቶ ነበርና"[19] ነገሩ ቅኝ በምትገዛ አገር ውስጥ እንደ መወለድ ነው። በተፈጥሮህ ነጻ ሆነህ ብትወለድም ከሰፈነው የቅኝ አገዛዝ ሥርዓት የተነሣ በዜግነትህ ነጻ አይደለህም። ወይም ልክ ከባድ ዓለም አቀፋዊ ማዕቀብ በተጣለበት አገር ያሉ ዜጎች ሁሉ በማዕቀቡ የተጠቀሱ ከውጭ የሚመጡ ቁሳቁሶችን በማግኘት ረገድ በእጦት እንደሚፈተኑት ሁሉ የሰው ልጆችም በአዳም በደል የተነሣ ራሳቸውን የእርሱ በደል ላመጣው ማዕቀብ አጋልጠው ይኖሩ ነበር። ወይም ልክ ተላላፊ ሕመም ያለባት ነፍሰ ጡር እናት ለወላጅ መደረግ ያለበትን ክትትል አለማድረግ እርሷንም ሆነ ልጇን ለሕማም እንደሚያጋልጥ የኃጢአት መከላከያ የሆነው ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ከተወሰደባት ሔዋን ማኅፀን የወጡ ልጆቿ ሁሉ ጸጋ ቢሶች፣ ለሕማመ ኃጢአት የተጋለጡ ነበሩ። ያልተከተቡ ልጆች በቀላሉ ታማሚ እንደሚሆኑ ጸጋ የተለያቸው የአዳም ልጆች ለኃጢአት ተጋለጡ። የዘፍጥረቱ ንጽሐ ባሕርይ (Original righteousness) ጠፍቶ ጥንተ አብሶ (Original Sin/ ቁራኝነት/ ርግመት) ተዘረጋ። ከርግማኑ በኋላ ከሰው ልጆች መካከል አዳምና ሔዋን መጀመሪያ

[18] የመዝሙረ ዳዊት አንድምታ፡ ገ.265
[19] የቅዱስ ጳውሎስ መጽሐፍ፣ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.53



ሊፈጠሩ በነበራቸው በመርገም ያልተዳደፈና በጸጋ የተሞላ የንጽሕና ደረጃ ሆኖ የሚወለድ አልነበረም።

(2.3.2) የጥንተ አብሶ (በመጀመሪያው የአዳም በደል የተነሣ የሰው ልጆች ጸጋ የተገፈፉበት ሁኔታ) መኖርን በሚመለከት ዋና ዋናዎቹ የዓለም አብያተ ክርስቲያናት ይስማማሉ። "አንድ ሰው ከአዳም ስለ ተወለደ 'ቅጣቱን/ ፍዳውን/ መርገሙን' ብቻ ነው ወይስ 'ኃጢአቱንም (አበሳውንም)' ተጋርቶ ይወለዳል?" የሚለው ጉዳይ ላይ ግን የተለያየ አመለካከት የሚንጸባረቅ ይመስላል። ከኤርትራ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ወንድሞቻችን በኩል "ኃጢአት እንደ ሥጋዊና ደማዊ ባሕርይ አይወረስም፤ ፍርዱ/ ፍዳው (ቅጣቱ) ብቻ ነው የሚወረሰው። ጳውሎስም በሮሜ መልእክቱ ሞት እንዴት እንደ ነገሠ ሲተርክ 'የበደሉም'፣ 'ያልበደሉም' ነው ያለው!" ሲሉ ከላይ በተጠቀሰው መጠመሪያቸው (ብሎጋቸው) ይከራከራሉ። ጨምረው ሲያብራሩም፦ "የወላጅ ኃጢአት ሳይሆን የወላጅ ዕዳ ነው የሚተላለፈው፤ በዘር ቁራኝነት የወረደው የአዳምና የሔዋን ኃጢአት ሳይሆን የተላለፈባቸው መርገም ብቻ ነው!" ሲሉ ጌታ ለንጽሕና አምሳል የጠቀሳቸውን የወንጌል ሕጻናት በምሳሌነት ይጠቅሳሉ (ማቴ.18:3፤ 19:14)። ኤርትራውያን ወንድሞቻችን እንደሚሉት፣ "ሕጻናት አይበድሉም፤ ሆኖም የአዳም ልጆች ስለ ሆኑ ብቻ ከመርገም በታች ሆነው ይወለዳሉ።" ቃላቸውን እላይ ከቀረበው ገጻቸው ተውሰን እንደ ወረደ ስናቀርበው "ኃጢአት ልክዕ ከም ሥጋን ደምን፡ ባሕርይን ኣይውረስን፡ ኣይክፈልን ድማ እዩ። ጥንተ ኣብሶ ተባሂሉ ዝጽዋዕ ግና እቲ ንኣዳምን ንሔዋንን ዚተዋህቦም ፍርዲ እዩ። ዝበደሉን ዘይበደሉን ኵሉም ሞት ገዚኡዎም ከም ዝበለ ሓዋርያ ቅዱስ ጳውሎስ፣ ዕዳ ኣቦ እደ ኵሉም ሞት ገዚኡዎም … ናብ ደቆም ከም ዚሓልፍ፣ እቲ ናይ ኣዳምን ሔዋንን መርገም፣ ባርነት፣ ሕማመ ሥጋን ሕማመ ነፍስን ሞተ ሥጋን ሞተ ነፍስን ናብ ደቆም ኪመሓላለፍ ይነብር ደኣ እምበር ጥንተ ኣብሶ ካብ ባሕርይ ኣዳም ዝተወሰደ ኪመሓላለፍ ነይሩ ናይ ውርሻ ኃጢኣት (Original sin) ኣይኮነን። ብባሕርይ ዚመሓላለፍ ነይሩ እንተዝኸውን ግና ዘይበደለ ኣይምተረኽበን፤ 'ዝበደሉን ዘይበደሉን' ተባሂሉውም ክኣ ኣይምተመቕሉን፤" ይሉናል።

(2.3.3) በአውግስጢኖስ አስተምህሮ በሚጓዙት ካቶሊካውያን ዘንድ ከአዳም ውድቀት ጀምሮ የሰው ልጅ ቅጣቱን ብቻ ሳይሆን በደሉንም (አበሳውን/

ኃጢአቱን)[20] ከማኅፀን ጀምሮ በሩካቤ ጊዜ ዘር ከወንዱ ወደ ሴቷ ማኅፀን በሚሄድበት ግንኙነት አብሮ ስለሚቀበል የነፍስ የማገናዘብ ችሎታ እንደ ተነጠቀ/ ፈጽሞ እንደ ተዳከመ ተደርጎ ይታሰባል።[21] የምሥራቅ ኦርቶዶክሳውያን ከካቶሊካውያን በተቃራኒ "The Orthodox Church has kept alive the original understanding of the early Church as regards "Original sin." The early Church did not understand "original sin" as having anything to do with transmitted guilt but with transmitted mortality. Because Adam sinned, all humanity shares not in his guilt but in the same punishment . ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ጥንተ አብሶን በሚመለከት የቀደመችውን ቤተ ክርስቲያን ብሒል (ዛሬም) አጽንታ ይዛለች። የቀደመችው ቤተ ክርስቲያን ጥንተ አብሶን ከዘር ወደ ዘር ከሚተላለፍ በደል ጋር ሳይሆን (ከሚተላለፈው) መዋቲነት ጋር አያይዛ ነው የምትረዳው። አዳም በመበደሉ የሰው ልጆች የሚጋሩት በደሉን ሳይሆን ፍዳውን (ቅጣቱን) ነው፤" ይላሉ።[22] ስለዚህ በእነርሱ እምነት ሊቃለል/ ሊወገድ የሚገባው ቅጣት እንጂ ድምሳሴ (ሥርየት) የሚጠብቅ በደል የለም።[23] ይህን አቋማቸውን ከእመቤታችን ጽንሰት ጋር በማያያዝ እንመለስበት።

ወደ ግብጻውያን ወንድሞቻችን ስናልፍ በእነርሱ በኩል የአዳም ቅጣት (consequence of sin) ብቻ ሳይሆን አበሳው (ኃጢአቱ) ጭምር ወደ ልጆቹ እንደ ተላለፈ ይተርካሉ፤ የጥምቀት አስፈላጊነት (The Purpose of Holy Paptism) ይህን የውርስ በደልና ቅጣት ለማስተሥረይ እንደ ሆነ

---

[20] አውግስጢኖስ በቀደመ እምነቱ ግኖስቲክ ነበር። ግኖስቲኮች ደግሞ ጋብቻንና ሩካቤ ሥጋን እንደ ድቀት፣ ከክብር እንደ መውረድ፣ እንደ ርኩሰት ነው የሚያዩት። (አቡነ ጎርጎርዮስ፣ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ፡ገ.57፣61፣65፣67።) ስለሆነም አውግስጢኖስ ይህን የኃጢአትን በሩካቤ ተላላፊነት አስተምህሮ ከቀደመ ሩካቤን እሩካሽ ግኖስቲካዊ እምነቱ ይዞት የመጣ ይመስላል፤ በጥንተ አብሶ ትንታኔውም ይህ አስተሳሰቡና የምንታዌ እርሾው ስለመኖሩ ይጠረጠራል። የኛ ሊቃውንት ግን "መውለድ ለአዳምና ለሔዋን በረከት እንጂ መርገም አይደለም። አዳምና ሔዋን ምንም እንኳ ልጅ የወለዱ ከበደል በኋላ፣ ከገነት ከወጡ በኋላ ቢሆንም 'ብዙ ተባዙ፤ ምድርንም መሏት' የሚለውን በረከት ከእግዚአብሔር ያገኙት በገነት ሳሉ ነው። ... ይህ የመውለድ በረከት በተፈጥሮ የተሰጠ እንጂ በኃጢአት ውርስ የመጣ አይደለም።" ይላሉ። (አለቃ አያሌው ታምሩ፣ ምልጃ፣ ዕርቅና ሰላም፣ 1992 ዓ.ም፣ ዲማ:7.58።)

[21] Abune Paulos;p.307

[22] http://www.antiochianarch.org.au/Orthodox-view-on-Immaculate-Conception.aspx

[23] The Encyclopedia of Eastern Orthodox Christianity, Edited by John Anthony McGuckin , 2011, p.429



ይናገራሉ።[24] በእነሱው ቃል ስንገልጸው፡- "The Holy Sacrament of Baptism is for the remission of sins which is the Original Sin with which everyone is born. We were in Adam when he sinned and in him we all have sinned. This is in addition to the corrupted image that moved away from the holy and pure image of God. We, humanity, the descendants of Adam are born with the original sin as well as his distorted image which became prone to sin - ሥርዓተ ጥምቀት የሚከናወነው እያንዳንዱ ሰው ሲወለድ አብሮት ለመጣው ጥንተ አብሶ ሥርየት ነው። አዳም ሲበድል እኛም በአዳም (ወገብ) ነበርንና በእርሱ ሁላችን በድለናል። ይህም ከሳደፈው ሰውነታችንና ከእግዚአብሔር ንጽሕ አምሳልነት ከመራቃችን በተጨማሪ ነው። የአዳም ልጆች የምንሆን እኛ ሰብአውያን ፍጥረታት ከጥንተ አብሶና ከሳደፈ ማንነት ጋር በመወለዳችን ለኃጢአት ተጋላጮች ነን።[25] ግብጻውያኑ አክለው "We are born with Adam's sin and its consequence, which is death; for death is the wage of sin. Adam's sin has infected all his posterity; and the corrupt nature inherited from Adam drags all his posterity into sin ... ከአዳም ኃጢአትና ከኃጢአቱ ውጤት ይኸውም ሞት ጋር ተወልደናል፤ የኃጢአት ደሞዝ ሞት ነውና። የአዳም ኃጢአት ተወላጆቹን ሁሉ አጉድፏል፤ ከአዳም የተወረሰው የጎደፈ ተፈጥሮ የእርሱን ዘሮች ሁሉ ወደ ኃጢአት ስቧቸዋል፤" ሲሉ መርገሙንም ኃጢአቱንም ተቀራኝተን እንደምንወለድ ያትታሉ።[26]

(2.3.4) የእኛን ብሔራውያን ሊቃውንት አቋም ስንፈትሽ አለቃ ኪዳነ ወልደ ክፍሌን እናገኛለን። እርሳቸው "የአዳም ኃጢአት ከአባት ወደ ልጅ መውረዱ አዳምን መስለው ተከትለው በሚሠሩት ብቻ ነው እንጂ በማይሠሩትና በሚነቅፉት እንደ ኄኖክ በሚጸየፉት በልጆቹ ሁሉ አይ[ደ]ለም፤ ይኸውም 'ቡርክት አንቲ እምአንስት ወቡሩክ ፍሬ ከርሥኪ' በተባሉት በእናትና ልጅ ይታወቃል። ... ጽድቁም እንደ ኃጢአት ነው፤ ከክርስቶስ ተከፍሎ በመወለድ አይወረስም፤ አባትን መስሎ በመሥራት እንጂ ... በዘርም እንደሚወርድ የአዳም ኃጢአት የነፍስ ነው እንጂ የሥጋ አይ[ደ]ለም፤ ነፍስም እንደ አዳም

---

[24] Coptic Orthodox Dioces of Southern United States, RIT 102, Rituals of The Sacraments, Servants' Preparation Program, 2006, p.1 http://www.suscopts.org/servantsprep/pdf/RIT/RIT102-RitualsoftheSacraments.pdf

[25] http://www.suscopts.org/q&a/index.php?qid=1530&catid=278

[26] Ibid

ነፍስ ከፈጣሪ እፍታ በንጽሐ ጠባይዕ ተገኝታ ከአባት በእናት በተከፈለው በዘርና በደም ታድራለች እንጂ እርሷ አትከፈልም፤" ሲሉ ከሚያራምዱት የነፍስ አፈጣጠር አቋማቸው ጋር አስናስለው የጥንተ አብሶን ትርጉም ከኃጢአትና የመርገም ሐተታው ገለል ያደርጉታል፤ አይቀበሉትም።[27]

(2.3.5) አሰቃ ይህን አቋማቸውን ለማስረገጥ የሚጠቅሷቸውን ኢሳ.42፡5፣ ዘካ.12፡1 እና መዝ.21፡10'ን ከነተጻፉበት ዓላማ የአንድምታ ትርጓሜያቸውን በማጣቀስ ቀደም ሲል ስለ ነፍስ አፈጣጠር ስናነሣ አይተናቸዋልና እንመለስባቸውም። ራሳቸው አሰቃ ኪዳን ወልድ አንምድታውን የሠሩለትንና ለአቋማቸው በሁነኛ አስረጂነት የተጠቀሙበትን ትንቢተ ሕዝቅኤል 18:20 እንይ። "ኢይነሥዕ ወልድ ኃጢአተ አብ - ልጅ ካደገ ራሱን ከቻለ በኋላ ያባቱን ኃጢአት አይሸከምም። ሕጻን ቢሆን ግን ባባቱ ኃጢአት ይቀሰፋል፤ እንደ አክአብ እንደ ሴዴቅያስ ልጆች (2ኛ ነገ.10:1-10፣ 25:5-7)።... ወኢይነሥዕ አብ ኃጢአተ ወልድ - አባትም ሠርቶ ቀጥቶ ካሳደገ በኋላ የልጁን ኃጢአት አይሸከምም። 'እስመ ኵሉ ለለአሐዱ ጾሮ ይጸውር፤' እንዳለ (ገላ.6፡5)። ጽድቁ ለጻድቅ ትከውን ላዕሌሁ - የጻድቅ ሰው ጽድቁ በርሱ ላይ ብቻ ትሆናለች። ወኃጢአቱ፡ ለኃጥዕ፡ ትከውን፡ ላዕሌሁ - የኃጥዕም ሰው ኃጢአቱ በርሱ ላይ ብቻ ትሆናለች። ጽድቅም ሁና፣ ኃጢአትም ሁና ወዳባት አትወጣም፤ ወደ ልጅ አትወርድም፤" ይላሉ።[28] ይህን ጥቅስ እንደ ወረደ ተጠቅመው ነው አሰቃ ጥንተ አብሶ እንደሌለና በአዳም በደል ልጆቹ እንደማይጠየቁ የሚከራከሩት።

(2.3.6) የአሰቃ አቋም ስለ ግላዊ የዕለት ተዕለት ኃጢአት (ምልአተ ኃጢአት - actual sin) ቢሆን ኖሮ የተነገረው ትክክል ይሆናል። ስለ ጥንተ አብሶ ከሆነ ግን ለመቀበል አስቸጋሪ ነው። ምክንያቱም ምንም እንኳ የአዳምን ኃጢአት ስለ መውረሳችን የሚቀርበው ክርክር ላይ የተለያየ አቋም ቢንጸባረቅም በሁሉም አብያተ ክርስቲያናት ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ በአዳም በደል ምክንያት የመጣው ቅጣት በሁላችንም ላይ ተፈጻሚ መሆኑ ይታመንበታል። አሰቃ ለንጽሐ ጠባይዕ ማሳያ በምሳሌነት የጠቀሷቸው

[27] አሰቃ ኪዳን ወልድ፡ ገ.25

[28] አሰቃ ኪዳን ወልድ ክፍሌ፣ መጽሐፈ ሕዝቅኤል፣ ንባቡና ትርጓሜ፡ ገ.190-191



ሄኖክና ኤልያስም ቢሆኑ ኃጢአት ባለመሥራታቸው ገነት ተከፍታ እንደ ጠበቀቻቸው የሚያሳይ ማስረጃ የለም፤ "ብሔረ ሕያዋን ገቡ፤" እንዳለን እንጂ "ገነትን አስከፈቱ፤" አንልም።[29] ገነት እስከ ክርስቶስ ስቅለት ድረስ አዳም ላይ በወረደው መርገም የተነሣ ለበደሉም ላልበደሉም የአዳም ልጆች ዝግ ነበረች። ስለዚህ በግል ባለመበደል ከመርገሙ ማምለጥ አይቻልም።

(2.3.7) ግብጻውያን አባቶች በሕዝቅኤል 18፡18-31 የተጠቀሰው ግላዊ ኃጢአት እና ጥንተ አብሶ ስላላቸው ልዩነት ተመሳሳይ ጥያቄ ቀርቦላቸው፡- "Original sin can be likened to one whose parents are taken into captivity and thrown into a dungeon. Their offspring have no choice but to born into that same state of captivity and within that same dungeon and their children after them, and so on. Since the fall of man, all offspring of humanity was born with original sin... humanity could not escape death under the penalty of original sin ... Sins committed during one's life are on an individual basis and will vary - ጥንተ አብሶ ወላጆቹ በእስር ቤት (በማጎሪያ ካምፕ) በታሠሩ ሕጻን ይመሰላል። (የታሳሪዎቹ) ልጅ በእስረኛ ወግ በእስር ቤቱ ውስጥ ከመወለድ በቀር አማራጭ የለውም። ከ(አዳም) ድቀት ጀምሮ የሰው ልጆች ሁሉ ከጥንተ አብሶ ጋር ተወልደዋል። ... የሰው ልጅ በጥንተ አብሶ የተነሣ የሚመጣውን የሞት ቅጣት ማምለጫ አልነበረውም። [በሌላ በኩል] በሕይወት ዘመን የሚፈጸሙ ኃጢአቶች በግለሰብ ደረጃ ያሉ ናቸው፤ በመጠንም ይለያያሉ!" ሲሉ ልዩነቱን አብራርተው ምላሽ ሰጥተዋል።[30] የአሰቃ አቋም እንዳለ ከተወሰደ ወደ ተወገዘው የቢላግዮስ አሳብ ይመራናል። ጌታ ከነፍሳችን ነፍስን ነሥቶ ተዋሐደ ካላልን "ያልተዋሐደውን አዳኝ" ወደሚል የምሥጢረ ሥጋዌ ተፋልሶ ይጨምረናል። ያም ሆኖ ደግሞ ስለ ጉዳዩ እርሳቸው የጻፉት አሳብ ከሁለት ገጽ ያልበለጠ በመሆኑ ጽሑፉ ሙሉ አሳባቸውን ተከትሏል ለማለት ስለማያስችል፣ ጉዳዩ በእግረ መንገድ የተነሣ ስለ ሆነ፤ ዛሬ መካከላችን ቆመው አቋማቸውን አፍታተው ራሳቸውን የሚከላከሉበት ዕድል ስለ ሌለ

[29] አክሊማሮስ ዘሥሉስ ገጽ 92 እንደሚነግረን ብሔረ ሕያዋንና ገነት አንድ አይደሉም።

[30] http://www.suscopts.org/q&a/index.php?qid=1486&catid=278

አሳባቸውን እንደ አሳብ ባለበት አክብረን ባበረከቱልን በግለሰብ ደረጃ ቀርቶ በተቋም እንኳ ለማከናወን የሚያዳግቱ ትሩፋቶች አመስግነን እንለፋቸው።

(2.3.8) አቡነ መልከ ጼዴቅ በበኩላቸው የኃጢአተኛ ልጅ ኃጢአተኛ ነው፤ የጥንተ አብሶ ኃጢአት ከዘር ጋር አብሮ እንደሚወረስ "እስመ ናሁ በኃጢአት ተፀነስኩ፤ ወበአመፃ ወለደተኒ እምየ" ብሎ ንጉሥ ዳዊት (መዝ.50:3) አረጋግጦዋል፤ ከውኃና ከመንፈስ የሆነ ዳግም ልደት ያስፈለገውም ከወላጆ በሆነው ልደት ኃጢአት በዘር ስለሚተላለፍ እርሱን ለመደምሰስ ነው የሚሉ ምክንያቶችን በማቅረብ የጥንተ አብሶ ኃጢአት በዘር ይተላለፋል ሲሉ ከኤርትራውያን ወንድሞቻችን ለየት ያለ ትንታኔ ያቀርባሉ።[31] ሊቀ ጉባኤ አበራ በቀለ በተመሳሳይ "የመጀመሪያው ሰው አዳም የፈጸመው በደልና የደረሰበት መርገም ሁለቱም አይለያዩም። ሁለቱም ወደ አዳም ዝርያዎች ከትውልድ ወደ ትውልድ ተላለፈዋል፤" ይላሉ ሮሜ.5:19 ላይ በመመሥረትና የቢላግዮስን ኑፋቄ በማስታወስ።[32] ርእሱን በሚመለከት የእኔ ልብ ወዲያ ነው፤ ወደ ኤርትራውያኑ ያደላል! አቋሜን ለመታረም ዝግጁ በሆነ ልባዊ መንፈስ ለብቻ አቀርባለሁ። ከዚያ በፊት ግን ቢላግዮስ የሚባል መነኩሴ ከጥንተ አብሶ ጋር በተያያዘ ስሙ ስለሚጠራ አስተሳሰቡን በጥቂቱ እንዳስሰዋለን።

(2.3.9) ቢላግዮስ በ405 ዓ.ም. በብሪታንያ (አየርላንድ) ተወልዶ በክርስትና ሕይወቱ ለመዓርገ ምንኵስና የበቃ ሰው ነበር። ይህ መነኩስ ከጥንተ አብሶ ጋር በተያያዘ "አዳም ባይበድልም መሞት ነበረበት፤ የአዳም በደል የጎዳው ራሱን ብቻ ነው ወደ ዘሮቹ አልተላለፈም፤ ስለዚህም ሕፃናት በሚወለዱበት ጊዜ አዳም ከመውደቁ በፊት እንደ ነበረው ንጹሐ ጠባይዕ ሳያድፍባቸው ይወለዳሉ። የሰው ዘር በራሱ ሥራ እንጂ በአዳም በደል አልሞተም፤ አይሞትምም። በክርስቶስ መነሣትም አይነሣም። ... ክርስቶስም ሳይመጣ ሰው ያለኃጢአት ሊኖር ይችል ነበር ..." የሚል ኑፋቄ አመጣ።[33] ይህ ኑፋቄው የተከበረውን የድኅነት (የመዳን) ምሥጢር ዋጋ የሚያሳጣ፤ የክርስቶስን ደም ክብር የሚቀንስና ከቅዱሳት መጻሕፍትም መዝ. 50:3ን፤

[31] አባ መልከጼዴቅ፡ ገ.142-143
[32] ሊቀ ጉባኤ አበራ በቀለ፡ ገ.90
[33] አባ ጎርጎርዮስ፤ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ ገ.145። ዓሥራት ገ/ማርያም፡ገ.79



ሮሜ.5:12 እና "በአዳም ምክንያት ሰው ሁሉ እንደሚሞት እንዲሁም በክርስቶስ ምክንያት ሰው ሁሉ ሕይወትን ያገኛል፤" የሚለውን የ1ኛ ቆሮ 15:21 ንባብ ይጣረሳል ተብሎ ቀደም ሲል በሮም በኋላም በ430 ዓ.ም. በተደረገው የኤፌሶን ጉባኤ ተወግዟል።[34]

## 2.4. እውነት ግን፡- በጥንተ አብሶ የሚተላለፈው መርገምና ፍዳ ብቻ ወይስ ኃጢአቱም ጭምር? ልቤ የተከፈለበት ጥያቄ

(2.4.1) ሥጋ ለባሽ ሁሉ ኃጢአትን ሠርቷል፤ አንድም ጻድቅ የለም ለማለት የሚቀርቡ ጥቅሶች ብዙ ናቸው። ተዘውትረው የሚጠቀሱትን ሦስቱን ይዘን ገሏቸንን እንቀጥል። (1) መዝ.13:1 እና ሮሜ.3:11 "ጻድቅ የለም፤ አንድ ስንኳ አስተዋይ የለም፤ እግዚአብሔርንም የሚፈሉ የለም፤ ሁሉም ተሳስተዋል።" (2) ሮሜ.5:12 "ኃጢአት በአንድ ሰው ወደ ዓለም ገባ፡" (3) እዮ.15:14 "ንጹሕ ይሆን ዘንድ ሰው ምንድን ነው? ጻድቅስ ይሆን ዘንድ ከሴት የተወለደ ምንድር ነው?" የሚሉትን መረጥን።

(2.4.2) የመዝ.13:1 እና ሮሜ.3:11 "ሁሉም ተያይዞ ስለ በደለ አንድ ስንኳ ፈሪሃ እግዚአብሔር ያለው ሰው እንደ ታጣ የሚያመለክት ጥቅስ በአበው ሲብራራ፤ "ከበዛ ዘንድ 'ሁሉ'፤ ካነሰ ዘንድ 'አልቦ' [ምንም የለም] ማለት ልማድ ነው፤ ወበውስተ ውጉድኒ ንብል አልቦ [መጠኑ እጅግ ሲያንስ የለም እንላለን] እንዲል ዮሐንስ አፈወርቅ" በማለት "ሁሉም" የሚለው ገለጻ በደለኞች መብዛታቸውን፤ ጽድቅ የሚሠሩት ማነሳቸውን ከማሳየት በቀር ጭራሽ ፈሪሐ እግዚአብሔር የነበራቸው ሰዎች አልነበሩም ለማለት እንዳልተጻፈ ያብራሩልናል።[35] ከኒቅያና ድኅረ-ኒቅያ አበቶች ጋር ተጠርቶ የደረሰን የቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ የሮሜ.5:12 ትርጓሜ፡- "But what means, 'for that all have sinned?' This, he having once fallen, even they that had not eaten of the tree did from him, all of them, become mortal — 'ሁሉ ኃጢአትን ስላደረጉ' ማለት ምን ማለት ነው? እርሱ (አዳም) ከክብሩ ሲወርድ ዕፀ በለሷን ያልቀመሱ ልጆቹ ሁሉ

[34] ከላይ የተጠቀሱት ምንጮች፡ገ.146 እና 79
[35] ቅዱስ ጳውሎስ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.40

በእርሱ የተነሣ ድቀት አገኛቸው፤ መዋቲ(ያን) ሆኑ፤" ይላል።[36] የአዳም ተሳትፎ በድርጊቱም በሞቱም ነው፤ የልጆቹ ግን በድርጊቱ ሱታፌ ኖራቸው አልኖራቸው የሞት መርገም አይቀርላቸውም።

(2.4.3) የኢዮብ 15:14'ን ከሴት የተወለደ ሁሉ ንጹሕ ሲሆን እንደማይችል የሚያትት ድንጋጌ እንዲሁ በዘመን አራት ኃጢአተኝነት መንገሡን እና የፈጣሪ ጸጋ ከሰው ልጆች መጓደሉን ለማሳየት ካልሆነ በቀር በአንጻራዊ እይታ ለምልክት የሚሆኑ የቅድስና ሥራዎች አልተሠሩም፣ ጻድቃንም አልነበሩም ለማለት እንደ ተነገረ አድርጎ መውሰድ አስቸጋሪ ይሆናል። ምክንያቱም፦ (1) መጽሐፈ ኢዮብ ራሱ ሲጀምር፣ "ዖፅ በምትባል አገር ስሙ ኢዮብ የተባለ አንድ ሰው ነበረ፤ ያም ሰው ፍጹምና ቅን፣ እግዚአብሔርን የሚፈራ ከክፋትም የራቀ ነበር፤" በማለት ከሴት የተወለደውን ኢዮብ በማወደስ ነው። (2) ኢዮብ 15:14 ላይ ያለውን ቃል የተናገረው ጻድቁ ኢዮብ ሳይሆን ቴማናዊው ኤልፋዝ ነበር። ይህ ጅምላ ንግግሩ ኢዮብን ለመተቸትና መከራው የመጣበህ በኃጢአትህ ነው ለማለት የተነገረ ስለ ነበረ እግዚአብሔር በኤልፋዝ ላይ ቁጣው ነዶ በኢዮብ አማላጅነት ከቁጣው ማምለጡን በመጽሐፉ መጨረሻ እናነባለን (ኢዮ.42:7)። (3) ከኢዮብ በተጨማሪ አቤል (ዕብ.11:4)፣ ኖኅ (ዘፍ.6:9)፣ አብርሃምና ሣራ (ዘፍ.20:1-18)፣ ዘካርያስና ኤልሳቤጥ (ሉቃ.1:6) የመሳሰሉ አበው ወእመው በዚያ "ሁሉም በደለ" በሚባልበት ዘመን ቅዱስ/ ቅድስት ተብለው በቅድስና ሲጠሩ እናያለን። (4) ሊቃውንት እንደሚሉት "ከቶ እና አካቶ" ማለትም ያለምንም ልዩ ሁኔታ (exception) ከሴት የተወለደ ሁሉ ከኃጢአት እንደማይነጻ አድርገን በቴማናዊው ኤልፋዝ የተነገረውን የኢዮብ 15:14 ጥቅስ በቁሙ (እንደ ወረደ) ከወሰድነው ለስሙ አጠራሩ ክብር ይግባውና "ዘመኑ በደረሰ ጊዜ ከሴት ተወለደ" የተባለውን ጌታም ከኃጢአተኞች ጋር የመደመር ኑፋቄ ውስጥ እንገባለን (ገላ.4:4)።

(2.4.4) "ኃጢአት በአንድ ሰው ወደ ዓለም ገባ፤ በኃጢአትም ሞት፤ እንደዚሁም ሁሉ ኃጢአትን ስላደረጉ ሞት ለሰው ሁሉ ደረሰ፤" በሚለው

[36] The Nicene and Post - Nicene Fathers of the Christian Church, Chrysostoms, Homily 10 on Romans



(ሮሜ.5:12 ጥቅስ ውስጥ ያለችው በአንድ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ሦስት ጊዜ ተደጋግማ የተጠቀሰች "ኃጢአት" የምትል ቃል እንደየአገባቧ እየተፈለጠች ብትተረጎም አይከፋም። (1) "ኃጢአት በአንድ ሰው ወደ ዓለም ገባ፤" የምትለዋ፦ አዳም የተሰጠውን ሕግ ተላልፎ የተከለከለውን ዕፀ የመብላት ድርጊት ነው የምታሳየው። የአዳምን የአፍታ ደረቅ ወንጀል - actual sin /personal/ guilt - ብቻ ትመለከታለች። (2) "በኃጢአትም ሞት" መባሉ፦ የመጣውን ርግማን/ ፍዳ ያመለክታል። (3) "እንደዚሁ ሁሉ ኃጢአትን ስላደረጉ ሞት ለሰው ሁሉ ደረሰ፤" መባሉ፦ በአዳም ርግማን የተነሣ ሁላችን ከጸጋ መራቃችንን፣ ከጸጋ በመራቆታችን መበደላችንን፣ ይህም በደል ባመጣው ጉድለት ለኃጢአት ያለን ተጋላጭነት በርክቶ ሞትና ኃሳር እንደ ፀናብን ያሳያል። ዕፀ በለስን መቁረጥ የአዳምና የሔዋን የብቻቸው ድርጊት ናት። በሏት። ጸጋቸው ተገፈፈ። ተፈረደባቸው። የሞት ፍርዱ ግን በዘራቸው ላይ ሁሉ ጸና። ኃጢአቱ የግላቸው፤ ቅጣቱ ግን የጋራ! ሊቃውንቱም "አዳም ሆይ የሞት ፍርድን ያመጣህብን ምን አደረግንህ? ... ሔዋን ሆይ ምን አደረግንሽ?" እያሉ በፀፀት ይተክዛሉ።[37]

(2.4.5) ቅጣቱ የባሕርይ መዛባት አመጣ። ከአዳምና ሔዋን የተወለደ ሁሉ ባሕርዩ ወደ ኃጢአት አዘነበለ፣ አካሉ ማኅደረ መንፈስ ቅዱስ ከመሆን ራቀ፣ ከእግዚአብሔር ፈቃድ ይልቅ የራሱን ፈቃድ የሚፈጽም ሆነ። ይኸውም የኃጢአቱ ውጤትና ተከታይ ነበር። በአዳም በደል ሁሉ በደለኛ ተባለ፤ ተቀጣ።"[38] ከላይ ያለው እንዳለ ሆኖ አዳምና ሔዋን ሲበድሉ በእነርሱ ወገብ ዘራችን ስለ ነበር እና እንዲሁም እነርሱ የሰው ዘር ሁሉ ወኪል ስለ ሆኑ በደላቸው በደላችን ነው፤ ምክንያቱም በዕብራውያን 7:4-9 እንደ ሰፈረው አብርሃም ለመልከ ጼዴቅ የሰጠው ዓሥራት ከትውልድ መተላለፍና ከዓመታት መቈጠር በኋላ ለተነሣው የልጅ-ልጅ-ልጁ ሌዊ "በአብርሃም ወገብ ስለ ነበረ" ተብሎ የአብርሃም ዓሥራት ለሌዊ ተቈጥሮለታል። በዚህ አንጻር ጻድቁ በዘር መተላለፉ ተጠቅሶ ከተቈጠረ በአዳም ወገብ ለነበርነው ለእኛ የአዳም ኃጢአት በዘር ተላልፎ ይቈጠርብናል፤ አትናቴዎስም ከፀፀቱ ብዛት ወደ መደምደሚያው ሲመለስ አዳምንና ሔዋንን "እናንተ እኛን ናችሁ፤ እኛም

[37] ቅዳሴ አትናቴዎስ ቍጥር 28፡ገ.255
[38] አባ መልከጼዴቅ፡ገ.142

እናንተን ነን!" ብሎ ባሕርያቸው ባሕርያችን መሆኑን ስላመላከተ መርገሙ ብቻ ሳይሆን ኃጢአቱም ተላልፎብናል የሚል ክርክር ሊቀርብ ይችላል።[39] ይችላል! በዚህ ርእስ ገና ልቤ አልፀናልኝም። ከተሳሳትኩ ለመታረም ፍጹም ዝግጁ በሆነ ልብ "ሰው በጥንተ አብሶ የተነሣ በርግማን ሥር ሆኖ፣ ጸጋ ጎድሎት፣ ባሕርዩ ለኃጢአት ተጋላጭ ሆኖ (ኃጢአተኛ ሆኖ አላልኩም) ይወለድ ነበር!" ወደሚለው አስተሳሰብ ማዘንበሌን ብቻ ደጋግሜ ልናገር።

(2.4.6) የበለጠ ለማብራራት፥ የሰው ልጅ ከአዳም እና ሔዋን ስለ ተገኘ በርግማን ሥር ሆኖ ስለ ተወለደ ብቻ በተፈጥሮው ነጻ ፈቃዱ ተነጥቆ ይወለዳል እያልኩ አይደለም። እርግጥ ነው የጸጋ መጓደሉንና የእርሱ ውጤት የሆነው ወደ ኃጢአት ማዘንበል (nature /state/ of sin) የወለደውን ሞት የግድ ይወርሳል። ነገር ግን በሰው ዘርነቱ በመርገምና በሞት ጥላ ስር መወለዱ እንደ ተጠበቀ ሆኖ በግላዊ ኑሮው በግዳጅ ኃጢአተኛ አይሆንም። በአንዲት አገር ላይ ማዕቀብ የሚጣለው ሁሉም ዜጋ ስለ በደለ አይደለም፤ በደለኛው ቢበዛ አንድ ፓርቲ ወይም መሪ ነው፤ ሆኖም መሪው የአገር ወኪል ነውና በእርሱ ያልተገባ አካሔድ የመጣው ማዕቀብ ጉዳቱ ለዜጎች ሁሉ ይተርፋል። የጥንተ አብሶ ትረካም እንዲያ ነው። ጸጋን የመግፈፍ ማዕቀብ ከፈጣሪያችን የተጣለብን በአዳም ያልተገባ ድርጊት (የመጀመሪያ በደል) ነው፤ እኛ አልበደልንም፤ ነገር ግን ማዕቀብ የተባለው አዳምና ሔዋን ላይ የተጣለ ፍዳና መርገም ይፈጸምብናል። ለአንድ ዜጋ የማዕቀቡ ሰለባ ለመሆን ማዕቀብ በተጣለባት አገር መኖር እንጂ የመሪውን ድርጊት መደገፍ ወይም አለመደገፍ የሚያመጣው ለውጥ የለም። "ኃጢአትን ባልሠሩት ላይ እንኳ ከአዳም ጀምሮ እስከ ሙሴ ድረስ ሞት ነገሠ፤" የሚለው ለዚህ ነው (ሮሜ.12፡14)። "ኃጢአትን ባልሠሩት ላይ እንኳ" የሚለው የሐዋርያው ጳውሎስ ቃል ኃጢአትን አለመሥራት እንደሚቻል፤ ነገር ግን ኃጢአት አለመሥራት ሳለመሞት ዋስትና እንዳልሆነ ያሳያል። ለዚህ ነው "የአዳም መርገምና ፍዳ እንጂ ኃጢአቱ አይደለም የሚተላለፍብን፤" የሚለው ከወደ ኤርትራ ያነበብኩት ኦርቶዶክሳዊ ክሽን ጽሑፍ ለልቤ የሚስማማኝ። የአዳም ልጆች እስከ እግዚአብሔር ወልድ ሥጋ መልበስ ድረስ ወደ ኃጢአት ቁልቁለት በመንደርደር የፈቃደ ሥጋቸው ተገዥ ቢሆኑም የተፈጥሮ ግዕዛናቸው (ነጻ

[39] ቅዳሴ አትናቴዎስ፡ ገ.255



ፈቃዳቸው) ግን ስላልተነጠቀ በጎውን ከክፋው አመዛዝኖ የመምረጥ መብት አልተወሰደባቸውም።[40] ሊቁ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ አዳም ላይ ትካቱ በጸጋም ማስተዋል ችሎታው አለመገፈፉን ለመግለጽ፦ "የእግዚአብሔርን ትእዛዝ በተላለፈ ጊዜ የብርሃን ግምጃ ተለየው፤ የሕይወት መንፈስ እና ያለበት ልቡናው ግን አልተለየውም፤" ማለቱ ለዚህ ነው።[41]

(2.4.7) ዮሐንስ ዘእስክንድርያ የተባለው አባት ከላይ ያለውን ጽንሰ አሳብ ሰሎሞንን ዋቢ አድርጎ በውብ ቋንቋ ይገልጽልናል። እንደማመንም ሰሎሞን 'እግዚአብሔር ሰውን ዐዋቂ አድርጎ፣ ባሕርዩም ሁሉን የሚችል አድርጎ ፈጠረው' ብሎ እንደ ተናገረ ከእግዚአብሔር የሚገኙ ጸጋና ረድኤት መንገዱን እየመሩት በድካም ትሩፋት ይሠራ ዘንድ እንዲቻለው በራሱ ብቻ ሥልጣን እንዳለው ተናገረ (ጥበ.2፡23)። ኃጢአት የማይስማማው አይደለም፤ ነገር ግን በግዴታ አይደለም፥ ትሩፋትን ቻል በምትል ሕሊና ነው እንጂ። ማንም ማን ኃጢአት የሌለበት ባይሆን ኃጢአትን ለመሥራት ባሕርይ የሚለውጥ አይደለም፤ አስቀድመን እንደ ተናገርን ኃጢአት የሕሊና እንጂ የባሕርይ ናት ልትባል አይገባም። ለውጥ ያለኃጢአት ሊኖር አይችልም፤ ይልቁንም ከሐልዮ ኃጢአት የሚነጻ የለም፤ የሰው ሕሊና ከተወለደበት ቀን ጀምሮ እስከሚሞትበት ቀን ድረስ ሲወጣ ሲወርድ ይኖራልና። ሮሜ.8፡6-9፣ ያዕ.1፡13-17።" ይለናል።[42] ከዚህ ምንባብ ውስጥ "ኃጢአት የሕሊና እንጂ የባሕርይ አይደለችም፤" የምትለዋ ልዩ ኃይለ ቃል ሰዎች ሁሉ ኃጢአተኛ እንደ ሆኑ ቢገለጽም ነገር ግን ኃጢአት በተፈጥሮ (በባሕርይ - /inherently/ inborn) ከወላጅ ወደ ልጅ እንደማይተላለፍ በነጸብራቅ ትጠቁመናለች። ስለዚህ ፍዳውን እንጅ ኃጢአቱን የአዳም ልጆች አልወረሱም። የመምረጥ መብት ቢኖራቸውም ፈቃዳቸው ወደ ገቢረ ኃጢአት ማዘንበሉ ግን እውነት ነው፤ "ፈቂደ ገቢረ ሠናይሰ ሀሎ ኀቤየ፣ ወምግባረ ሠናይሰ አልብየ ... ፈቃድ አለኝ፣ መልካሙን ግን ማድረግ አልችልም፤" እንዲል ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ (ሮሜ.7፡18)።

[40] አቡነ ጎርጎርዮስ፣ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ፡ ገ.101
[41] መጽሐፈ ምሥጢር፡ ገ.184
[42] ሃይማኖተ አበው ዘዮሐንስ፡ ገ.168-169

(2.4.8) የአገራችን ሊቃውንት ገለጻ ድምጸት እንዲሁ በብዛት መርገሙንና ፍዳውን ብቻ እንደ ወረስን የሚያመላክት ሆኖ ይሰሰማኛል። ለአብነት አባ ጎርጎርዮስ የአዳምን ኃጢአትና የልጆቹን የመርገም ወራሽነት ሲገልጹ፡ "ሰውም በንጹሐ ስለ ባለገ በሞት ቀጣው፣ በእርሱም ምክንያት ልጆቹ ከአባታቸው መርገምን ወረሱ ኑሮአቸውም እንደ አባታቸው በምድረ ፋይድ ሆነ!" ይላሉ።[43] አባታችን ውርስ የሚሉት ከኃጢአቱ ይልቅ መርገሙን አጉልተው ነው! በሰንበት ውዳሴ ማርያም ትርጓሜ፡- "ጌታችን ከእመቤታችን ሰው ከሆነ በኋላ ፍዳ የማይተላለፍ ሆኑዋልና። ከዚህ አስቀድሞ ይተላለፍ ነበር? ቢሉ አዎን መስሎ ቢሠራው። ዛሬ ግን ቢሠራው ቅሉ በገዚሐ የሚሠረይ ሆኗልና፣" የሚል ትርጓሜ አለ።[44] ይህም እስከ ጌታ እንበለ ዘርዕ ሰው መሆን ድረስ ፍዳ በሰው ሁሉ ይደርስ እንደ ነበር ያሳያል።[45] እዚህ ላይ "ፍዳ" የሚለው ቃል "ፍርድ" በሚለው ቀጥተኛ ትርጓሜው ሳይሆን "ኃጢአት" ለማለት የገባ ነው። መጻሕፍቱ ፍዳን፣ ኃጢአትን፣ አበሳንና መርገምን እያቀላቀሉ መጠቀማቸው የተለመደ ነው። ለምሳሌ፡- በቅዳሴ ዲዮስቆሮስ ትርጓሜ ውስጥ "ኢትዝክር ለነ <u>አበሳነ ዘትካት</u>" የሚለው ንባብ "<u>የቀደመ ኃጢአታችንን</u>፣ አንድም <u>የአዳምን ኃጢአት</u> [ጥንተ አብሶ] አትዘክርብን። <u>...ፍዳ ይወርዳል የሚሉ ስሑታን አሉና 'አበሳነ ዘትካት' አለባቸው</u>!" ሲል ያብራራዋል።[46] በዚህ ትርጓሜ "አበሳ" የሚለው የግእዝ ቃል፡- ፍዳ፣ ኃጢአት እንዲሁም በቁም አበሳ ተብሎ መተርጎሙን መረዳት ይቻላል፣ አባቶቻችን ኃጢአት ይወርዳል ብለው እንደማያምኑም እንዲሁ። በሥርዓተ ቅዳሴያችን ያለው አመክንዮ ዘሐዋርያትም "ኃጢአት ለነፍስ የባሕርይዋ ናት!" ለሚሉ ሰዎች ምላሽ ለመስጠት ባሰፈረው ቃል "ወመንፈስሰ ሕይወተ ሥጋ ይእቲ፣ ንጽሕት ወቅድስት በኵሉ - የሥጋ ሕይወት የምትሆን ነፍስ ንጽሕት ክብርት ናት፣" ይላል።[47] የአባቶች አቋም በአንዱ በደል ሁላችን ተገረፍን የሚል ሆኖ ይሰማኛል፣ "ኵነኔ ኃጢአት

[43] አባ ጎርጎርዮስ፡ ገ.49
[44] ውዳሴ ማርያም፣ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.119
[45] የእመቤታችንን ንጽሕን ለመግለጽ አበው በተደጋጋሚ "መርገመ ሥጋ፣ መርገመ ነፍስ የሌለባት" ማለታቸውም የትውፊታችንን ጥንተ አብሶን ከተላላፊነቱ ኃጢአትነቱ ይልቅ መርገምነቱን አጉልቶ መመልከት ያሳያል።
[46] መጽሐፈ ቅዳሴ፣ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.453
[47] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.105



አምኃለለ አሐዱ ብእሲ ወጸአ ዙሉ ተቀበሬ ባቲ - የኃጢአት ፍርድ ከአንድ ግለሰብ ወጥታ ሁሉ ተቀጣባት" እንዲል የትምህርተ ኅቡዐት ትርጓሜ።[48]

(2.4.9) ታዲያ "በአንዱ ሰው አለመታዘዝ ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደ ሆኑ..." የሚል የሮሜ.5:19 እንዴት ይታያል? ይባል ይሆናል። ሊቀ ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ ይህን ንባብ በሚመለከት እርሱም ጥያቄ አንሥቶ የራሱን ትርጓሜ ያስቀምጣል። አብረን እናንብበው። "For as by one man's disobedience many were made sinners, so by the obedience of One shall many be made righteous. But how would it follow that from his disobedience another would become a sinner? For at this rate a man of this sort will not even deserve punishment, if, that is, it was not from his own self that he became a sinner. What then does the word sinners mean here? To me it seems to mean <u>liable to punishment and condemned to death</u>. <u>Now that by Adam's death we all became mortals</u> - በአንዱ ሰው አለመታዘዝ ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደ ሆኑ እንዲሁ ደግሞ በአንዱ መታዘዝ ብዙዎች ጻድቃን ይሆናሉ። ግን እንዴት በአንዱ አለመታዘዝ ሌላው ኃጢአተኛ ይሆናል? እንዲያ ከሆነ በዚህ ጉዳይ ማንም ሰው እንኳ ኃጢአተኛ ሊሰኝ ቅጣትም (ፍዳ) አይገባውም። ለእኔ እንደሚመስለኝ ይህ [በአንዱ ሰው አለመታዘዝ ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደሆኑ] ማለት <u>ለቅጣት የተገባ ሆነ፣ ለሞት ተላልፎ ተሰጠ ማለት ነው</u>። <u>በአዳም ሞት ሁላችን ሟቾች ሆነን</u>"[49] የቅዱስ ዮሐንስ ትርጓሜ "ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደሆኑ - For as by one man's disobedience many were made sinners." የሚለውን ኃይለ ቃል ለፍዳውና ለሞቱ ሰጥቶ ነው የተረጎመው። ከአዳም ቅጣቱንና ሞቱን እንጂ ኃጢአቱን እንወርሳለን ማለት አይደለም፣ የክርስቶስን ስቅለት ሳንጋራ ጸጋውን በቸርነቱ እንደምንጋራው መሆኑ ነው። ንጽጽሩም እንዲያ ነው። አዳምና ክርስቶስ፣ መርገምና ጸጋ፣ ሞትና ሕይወት በከፋና በጎ አንጻር

[48] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.6
[49] የሮሜ መልእክት ትርጓሜ በቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ፡ ገ.123 http://www.documentacatholicaomnia.eu/03d/0345-0407,_Iohannes_Chrysostomus,_Homilies_on_The_Epistle_To_The_Romans,_EN.pdf ወይም http://www.newadvent.org/fathers/210210.htm

ይነጻጸራሉ። በአዳም መርገምና ሞት መጣብን። በክርስቶስ ጸጋና ሕይወት አገኘን።

(2.4.10) አሁንም ሌላ ጥያቄ እንሰንዝር! ታዲያ በአራቱ ዘመን የሰው ልጅ በቀቢጸ ተስፋ ውስጥ ለጥሞ እንዳይቀር የተስፋ ፋና ሲያበሩ የነበሩ ቅዱሳን አበው ዕጣ ፈንታ እስከ ጊዜው ምን ነበር? መልሳችን ይኼ ነው፡- በቀደመው ዘመን በቅድስና የተጠሩ ደጋግ አበው መኖራቸው እውነት ነው። ሆኖም ደግነታቸው በሱራፌ የምትጠበቀውን የገነት በር ለማስከፈት የሚችል አልሆነም (ዘፍ.3፡24)፤ ማንም ማን ነፍሱን ከሲኦል እጅ የሚያድን አልነበረምና (መዝ.88፡48)። "ያን ጊዜ፣ በዚያ ወራት፣ ነፍሳት ከሥጋቸው በተለዩ ጊዜ ከምድር በታች ወደ ሲዖል ይወርዱ ነበር፤ የሞት ቤቶችም እስኪሞሉ ድረስ ወደ ገሃነም ይወርዱ ነበር።"[50] የበደለና ያልበደለ ሳይባል ሁሉም በሞት ተገዛ፤ ወደ ሲዖል ተጋዘ። (ሮሜ.5፡14)።[51] እንዲያም ሆኖ ታዲያ እነዚህ ደጋግ አበው ከመከራ እንዴት እንደ ተሰወሩ በካቶሊካውያንና በእኛ ቤተ ክርስቲያን ቀኖና ከቅዱሳት መጻሕፍት የሆነው ጥበበ ሰሎሞን (Wisdom) በምዕራፍ 3፡1-3 ሲተርክ "የደጋግ ሰዎች ነፍስ ግን በእግዚአብሔር እጅ ናት፤ የኃጢአተኞች መከራ አላገኛቸውም። ላዋቆች ዐይናች ግን የሞቱ መሰሉ፤ በሞትም ከዚህ ዓለም መውጣታቸው ክፋት እንዳለባቸው ተቈጠረ። ሞታቸውም ጥፋት መሰለ፤ እነርሱ ግን በተድላና ደስታ አሉ፤" በማለት የተላለፈውን ቅጣት ለመፈጸም ሲዖል ቢወርዱም እስራታቸው ጽኑዕ እንዳይሆን ብርቱው የጌታ ክንድ ይጠብቃቸው እንደ ነበር ይገልጻል።

(2.4.11) 'የለም፤ ይህ ከአዋልድ የተገኘ ታሪክ ነው' ብሎ የሚሸፍትና የሚሸፍጥ ካለም በዚያ ጸጋ ጎደለ በተባለበት ዘመን፤ ገና ደመ ክርስቶስ ፈስሶ ሳይቤዠን በንስቁልና የኖረውን ድኻ ነፍስ መላእክት ተቀብለው ወደ አብርሃም ዕቅፍ እንደ ወሰዷት የሚገልጸውን የሉቃስ 16፡22 ታሪክ ማየት ይቻላል። ስለዚህ የገነት እስከ ስቅለተ ክርስቶስ ድረስ ዝግ መሆን የሰው

[50] ሃይማኖተ አበው ዘቄርሎስ፡ ገ.380

[51] ሃይማኖተ አበው ዘአቡሊዲስ፣ ምዕ.42 ቁ.9፣ ገ.145። እንድምታው "ከአዳም በደል ምክንያት ያልበደሉትንም ሁሉ ሞት ገዛቸው" ይላል ። ሊቀ ሊቃውንት ዕዝራ ሐዲስ፣ ሃይማኖተ አበው፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ ጎንደር፣ 2007 ዓ.ም፡ገ.263።



ልጆች ጸጋው ጎድሏቸው ወደ ኃጢአት ማዘንበላቸውን ከማሳየት ውጪ ሙሉ ለሙሉ ደጋግ ሰዎች አልነበሩም፤ ቢኖሩም ዕጣቸው በሲዖል ካሉ በደለኞች ጋር ተቀላቅሎ በእሳት መጠበስ ነበር ብለን አናምንም። "የደጋግ ሰዎች ነፍስ በእግዚአብሔር እጅ ነበረችና መከራ አላገኛትም" እንዳለን እንጂ። "ክቡራት የእግዚአብሔር ጠለ ምሕረቱ እየጠበቃቸው በሲዖል በዕረፍት ስለ መኖራቸው የቃሉ ምስክርነት በሉቃስ ወንጌል (16፡18-30) እንደ ተጻፈ ምስክሩና መታመኛዬ የእግዚአብሔር ልጅ ነው፤" የሚለው የአባ ጊዮርጊስ ቃል ለእኛም ምስክር ይሁን።[52] ተመሳሳይ አቋም በካቶሊካውያንና ስለ መኖሩ ጸሐፎቻቸው ይመሰክራሉ።[53]

## 2.5. ድምሳሴ ጥንተ አብሶ፡- ጌታችን የተሰቀለው ለጥንተ አብሶ ብቻ ወይስ ለምልአተ ኃጢአት (ለእያንዳንዳችን ዕለታዊ ወይም የዘወትር) ኃጢአት ጭምር?

(2.5.1) ጌታችን የተሰቀለው ለጥንተ አብሶ ማለትም ለአዳምና ሔዋን የመጀመሪያ በደል ብቻ አይደለም። በደሉን ተከትሎ በሁላችንም ላይ የመጣውን መርገም ለመሻር፣ ጸጋ ጎድሎት ወደ ኃጢአት ያዘነበለው የሰው ልጅ በነጻ ፈቃዱ በየዕለቱ የሚሠራውን ዘወትራዊ ኃጢአት (ምልአተ ኃጢአት/ actual sin/) ለማስተስረይ፣ በአጠቃላይ የአዳምና የልጆቹን ኃጢአት ከነመርገሙና ፍዳው (ቅጣቱ) ለመደምሰስ ነው። መጻሕፍቶቻችን ስለ ክርስቶስ የማዳን ሥራ ሲተርኩ ጥንተ አብሶን (Original Sin) እና ምልአተ ኃጢአትን (Actual Sin) ለያይተው አይደለም። በደሉን (ኃጢአቱን) ከርግማኑ፣ ርግማኑን ከፍዳው (ከቅጣቱ) ለይቶ እንድነትና ልዩነቱን ከማብራራት ይልቅ ሁሉም ተደማምረው በቀራንዮ መሻራቸው ላይ አጽንዖት መስጠትን ያስቀድማሉ። የቃልና የድርጊት ትንተና ላይ አላተኩም። የአዳም በደል፣ ቅጣትና የምሕረት መዝገብ (ፋይል) ተተንትኖ ቃላትና ድርጊቶች ቢለነጠቁ መረዳታችንን ከፍ ያደርገዋል እንጂ የክርስቶስን ድምሳሴ ኃጢአት ከቶም አያሳንሰውምና ጥቂት እንሒድበት!

[52] መጽሐፈ ምሥጢር፡ ገ.194

[53] http://www.newadvent.org/cathen/09256a.htm

(2.5.2) በኦርቶዶክሳውያን መጻሕፍት[54] እንደ ተጻፈ "ሥርዓተ ሰማይ ተሠርዐ በምድር" በሚል ዐላማ ተነሣስተን የአዳምን ፋይል በአገራችን የሕግ መነጽር ባጭሩ በለዘበ መንፈሳዊ ጨዋታ እናስቀምጠው፦

(1) አዳም "አትብላ" የሚል ሕግ ወጣለት። ይህም በአገራችን የወንጀል ሕግ አንቀጽ 2 "የሕጋዊነት መርሕ/ Principle of Legality" የተባለው ሲሆን ጽንሰ አሳቡ "ሕግ ወንጀል ያላደረገው ሁሉ መብት ነው - No law, No crime" ማለት ነው። ጳውሎስም "ነገር ግን ሕግ በሌለበት መተላለፍ የለም፤" ሲል ቀድሞን ይቆማል (ሮሜ.4፡15)። አዳም የወንጀል ማቋቋሚያ ከሆንችው የተከለከለችውን ፍሬ የመብላት ድርጊት በቀር ሁሉን መብላት መብቱ ነበር።

(2) ሆኖም አዳምና ሔዋን የተጣለባቸውን አደራና ነጻ ፈቃድ ወደ ጎን በማለት ከሕግ ውጭ የፈጣሪያቸውን ዙፋን ለመገልበጥ በማሰብ በግብረ አበርነት የተከለከሉትን ፍሬ ሲመገቡ እጅ ከፍንጅ ተያዙ (ዘፍ. 3፡6)።[55] "አበሳ/ ኃጢአት" = የወንጀል ድርጊት።[56]

(3) አዳምና ሔዋን ድርጊቱን መፈጸማቸውን አልካዱም። ጥፋተኝነትን በሚመለከት ግን አዳም በሔዋን፣ ሔዋን በእባብ ለማሳበብ ሞክረው ነበር። ሆኖም ጌታ አዳምና ሔዋንን ነጻ ፈቃድ እስካላችሁ ድረስ ራሳችሁን በኃላፊነት መጠበቅ ሲገባችሁ ለጥፋት ካጋለጣችሁ በኋላ ሰበብ አትደርድሩ ሲል መከላከያቸውን ለጊዜው ውድቅ አደረገው።[57] እባብም ለእኔ እንደ አዳምና ሔዋን ሕግ ስላልወጣልኝ ከእነርሱ ጋር ተደምሬ ልቀጣ አልገባም ብትልም በሕጉ አንቀጽ 81(1) መሠረት 'ሕግን አለማወቅ ከተጠያቂነት አያድንም፤' ሲል መቃወሚያዋን ውድቅ አደረገው፤ በእንኩትት አስኬዳት። ሁሉም ተረገሙ፤ ጥፋተኛ ተባሉ። "ርግማን" = የጥፋተኝነት ውሳኔ።

(4) ጉዳዩ ለቅጣት ውሳኔ ተላለፈ። በዚህም መሠረት አዳምና ሔዋን ቤታቸው ገነትን እንዲለቁ፣ አዳም የጉልበት ሥራ እንዲሠራ ተወሰነበት፤ ሔዋን እንዲሁ ልጅን በምጥ የመውለድ ቅጣት ተላለፈባት።[58] የቅጣት ውሳኔ = "ፍዳ"። ፍዳው /ቅጣቱ/ በምድር አምሳል ለልጆቻቸው ሁሉ እንዲሆን

[54] አክሲማሮስ ዘረቡዕ, ገ.128
[55] የወንጀል ሕግ አንቀጽ 34፣ 57 እና 238
[56] ኃጢአት የጽድቅ አለመኖር እንጂ ወንጀል እንዳልሆነ ሳንዘነጋ!
[57] የወንጀል ሕግ አንቀጽ 50(2)
[58] የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ ሥነ ሥርዓት አንቀጽ 149(5)



ተወሰነ።[59] ጸጋ የተባለው ከመንፈስ ቅዱስ የሚገኝ ደጎግ ተገፈፈባቸው። የሚገርመው ጌታ ሲቀጣቸው ወንድና ሴት ብሎ አልለየም፤ እኩል ቀጥቶ እኩል ኃላፊነትና ተፈጥሮ እንዳላቸው ነገረን (ዘፍ.3)።[60]

(5) የእስራት ዘመናቸው ማብቂያ ሲደርስ ሰማያዊው ዳኛ ድንግል ማርያምን ዙፋኑ አድርጎ በግዘፍ ተገለጠ። መስቀሉን እስከርቢቶ፣ ደሙን ቀለም፣ ቀራንዮን ደብተር በማድረግ፣ ራሱን ተያዥ አድርጎ የመፈቻ ትእዛዝ /ዋራንት/ ጻፈ። ምሕረት ወረደ። አዳምና ሔዋን በምሕረት ተለቀቁ፤ በዚህም ላይ "ተሰየመ"። ምሕረት ከይቅርታ የሚለው ክሱንም ወንጀሉንም ስለሚያስቀር ነው። "መሠየም" ማለትም ታስሮ ለተፈታ ሰው መልካም ስሙን መመለስ ማለት ነው።[61]

(2.5.3) የጌታ ስቅለት ምሕረት አወረደ ስንል ተከሰውና ተፈርዶባቸው የነበሩት አዳምና ሔዋን ከኃጢአቱ፣ ከፍርዱና ቅጣቱ በነጻ ተሰናበቱ፤ ልጆቻቸው ላይ ሲቀጥል የነበረው ጥንተ አብሶ የተባለው ክስና ፍርድ ተቋረጠ፤ ምልአተ ኃጢአትንም የሚያጠቃልል ጠቅላላ የምሕረት ዐዋጅ ታወጀ፤ ሕጉም የሚሻሻለው ተሻሽሎ፣ የሚሻረው ተሽሮ፣ የሚጸናው ባለበት ፀንቶ ቀጠለ ማለታችን ነው። ታዲያ ይህ በዋጋ የተገዛ ሥርየት የማግኘት መብት እንዲሁ ሳይሆን በእምነት፣ በጥምቀት፣ በቊርባንና በተቀሩት ምሥጢራተ ቤተ ክርስቲያን እንዲሁም በምግባር በመታገዝ የሚፈጸም ነው።[62] ለእኛ የተፈጸመልን የማዳን ሥራ የሚተገበርልን እኛም ራሳችን ለጽድቁ የተገባን የሚያደርገንን ሱታፌ ስናበረክት ነው።

(2.5.4) ወግ ሲበዛ ከነጥባችን እንዳያናጥበን ወደ መጻሕፍቶቻችን እንመለስ። ከዚህ አለው የጌታን ሁለንተናዊ የማዳን ጉዞ ሲገልጹት "...እምላክ ነውና በዚህ ዓለም ኃጢአትን አጠፋ (ማቴ.1፡21)፣ በመስቀልም ተሰቅሎ ፍዳን/ ቅጣትን አጠፋ (1ኛ ጴጥ.2፡24)፣ በመቃብርም ፈርሶ በስብሶ መቅረትን አጠፋ

[59] እዚህ ላይ ከቅጣት አንጻር "crime is personal - የወንጀል ተጠያቂነት ግላዊ ነው" የሚለው መርሕ አይሠራም።
[60] የወንጀል ሕግ አንቀጽ 4 እና የፌደራል ታራሚዎች አያያዝ ደንብ ቁጥር 138/1999 አንቀጽ 3
[61] ስንርጉሩ የወንጀል ሕጉን ከአንቀጽ 229-237 ተመልከት
[62] H. H. POPE SHENOUDA III, SALVATION in the Orthodox Concept, 3rd Print. Oct. 2005; p. 21 — 57

(ሮሜ.6፡5 እና 1ኛ ቆሮ.15፡51-57)፣ ሥራ በሠራበት ሁሉ ድኅነት አደረገልን፤" ይላሉ።[63] ስለ ጥንተ አብሶ በየደረጃው መደምሰስም "...ቢዛችን በሚሆን በልጁ ሕማም ሞት ጠፋ፣ ዲያብሎስም ድል ተነሣ፤ ሲያል ታወከ፤ በኃጢአት የተፈረደውም ፍርድ ተፋቀ፣ ሰይጣን ያመጣው ስሕተት ጠፋ፤ እንዳልነበረም ሆነ፣ ገነት ተከፈተ፣ ትንሣኤ ተገለጠ፤" ይሉናል።[64] እርሱ ሞት የማይገባው ክርስቶስ በሞተ ጊዜ፣ "ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ በቀደመኝ ትእዛዝ ማፍረስ የመጣች ኃጢአትን አጠፋ፤" በማለት ኃጢአቱንም፣ መርገሙንም፣ ፍዳውንም /ቅጣቱንም/ እንዲሁም ጥንተ አብሶንና ምልአተ ኃጢአትን አንድ ላይ ጠቅልለው በክርስቶስ ደም መደምሰሳቸውን ይተርኩልናል።[65] እዚህ ላይ ኃጢአት የሚባለው የቀደመችውን ትእዛዝ ማፍረስ ሆኖ ሳለ በቀደመው ትእዛዝ ማፍረስ ምክንያት የመጣው መርገምና ፍዳም ኃጢአት ተብሎ መቅረቡ (በእኔ ለመታረም ዝግጁ የሆነ ትሑት አተያይ) ሊቃውንት ከቃላትና ድርጊት ትንተና ይልቅ ሙሉ ትኩረታቸው የክርስቶስን ሥጋ ለብሶ ማዳን ማጉላት ላይ መሆኑን ያሳያል።[66]

(2.5.5) የአገራችንን ኦርቶዶክሳውያን ሊቃውንት ስንቃኝ፣ "ዓዕረ ዘሞት ፈትሐ - የሞት ዓዕሩን፣ ዓዕረኛነቱን አሰናበተው፤" የሚለውን የትምህርተ ኅቡዐት ደረቅ ንባብ በትርጓሜ ሲያፍታቱት ጌታ ያለዘርዕ እና ያለሩካቤ ተፀንሶ በመወለድ፣ በገዳመ ቆሮንቶስ በጾምና በጸሎት በሦስቱ አርእስተ ኃጥውዕ (ትዕቢት፣ ስስት፣ ፍቅረ ነዋይ) ድል በመንሳት፣ በሞቱ ጊዜ ነፍሱን በዓዕረ ሞት ሳይሆን በገዛ መለኮታዊ ሥልጣኑ ከሥጋው በመለየት መንገዱን ሁሉ ለውጦ ጠላት ዲያብሎስን እንዳሸነፈው፣ እኛም ከኅኑ በፈሰሰ ማየ ገቦ ተጠምቀን ከፍዳ እንደ ነጻን፣ ከቁራኝነት እንደ ተላቀቅን ይተርካሉ።[67] ከቅርብ ጊዜ ጸሐፍያንም መምህር ኃይለማርያም ላቀው "ክርስቶስ የተሰቀለው በጥንተ

[63] ሃይማኖተ አበው ዘብንያሚ፡ ገ.385
[64] ሃይማኖተ አበው ዘሳዊሮስ፡ ገ.369
[65] ሃይማኖተ አበው ዘቄርሎስ፡ ገ.318
[66] ሁኔታው አባቶቻችን ቃላትን በፍልስፍና ቃና ከመፈላለጥና ከመተንተን ላይ ይልቅ ("ከተረዱና ካወቁ በኋላ ማመን - understand in order to believe" በሚባለው መንገድ ሳይሆን) "ለመረዳትና ለማወቅ አስቀድሞ ማመን - believe in order to understand" በሚለው የእምነት መንገድ እንደሚጓዙም ይጠቁማል።
[67] መልአከ ገነት ዘለዓለም እሰይ፣ የጸሎተ ሃይማኖት ትርጓሜ፡ ገ.79። መልአከ ብርሃን አድማሱ፣ ኩነተ ሃይማኖት፡ ገ.141



አብሶ በመጣው በደል ብቻ ሳይሆን በምልአተ ኃጢአት (እያንዳንዳችን በሠራነው ኃጢአት) ጭምር ነው፤" ሲሉ የቀደምት አበውን ቃል አጽንተዋል።[68]

(2.5.6) ንዑስ ርእሳችን የጥንተ አብሶ ድምሳሴ ነውና ከኢርትራውያኑ ኦርቶዶክሳውያን የጥንተ አብሶን በጌታ ደረጃ በደረጃ የመደምሰስ ትረካ እንዋስ። ወንድሞቻችን ድምሳሴውን ሲተርኩ "በጽንሰቱ ተስፋ ሰጠን፣ በልደቱ የዲያብሎስን ልብ አራደ፣ በጥምቀቱ የአዳምንና የሔዋንን የዕዳ ደብዳቤ ፋቀ፣ በጾሙ አርእስተ ኃጣውዕን አደከመ፤ በተአምራቱ ኃይለ ሰይጣናትን አደከመ፤ በስቃዩ ስቃያችንን አራቀ፤ በሞቱ ሞትን ደመሰሰ፤ በትንሣኤው ትንሣኤ ነፍስን አበሰረ፣ በዕርገቱ ወደ ቀደመ ክብራችን መመለሳችንን አበሰረ፤" በማለት ከላይ በተጠቀሰው የድራማ አድራሻቸው ቁልጭ አድርገው አስቀምጠውታል። ቅዱስ ጳውሎስ በበኩሉ ጠቅለል አድርጎ የጥንተ አብሶን ድምሳሴ ሲገልጸው፡- "በአንድ በደል ምክንያት ፍርድ ለኵነኔ ወደ ሰው ሁሉ መጣ፤ እንዲሁም በአንድ ጽድቅ ምክንያት በጸጋው ሕይወትን ለማጽደቅ ወደ ሰው ሁሉ መጣ። በአንዱ አለመታዘዝ ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደሆኑ እንዲሁ ደግሞ በአንዱ መታዘዝ ብዙዎች ጻድቃን ይሆናሉ፤" ይላል (ሮሜ.5፡18-19)። የአንምድታው ባለቤቶች አባቶቻችን ድምሳሴውን "በአንድ በአዳም በደል ብዙ ሰዎች እንደ ተፈረደባቸው በአንድ በክርስቶስ ትሩፋት ብዙ ሰዎች ይከብራሉ (1ኛ ቆሮ.15፡22)። ... በአንድ በአዳም ትእዛዝ ማፍረስ ብዙ ሰዎች እንደ ተጎዱ በአንድ በክርስቶስ ትእዛዝ መፈጸም ብዙ ሰዎች ይከብራሉ (ኢሳ.53፡11፣ ፊልጵ 2፡9)፤" ሲሉ ውብ ትርጓሜ አኑረውልናል።[69] ሶርያዊው ቅዱስ ኤፍሬምም፡- "ወነስተ ምክሮ ለጸላኢ፤ ... ወሰጠጠ መጽሐፈ ዕዳሆሙ ለአዳም ወለሔዋን፤ ... ወሠዐረ እምኔነ መርገመ ወገብረ ሰላመ ማዕከሌነ፤ ... አግብአ ለብእሲ ዳግመ ውስተ ገነት" በመሳሰሉ ምንባባት የጌታን ጥንተ አብሶንና ምልአተ ኃጢአትን መደምሰስ አስተባብሮ በውዳሴ ማርያም አስፍሮታል። ሊቀ ቅዱስ ያሬድ ይህን ሁሉ የጥቅስ ጓዝ እና "ርግምተ ትኩን ምድር በተግባርከ" ተብሎ

[68] መ/ር ኃይለማርያም ላቀው፣ ሐውልተ ስምዕ፡ ገ.172። የውዳሴ ማርያም አንድምታ ትርጓሜ፡ ገ.25
[69] የቅዱስ ጳውሎስ መጽሐፍ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.53

የመጣ ፍዳ በክርስቶስ ደም መደምሰስ "ወምድርኒ ትገብር ፋሲካ ተሐጺባ በደመ ክርስቶስ" ሲል በአንድ ኅብራዊ ዐረፍተ ነገር ይቋጨዋል። 'የምድር እድፍ በደመ ክርስቶስ ታጠበ፤ ርግማኗ በስቅለቱ ተሸሮ ሐሴት አደረገች' ሲል።

(2.5.7) 'ጥንተ አብሶ ከተደመሰሰ ለምን እንሞታለን?' የሚል ጥያቄ ይነሣል። ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ ይህንኑ ጥያቄ አንሥቶ ሲመልስ "እንደ ቀድሞው እንሞትምን? የሚል ሰው ቢኖር 'አዎ! እንሞታለን፤ ግን ሞት አይሠለጥንብንም፤' ብለን እንመልስለታለን፤" ይላል።[70] በዳግም ምጽአት (በትንሣኤ ዘጉባኤ) በቀኝ እና ግራ ቆመን ለማይድና ምድር እንደ ብራና ሲጠቀለሉ ሞተ ሥጋ ይቆማል። ሐዋርያው ጳውሎስ ይናገር፤ 1ኛ ቆሮ.15፡42-54፡- "የሙታን ትንሣኤ ደግሞ እንዲሁ ነው። በመበስበስ ይዘራል፥ ባለመበስበስ ይነሣል፤ በውርደት ይዘራል፥ በክብር ይነሣል፤ በድካም ይዘራል፥ በኃይል ይነሣል፤ ፍጥረታዊ አካል ይዘራል፥ መንፈሳዊ አካል ይነሣል። ፍጥረታዊ አካል ካለ መንፈሳዊ አካል ደግሞ አለ። እንዲሁ ደግሞ። ፊተኛው ሰው አዳም ሕያው ነፍስ ሆነ ተብሎ ተጽፎአል፤ ኋለኛው አዳም ሕይወትን የሚሰጥ መንፈስ ሆነ።ነገር ግን አስቀድሞ ፍጥረታዊው ቀጥሎም መንፈሳዊው ነው እንጂ መንፈሳዊው መጀመሪያ አይደለም። የፊተኛው ሰው ከመሬት መሬታዊ ነው፤ ሁለተኛው ሰው ከሰማይ ነው። መሬታዊው እንደ ሆነ መሬታውያን የሆኑት ደግሞ እንዲሁ ናቸው፥ ሰማያዊው እንደ ሆነ ሰማያውያን የሆኑት ደግሞ እንዲሁ ናቸው። የዚያንም የመሬታዊውን መልክ እንደ ለበስን የሰማያዊውን መልክ ደግሞ እንለብሳለን። ነገር ግን፥ ወንድሞች ሆይ፥ ይህን እላለሁ። ሥጋና ደም የእግዚአብሔርን መንግሥት ሊወርሱ አይችሉም፥ የሚበሰብሰውም የማይበሰብሰውን አይወርስም። እነሆ፥ አንድ ምሥጢር እነግራችኋለሁ፤ ሁላችን አናንቀላፋም ነገር ግን የኋለኛው መለከት ሲነፋ ሁላችን በድንገት በቅጽበት ዓይን እንለወጣለን፤ መለከት ይነፋልና ሙታንም የማይበሰብሱ ሆነው ይነሣሉ እኛም እንለወጣለን። ይህ የሚበሰብሰው የማይበሰብሰውን ሊለብስ ይህም የሚሞተው የማይሞተውን ሊለብስ ይገባዋልና። ዳሩ ግን ይህ የሚበሰብሰው የማይበሰብሰውን ሲለብስ

[70] ድርሳን ዘዮሐንስ አፈወርቅ፣ ምዕራፍ 17:56-57፡ ገ.304



ይህም የሚሞተው የማይሞተውን ሲለብስ፥ በዚያን ጊዜ። ሞት ድል በመነሣት ተዋጠ ተብሎ የተጻፈው ቃል ይፈጸማል።"

(2.5.8) ቅዱስ አትናቴዎስ ስለ ሞትና ሰው ግንኙነት በጥልቀት ይዳስሳል። እስቲ እናንብበው፡- "ሰው በባሕርዩ መዋቲ ነው፤ ምነው? ቢሉ ካለመኖር (እምኀበ አልቦ) የመጣ ነውና። ነገር ግን የፈጣሪውን አርአያ መልክ ይዞ ተፈጥሯል። ይህን አርአያ መልክ (ቅድስና) ቢያፀና ተፈጥሮአዊ ሞት በእርሱ ላይ ኃይል አይኖረውም፤ ከርኩሰት ርቆ ይኖራል። ከርኩሰት ከራቀ ወዲያ እንደ ፈጣሪው ቅዱስ ይሆናል። ይኸንንም መጽሐፈ ጥበብ 6:18 'ሕጉን መስማት መረዳት ሕይወተ ነፍስ ይሰጣል፤' ሲል ያስረግጣል። ክቡር ዳዊትም በመዝ.81፡6 'እኔ ግን አማልክት ናችሁ፥ ሁላችሁም የልዑል ልጆች ናችሁ አላለሁ' ብሏል...።" "ሆኖም" ይላል አትናቴዎስ "ሆኖም ሰው ሲፈጠር የተሰጠውን ንጽሐ ባሕርይ (ጸጋ) አጉድፎ ክንቱ እና ውዱቅ ከሆኑ ተፈጥሮአዊው ሕገ ሞት ተግባራዊ ይሆንበታል፤ በገነት መኖሩ ይቀራል፤ ከእርሷ ወጥቶ በሞትና በርኩሰት መኖር ይጀምራል። - But if they went astray and became vile, throwing away their birthright of beauty, then they would come under the natural law of death and live no longer in paradise, but, dying outside of it, continue in death and in corruption."

ሞት ትርጓሜው "ከፈጣሪ መለየት" ማለት ነው። ይህ ሞት ሊሸነፍ የሚችለው ሰውና እግዚአብሔር ሲታረቁ ብቻ ነበር። ያን ለማድረግ አምላክ ሰው ሆነ። ተወለደ። አስተማረ። ተሰቀለ። ከሙታን ተነሣ። በአዳም የመጣው ሞትና መቃብር በክርስቶስ ትንሣኤ ተሸነፈ። "ስለሆነም ከክርስቶስ ትንሣኤ ወዲህ ስንሞት በርግማን ለሞት የተሰጠን ሆነን አይደለም፤ በትንሣኤ ሒደት ላይ ሆነን የጌታን ዳግም ምጽአት በተስፋ በመጠባበቅ እንጂ።... Now, therefore, when we die we no longer do so as men condemned to death but as those who are even now in process of rising we await the general resurrection of all" ይላል ታላቁ አባት 1ኛ ቆሮ.15፡21 ላይ ተመሥርቶ።[71] ከአትናቴዎስ ቃል ውስጥ "ሰው በባሕርዩ

[71] http://www.copticchurch.net/topics/theology/incarnation_st_athanasius.pdf

መዋቲ ነው" የሚለው ገለጸ እንጻራዊ እውነታ ነው፤ ሰው በባሕርይው የመምረጥ ዕድል ያለው ፍጡር ነበር። መዋቲና ኢመዋቲ የመሆን ዕድሉ በገዛ እጁ ነበር፤ የጌታን ትእዛዝ ቢያከብር ኖሮ ሕያው ሆኖ በገነት እየታደሰ ይኖራል፤ ካላከበረ ከእርሱ አስቀድሞ በጌታ ሁሉን ዐዋቂነት ጥበብ ወደ ተዘጋጀው ሲዖል ይወርዳል። አላከበረምና ወረደ።

## 2.6. ድምሳሴ ኃጢአትን በሚመለከት "መዳን በማንም የለም" ከተባለ እኛ ኦርቶዶክሳውያን፣ ካቶሊካውያንና የምሥራቅ ግሪክ ኦርቶዶክሶች እመቤታችንንና ሌሎች ቅዱሳንን "አድነኝ/ አድኚኝ" የምንለው ለምንድን ነው? የሚያድኑንስ ከየትኛው ኃጢአት/ ፈተና?

(2.6.1) ንዑስ ርእሳችንን የተሐድሶዎች የመንፈስ አባት ከሆኑት አለቃ ታዬ ገብረ ማርያም አርኬ በትንሹ ቆንጥረን በማቅረብ እንጀምራት፡-

"...በጽድቀ ርእሰክሙ ቀዊመ እለ ትዕሕቁ፣
እምጸጋ መድኃኒት ኀበ ደይን ከመ ኢትደቁ፣
መጻሕፍተ ብሉይ ወሐዲስ በአስተሐይጾ ጠይቁ፣
እንበለ ክርስቶስ በርእሶሙ ከመ ኢድኀኑ በሕቁ፣
አብርሃም በምግባሩ ወኢዮብ በጽድቁ።"[72]

ይህች አርኬ የቅኔን ሰምና ወርቅ ሕግም ሆነ የዜማ ልክ ምጣኔ ድንጋጌዎችን ያልተከተለች ሆና ግን ቤት የምትመታ የግእዝ ስብከታዊ ግጥም ናት። ልናቃልላት ከፈለግን እንዲህ እንበላት፡- ቅኔም አይደለች! ዝም ብላ ወርቅ ናት - ጽድቅ ነገር! ሰም የሌላት ፍጥጥ ያለች ወርቅ - አማን በአማን! ነፍሳቸውን ይማርና የቅኔ መምህራችን በጀማሪነታችን ወቅት ሰም የሌለው ቅኔ ስናቀርብ "እሰይ! እንዲያ ነው! ወርቅ የሆነች ቅኔ!" ይላሉ፤ ወይም

[72] በመንፈስ ቅዱስ አብርሃ በመልአክ ብርሃን አድማሱ እንደ ተጠቀሰው፣ ገ.154



እንዳልሰሙ ሆነው "አማን በአማን፣ አማን በአማን..." እያሉ ያዜማሉ። ታዲያ የጀማሪ ልባችን በሐሴት ትዘላለች። ሰም ያልለበሰ፣ ዜማ ያልጠበቀ፣ ፈት ታሪክና ምሥጢር ያልጠነቀቀ ቃል ተገጣጥሞ ቤት ስለ መታ ብቻ ቅኔ እንደማይባል ዘግይቶ ገባን። ሲገባን በራሳችን ሳቅን። ዕድለኞች ነበርን - ስሕተታችንን ዐውቀን ለመሳቅ ስለ ታደልን። የአለቃ ታዬ አርኬም ወርቅ ናት! ሰም የላት፣ ዜማ አትጠብቅ፣ በየትኛውም የቅኔ መደብ አትመደብ! በዚህ ላይ ጥንተ አብሶንና ምልአተ ኃጢአትን ቀላቅላ ነው የምትቀማጠል! አለቃ ታዬ እንኳ በኑፋቄ እንጂ በቅኔ ዕውቀት የሚታሙ አልነበሩም፤ ለቀሊላን ደቀ መዛሙርቶቻቸው ለማቅለል ሲሉ ነው ነገሩን ቀልለው ያቀለሉት! የቀሊሏ አርኬ ትርጉሟ ባጭሩ፡- "በራሳችሁ ሥራ (ጽድቅ/ እውነት/) ለመቆም የምትደክሙ፣ መድኃኒት ከሚሆን ጸጋ ወደ ደይን እንዳትወድቁ፣ የብሉይና የሐዲስ መጻሕፍትን በማመሳከር (በማመላከት) ከክርስቶስ በቀር (በእርሱ ከማመን ውጪ) አብርሃም በምግባሩ ኢዮብ በጽድቁ በፍጹም እንዳልዳኑ ተረዱ፤" ትላለች። መልእክቷ የተለመደው የተሐድሶዎች ፕሮቴስታንታዊ ጠባብ የነገረ ድኅነት ትርጓሜ ቅኝት ነው። "መዳን በእምነት ብቻ!" እና "አማላጅ ራሱ ጌታ ስለ ሆነ ሌላ አማላጅ አያስፈልግም!" የሚል ተደጋጋሚ ቅኝት። ወርቂቷን አርኬ እንሒድባት!

(2.6.2) አርኬው ውስጥ የማይካዱ ሁለት እውነቶች አሉ። የአብርሃም ምግባርና የኢዮብ ጻድቅነት የተመሰከረ ነው። እንዲሁም የሁለቱም ማለትም የአብርሃም ምግባርም ሆነ የኢዮብ ጽድቅ ጥንተ አብሶን ለመደምሰስ አለመቻላቸውም እውነት ነው። ምክንያቱም እነርሱ በነበሩበት ዘመን የሰው ልጅ በሠዋው መሥዋዕት፣ በጸለየው ጸሎት፣ ባጠነው ዕጣን፣ ባቀረበው ቁርባን ከዲያብሎስ ባርነት ሊወጣ የማይችልበት ዓመተ ፍዳ ዓመተ ኩነኔ ነበር።[73] ከዚህ ጥንተ አብሶ የነገሠበት ዘመን ለመውጣት በአማላጅ ወይም በፍጡር መሥዋዕት የሚሆን አልነበረም። "... ሰው ሆኖ ያድነን ዘንድ እርሱ ራሱ እግዚአብሔር ነው እንጂ አማላጅ ወይም መልአክ አይደለም፤ በባዕድ ደም በዕሩቅ ብእሲ [መለኮታዊ ባሕርይ በሌለው ሥጋ ለባሽ ሰው] ሞት አላዳነንም፤ እርሱ ራሱ በደሙ አዳነን እንጂ፤ የሌላ ደም አይደለም፤"

[73] መልአክ ብርሃን አድማሱ፣ ኩኩሐ ሃይማኖት፣ ገ.137

እንዲል።[74] ስለዚህ ጥንተ አብሶን በሚመለከት አብርሃምና ኢዮብ ለራሳቸውም በጽድቃቸውና በምግባራቸው የገነትን በር ለማስከፈት አቅቷቸው በሲዖል ካለች መከራ በእግዚአብሔር እጅ እየተጠበቁ የመሲሑን መምጣት የሚናፍቁ ምስኪናን ነበሩ - እንኳንስ ለሌላው ሊተርፉ። መልአከ ብርሃን እንዳሉት "አብርሃም በምግባሩ ወኢዮብ በጽድቁ" እንዲልጸደቁ የተነገረው ለዚያ ዘመን ነው፤ ትረካውም "በኦሪት የነበረውን ፍዳ መርገም የሚተርክ እንጂ ዛሬ በክርስቶስ ደም የቀረልንን" መርገም አይደለም። "ዛሬስ ... በጎ ገድል ተጋደልሁ ... ሃይማኖቴን ጠበቅሁ ... እግዚአብሔር የሚሰጠኝ ዋጋ ይቆየኛል ... የምንልበት ጊዜ ነው። (2ኛ ጢሞ.4፡6)።"[75]

(2.6.3) ምልአተ ኃጢአትን (የየዕለት ኃጢአትን) በሚመለከት ሩቅ ሳንሔድ ኢዮብን በገዛ መጽሐፉ 42፡7፤ አብርሃምንም በዘፍጥረት 20፡1-18 እግዚአብሔር በራዕይ እየተገለጸ በደላቸውን ነግሮ 'ወዳጆቼ አብርሃምና ኢዮብ ካልማለዱኝ በቀር ቁጣዬ ትወርድባችኋለች!' ያላቸውን በደለኛ ሰዎች አማላጅ ሆነው የታዘዘ ቁጣ ሲመልሱ እናያለን። ስለዚህ ምልአተ ኃጢአት በምንገባው ንስሐ (መዝ.50፡1-2)፤ በካህናት ኑዛዜ (ማቴ.16፡19)፤ በአብርሃምና ኢዮብ ዓይነት የበቁ ቅዱሳን አማላጅነት እና በክርስቶስ ይቅር ባይነት የሚደመሰስ ሲሆን ጥንተ አብሶ ግን በክርስቶስ ደም ብቻ የተደመሰሰ ታላቅና የመጀመሪያዎቹ ሰዎች የመጀመሪያ በደልና በልጆቻቸው የደረሰ መርገምና ፍዳ ነው (ሮሜ.3፡23፤ ዕብ.9፡11-28፤ 1ኛ ዮሐ.2፡2፤ 4፡10፤ ቆላ.1፡20)። ተራውንና ተርታውን የየዕለቱን ግላዊ በደላችንን'ማ (ምልአተ ኃጢአታችንን) የኦሪቱ ካህናትም ያስተሠርዩት ነበር (ዘኁ.16፡47)። መሥዋዕቱና ቁርባኑ እንዲሁም የኦሪቱ ደጋግ አበው መደምሰስ ያቃታቸው ጥንተ አብሶ ያመጣውን የጸጋ መታጣትና ሞት፤ መርገሙንና ፍዳውን ነው። ከዚህ መርገም 'መዳን በማንም የለም፤ በደመ ክርስቶስ ብቻ!' ወይም በአባ ጊዮርጊስ የሠርክ ስቅለት ንባብ ስንገልጸው "... ያለአምላክ ደም መፍሰስ በአዳም ኃጢአት ምክንያት የመጣ የምድር ርግማን አልተሻረም።"[76]

[74] ሃይማኖተ አበው ዘቄርሎስ፡ ገ.303
[75] መልአከ ብርሃን አድማሱ፣ኵሎሙ ሃይማኖት፡ ገ.181
[76] መጽሐፈ ምሥጢር፡ ገ.182



(2.6.4) ምግባርን በሚመለከት ምንም እንኳ የአብርሃምና የኢዮብ ጽድቅና ምግባር ከእምነታቸው ጋር ተባብሮ ጥንተ አብሶን ባይደመስስላቸውም ለጊዜው በበጎ ምግባራቸው የተነሣ ከዕለታዊ ኃጢአት የራቀ በረከት ያለበት የቅድስና ሕይወት እንዲኖሩ፤ በሥራቸው ጻድቃን ተብለው እንዲጠሩ፤ ከሲዖል መከራ በእግዚአብሔር የቸርነት መዳፍ እንዲጠበቁ (ጥበ.3፡1-3 እና ሉቃ.16፡22)፤ ከደጉ አብርሃም ሐረገ ትውልድ (ዘር) ትንቢት የተነገረለት ጌታ እንዲወለድ ሆኗልና የምግባርን ነገር ቸል ማለት አይገባም። በተለይ...! አዎ! በተለይ ዓመተ ፍዳን የሚያመለክቱና ጥንተ አብሶ ባልተደመሰሰበት ዘመን የተነገሩ ጻድቅ በምድር እንደሌለ (መክ.7፡20)፤ ጽድቃችን መርገም እንደ ሆነ (ኢሳ.64፡6)፤ ማንም ከኃጢአት እንደማይነጻ (ኢዮ.14፡4)፤ ከሴት የተወለደ ሁሉ ጻድቅ መሆን እንደማይችል (ኢዮ.15፡14)፤ ሁሉም ሰው በደለኛ እንደ ሆነ (መዝ.13፡1-3) የመሳሰሉ ጥቅሶችን ጥንተ አብሶ በተደመሰሰበት፤ መላእክት እና የሰው ልጆች በጌታ ልደት ታርቀው፤ "ሰላም፡ ሰላም እምይእዜሰ ይኩን ሰላም፤" እያልን በምንዘምርበት የዓመተ ምሕረት ዘመን እየጠቀሱ የቅዱሳንን አማላጅነት ለመንቀፍ ያለቦታቸውና ያለጊዜያቸው በየደረሱበት መሰፈፍ ደስ አይልም። የእነ አለቃ ታዬ ለስዊድን ሚሲዮን ገጸ በረከትነት የቀረበ ሰም አልባ የአርኬ ድርደራ የማይጥመንም ለዚህ ነው። የኦሪትን የሥርየት ድንጋጌ ከወንጌል የማዳን ትምህርት፤ የቅዱሳንን አማላጅነት ከክርስቶስ ራሱን ከሶ ከራሱ አስታራቂነት፤ የጥንተ አብሶን ባሕርይ ከምልአተ ኃጢአት ባሕርይ ከነድምሳሴያቸው ለይቶና አብላልቶ፤ እንጠርጥሮና አበጥሮ በሰምና ወርቅ ካልለየሩት ምኑን ተቀኙት?! ቁንፅል አርኬ ቢደረደር ኵሸት እንጂ ቅኔ አይሆን'ማ! ፊደልና ትርጓሜ ለይቶ ለመረዳት ቅን ልብ ጠፋ እንጂ እመቤታችንን መድኃኒት ስንላት የእርሱን ሚና ለእርሷ ሰጥተን አልነበረም፤ አይደለም፤ አይሆንም!

(2.6.5) እመቤታችን ቤዛ፤ መድኃኒት መባሏ እንደ ጌታ ተስቅላ ተቤዠችን፤ ቤት አዳነችን ማለት አይደለም። "በስመ ገዳሪ ይጼዋዕ ማኀደር - ቤት በሚያድርበት ይጠራል።" እመቤታችንን መድኃኒት ቤዛ ስንላትም እንደዚያ ነው - የልዑል ማደሪያ ስለ ሆነች። እንደዚያ ባይሆንና እርሷ ቤዛና መድኃኒት ነች ብለን ብናምን'ማ ለምን ከጌታ ለምኚልን ማለት አስፈለገ?! እርሷ መድኃኒት ከሆነች "አድኀኒነ - አድኚን" ብቻ እንጅ "ስአሊ ለነ -

አማልጅን" የሚል ቃል መቀላቀል አያስፈልገንም ነበር። ከዚህ በፊት ጌታን በመርፌ ውስጥ እንዳለ መድኃኒት፣ እመቤታችንን እንደ ሐኪም፣ ጌታን ፍሬ፣ እመቤታችንን እንደ ፍሬው ተሸካሚ ተክል እየተደረገ እንደ መድኃኒት መባል በዚያ መልኩ እንደሚገለጽ በብዙ ሰባክያን የእርሷ ተነግሯል። ከሕመማችን የፈወሰን መድኃኒቱ /ክኒኑ/ ሆኖ ሳለ መድኃኒቱን ይዞ የተገኘው ዶክተር 'አዳኙን' እንላለን። በምሳሌ ዘየሐጽጽ እርሷ አዳኝ መባሏ እንደ ሐኪሙ መድኃኒቱን ጌታ መድኃኔ ዓለምን ይዛ ስለ ተገኘች ነው - ምክንያተ ድኂን! ሐዋርያው በ1ኛ ጢሞ.2፡15 "የተታለለም አዳም አይደለም፣ ሴቲቱ ግን ተታልላ በመተላለፍ ወደቀች፣ ነገር ግን በእምነትና በፍቅር በቅድስናም ራሳቸውን እየገዙ ቢኖሩ 'በመውለድዋ' ትድናለች፤" ይላል። ይህን ቃል አባቶቻችን ሔዋን "...በልጇቿ በእመቤታችን በጌታ ተከብራለች፣" ብለው ተርጉመውታል።[77] እንግሊዝኛውም "She [Eve] shall be saved in child-bearing" በማለት ሔዋን በመውለዷ እንደ ዳነች ይገልጻል።

(2.6.6) የፍጡር መድኃኒት መባል በእመቤታችን አልተጀመረም። 'ኢያሱ' እና 'ኢሳይያስ' ማለት ትርጓሜው መድኃኒት ማለት ነው። መድኃኒትነታቸው እንደ ክርስቶስ የባሕርይ ሳይሆን የጸጋ መሆኑ ግልጽ ነው። መሳ.3፡9 እንዲህ ይላል፦ "የእስራኤል ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጮሁ፣ እግዚአብሔርም የሚያድናቸውን 'አዳኝ' የካሌብን ታናሽ ወንድሙን ጎቶንያልን አስነሳቸው" እንጨምር፦ አብድዩ ቍጥር 21 "በዔሳውም ተራራ ላይ ይፈርዱ ዘንድ 'አዳኞች' ወደ ጽዮን ተራራ ላይ ይወጣሉ፣ መንግሥቱም ለእግዚአብሔር ይሆናል።" ከላይ የተጠቀሱት ግለሰቦች "አዳኝ" ሲባሉ የመዳን ምክንያት ሆኑ መባላቸው ነው የሚገባን እንጅ እግዚአብሔርን ተክተው የማዳን ሥራ ይሠራሉ ማለት አይደለም። እኛ እመቤታችንን 'ቤዛዊተ ዓለም'፣ እግዝእትነ ወመድኃኒትነ' ስንላትም እንደሱ ማለታችን ነው። በነህ. 9፡27 እና በ2ኛ ነገ.13፡5 እስራኤልን የሚታደጉ "ታዳጊዎች"፣ "አዳኞች" ተብለው የተጠቀሱ ግለሰቦች አሉ። የበረታ አንብቦ ያገናዝብ! ቅዱሳን መላእክትም በዘፍ.48፡16፣ መዝ.33፡7፣ ኢሳ.63፡9፣ ዳን.10፡21፣ በዘካ.1፡12፣ ወዘተ ... ቃል በቃል "አዳኝ" ሲባሉና ለሰው ልጆች ሥርየተ ኃጢአት ሲማልዱ እናገኛቸዋለን። ይህ

[77] ቅዱስ ጳውሎስ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.360



አማኝነትና ምልጃ የሚጠቀሰው ለምልአተ ኃጢአት ነው፣ ለጥንተ አብሶ አይደለም። ስለዚህ ይህን ሳይረዱ ማንጠልጠያ በሌለው ዘበናይ ቅላጼ "ማርያምም አዳኝ፣ ገብርኤልም አዳኝ! የኦርቶዶክስ አምላክ ብዙ...ቱ!" ለማለት መፍጠን "ወፈቀዱ በጽድቀ ርእሶሙ ይቁሙ" የሚለውን የሮሜ.10፡2 ንባብ ያስጠቅሳል።

## 2.7. የሕጻናት ጥምቀት፦ ለዳግም ልደት ወይስ ለጥንተ አብሶ ሥርየት? ሌላው ጭንቀቴ

(2.7.1) የኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን የሕጻናትን ጥምቀትን ለጥንተ አብሶ ድምሳሴ የሚፈጸም ምሥጢር አድርጋ ታስተምራለች፣ 'The Holy Sacrament of Baptism is for the remission of sins which is the Original Sin with which everyone is born - ሥርዓተ ጥምቀት የሚከናወነው እያንዳንዱ ሰው ሲወለድ አብሮት ለመጣው ጥንተ አብሶ ሥርየት ነው"[78] ግብጻውያኑ ጥምቀት ከሚያስገኘው ዳግም ልደት በተጨማሪ 'ወነአምን በአሐቲ ጥምቀት ለሥርየተ ኃጢአት" የሚለውን ዶግማ በመንተራስ የሕጻናት ጥምቀት የአዳም ኃጢአት ወደ ልጆች እንዳይተላለፍ ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ ጭምር ያገለግላል እያሉ ያስተምሩታል። አቡነ መልከ ጼዴቅ በ1984 ዓ.ም. በጻፉት መጽሐፍ ከኮፕቶች ጋር በሚመሳሰል መልኩ ጥምቀት የግል በደልን መደምሰስ ብቻ ሳይሆን ሕጻናት ከወላጅ በዘር ቃና የወረሱትን ጥንተ አብሶ ለማንጻትም የሚፈጸም ምሥጢር መሆኑን ደጋግመው ገልጸዋል።[79] ግብጽ የተማሩት ዓሥራት ገብረ ማርያም እንዲሁ "ትምህርተ መለኮት" በተሰኘ መጽሐፋቸው ስለ ሕጻናት በጥምቀት ክርስትና በዘር ከሚመጣ ኃጢአት (ጥንተ አብሶ) መንጻት ከአቡነ መልከጼዴቅ ጋር የሚመሳሰል ጽሑፍ አስፍረዋል።[80] ሌላኛው ኦርቶዶክሳዊ ጸሐፊ ብፁዕ አቡነ ጎርጎርዮስን ዋቢ አድርገው "ጥምቀት ካልፈጸምን ... በመጀመሪያው መርገም ሥር ነን ... ከጥንተ አብሶ መርገምም ነጻ አይደለንም። ... ብፁዕ አቡነ ጎርጎርዮስ እንዳስተማሩን 'የአዳምና የሔዋን ልጆች ... በ40/ 80 ቀናቸው ሲጠመቁ በዘር ከወረደው መርገም ይነጻሉ። የቀደመውን ወላጆች ያስወሰዱት የጸጋ ልጅነት በጥምቀት ይመልሱላቸዋል፣'" ይላሉ።[81] አክለውም

[78] ከላይ በተራ ቍጥር 2.3.3 የቀረበውን ጥቅስ ተመልከት
[79] አባ መልከ ጼዴቅ፣ ትምህርተ ክርስትና 2ኛ መጽሐፍ፡ ገ.30፣91፣98፣100
[80] ዓሥራት ገ/ማርያም፡ገ.218-220
[81] ሊቀ ጉባኤ አበራ፡ ገ.92

"... ከዕለተ ዓርብ በደሙ ካሣ ሲከፍል ያን ጊዜ የአዳምና የዓለም ኃጢአት ሁሉ የተደመሰሰ ስለ ሆነ ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጥንተ አብሶ በሰዎች ላይ አይገኝም የተባለው እምነው ለተጠመቁ ክርስቲያኖች እንጂ ከቤተ ክርስቲያን ውጭ ለሆኑት ሁሉ አይደለም። የውጮቹ'ማ የዕለተ ዓርቡን ተልእኮ ስለማያምኑበት በጥንተ አብሶ በመጣብን መርገም ሥር ናቸው።" ብለዋል።[82] ከላይ የተዘረዘሩት ሁሉም አበው (በእኔ እምነት) ኢትዮጵያዊ የሆኑ መጻሕፍትንና ትርጓሜያትን[83] በበቂ ማጣቀሻነት አላቀረቡልንምና በመደምደሚያቸው ልቤ ይከፈላል።

(2.7.2) ከምድረ ኤርትራ በቅሰው በመላዋ ኢትዮጵያ ካንጸባረቁ ሊቃውንት አንዱ የሆኑት ሊቀ መዘምራን ሞገስ ዕቁበ ጊዮርጊስ ስለ ሕጻናት ጥምቀት ዐራት ሐሳቦችን ያቀብሉናል፡-

(1) [ልክ] 40/ 80 ቀን ሞልቷቸው ክርስትና መነሣት በሚችሉበት ቀን ሳይጠመቁ የሞቱ ሕጻናት ዕዳ የለባቸውም፤ ዕዳው ማስጠመቅ ሲገባቸው ባላስጠመቋቸው ወላጆቻቸው ላይ ነው።

(2) 40/ 80 ቀን ሳይሞላቸው የሞቱ ሕጻናት የእናትና አባታቸው ሥጋና ደም ስለ ሆኑ አልተጠመቁም ተብለው አይኰነኑም፤ ልጅ የአባቱን ኃጢአት አይሸከምም (ሕዝ.18፡20)።

(3) [40/ 80 ቀን አልፏቸው] ሳይጠመቁ የሞቱ የአማኞች ልጆች ለመጠመቃቸው በወላጆች ጥፋት ከሆነ ወላጆቻቸው ይቀጡና እነሱ ገነት ይገባሉ (ማቴ.19፡14)።

(4) [40/ 80 ቀን አልፏቸው] ሳይጠመቁ የሞቱት የአረማውያን (መናፍቃን) ልጆች ከሆኑ የአባቶቻቸው ርስት ወደ ሆነች ገሃነም ይገባሉ /1ኛ ቆሮ.6፡15/።[84]

---

[82] ገጺ ከማሁ፡ ገ.204

[83] አንድ ትጉህ አንባቢ የሆነ ኦርቶዶክሳዊ ወንድሜ ግን (ስሙን እንዳልጠቅስ "ቢቀለ መሀይምን ገዝቻለሁ" ስላለኝ ነው)፡- (1) ወንጌልም በአኃቲ ጥምቀት ለስርየተ ኃጢአት የሚለው ንባብ የኢድሜ ገደብ አያስቀምጥም፤ ህጻናትን አይመለከትም አይልም። (2) በትምህርተ ኅቡዓት "እኛም ከሥጋ በፈሰሰ ማየ ገቦ ተጠምቀን ከፍዳ ነጽተናል፤ ከቁራኝነት ተላቀናል፤" ተብሎ የቀረበው ትርጓሜም በራሱ አስረጂ ነው። (3) በሮሜ 6፡5 እንደተገለጸው ጥንተ አብሶ ውጤት የሆነውን ሞት ማሸነፍ የሚቻለው ሞቱን በሚመስል ጥምቀት ነው። ይኸውም በ2ኛ ቆሮ.5፡17 ማንም በክርስቶስ ቢሆን አዲስ ፍጥረት ነው ተብሎ በጥምቀት የምናገኘው ከቀደመው በደል የተላቀቀ አዲስ ሰውነት መሆኑን በሚጠቁም መልኩ ተጽፎልናል። ስለዚህ የህጻናት ጥምቀት ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ ሳይሆን ለዳግም ልደት ብቻ ነው ብሎ መደምደም ተገቢ አይደለም የሚል እይታ ያንጸባርቃል።

[84] መርሐ ጽድቅ ባሕለ ሃይማኖት፣ 1988 ዓ.ም.፡ ገ.103



ካቶሊካውያን ሳይጠመቁ የሞቱ ሕጻናት በጥምቀት ከጥንተ አብሶ ስላልነጹ በአሪቱ የነበሩ አበው ከሲዖል መከራ በእደ እግዚአብሔር ተጠብቀው በቆዩበት መንገድ ገነት ሳይገቡ limbo (ሕጽን አብርሃም/ የአብርሃም እቅፍ) የተሰኘ ጊዜያዊ የመንጽሔ ነፍሳት ቦታ ዐርፈው እስከ ምጽአተ ክርስቶስ በፈጣሪ ምሕረት እንደሚቆዩ ይገልጻሉ።[85]

(2.7.3) አሳባችን ዝርው እንዳይሆን በፍትሐ ነገሥት እንሰብስበው፤ እንደ ፍትሐ ነገሥቱ አንቀጽ ሦስት ድንጋጌ ሕጻን ልጅን በወቅቱ ክርስትና አለማስነሣት ካህን ከሆነ ከአገልግሎት፣ ምእመን ከሆነ ከቁርባን የሚያሳግድ ጥፋት ነው። በወላጅና በልጅ መካከል ስላለው የጥምቀት ግንኙነት ፍትሐ ነገሥቱ የፀነሱ ሴቶችን ጥምቀት ባብራራበት አንቀጽ ሲገልጽ "የፀነሱትን ሴቶች በወደዱት በማናቸውም ጊዜ ከመጠመቅ አይከልክሏቸው። በእናትና በልጁዋ መካከል በጥምቀተ ክርስትና አንድነት የለም። ሰው ሁሉ በየራሱ እምነቱን ሲገልጽ ይገባዋል እንጂ" ይላል።[86] 40/ 80 ቀን ሳይቆይ ቀድሞ ይሞታል ተብሎ የሚያሰጋ ሕጻን በምግዚት ቤተ ክርስቲያን ገብቶ ሊጠመቅ እንደሚገባ ተደንግጓል።[87] እንደ ፍትሐ ነገሥቱ የጥምቀት ዓላማ፦ ሰው በአብ ወልድ መንፈስ ቅዱስ ስም ተዘፍቆ በመውጣት በሚደረግ የጌታን ሞትና ትንሣኤ የሚያዘክር ታላቅ ምሥጢር ከውኃና ከመንፈስ ዳግም ልደት አግኝቶ የእግዚአብሔርን መንግሥት እንዲወርስ ማስቻል ነው (ዮሐ.3፡5፣ ማቴ.28፡19፣ ሮሜ.8፡1፣ 6፡3-5)።[88]

(2.7.4) በትምህርተ ኅቡዓት ትርጓሜ "ጸዕረ ዘሞት ፈትሐ" ላይ "እኛም ከሥጋ በፈሰሰ ማየ ገቦ ተጠምቀን ከፍዳ ነጽተናል፤ ከቁራኝነት ተላቀናል፤" የሚል ንባብ አለ።[89] ንባቡና ትርጓሜው በጌታ ቤዛነት ምሕረት ከመውረዱ በፊት ባለው ዓመተ ፍዳ፣ ዓመተ ኩነኔ ተሰጥቶ ቢነገር የቀና ይሆናል። ፍትሐ ነገሥቱ የሕፃናትን ጥምቀት ከውኃና መንፈስ ከሚገኘው ዳግም ልደት ጋር እንጂ ከአዳማዊው በደልና ቁራኝነት ጋር አላያያዘውም። አክሲማሮስ ዘዓርብ[90] ቁራኙን በተፈጠሩባት ቤተ ክርስቲያንን በገነት፣ አዳምና ሔዋንን በሕፃናት፣ ቤተ ክርስቲያንን በገነት፣ ቁራኙን በተፈጠሩባት ቦታ መስሎ በሚናገረው ኢትዮጵያዊ ትውፊት የሕጻናት ጥምቀት ማንጻሪያ

---

[85] Catholic Encyclopedia, http://www.newadvent.org/cathen/09256a.htm

[86] ፍትሐ ነገሥት፡ አንቀጽ 3(33)

[87] ገጺ ከማሁ፡ አንቀጽ 3፡34

[88] ገጺ ከማሁ፡ አንቀጽ 3፡27

[89] መ/ገነት ዘለዓለም አለይ፣ የአሉት ሃይማኖት ትርጓሜ፣ 1988 ዓ.ም.፡ ገ.79

[90] አክሲማሮስ፡ገ.157

ሆኖ በተደጋጋሚ የሚቀርበው "በተፈጠረባት ምድር ለአዳም ዐርባ ቀን ከተፈጸመለት በኋላ ይገባትም ይጠብቃትም ዘንድ ወደ ገነት አስገባነው፤ ሚስቱንም በሰማኒያ ቀን አስገባናት፤" የሚለው የኩፋ.4:9 ቃል ነው። ይህ ትውፊት ደግሞ ገና የአዳምና ሔዋን ባሕርይ በጥንተ አብሶ ሳያድፍ የነበረውን አኗኗር ስለሚያጣቅስ የሕፃናትን ጥምቀት ከጥንተ አብሶ ጋር ከሚያያይዘው ትረካ ጋር አይገጥምም። ከኢ/ኦ/ተ/ቤ/ክ. ትውፊት እንደምንረዳው አዳምና ሔዋን ዐራት የሕይወት ምዕራፎች አሏቸው። እነርሱም፡-

(1) በአክሊማርስ ዘዓርብና በኩፋ.4:9-10 የሰፈረው ተፈጥረው በንፍሐት የጸጋ ልጅነት አግኝተው ወደ ገነት ከመግባታቸው በፊት ያለው 40/ 80 ቀን፣

(2) በንፍሐተ መንፈስ ቅዱስ ልጅነት አግኝተው በገነት ያሳለፉት የተድላና የደስታ ጊዜ፣

(3) የተከለከሉትን ፍሬ በልተው የወደቁበት ጊዜ፣

(4) በጌታ ቤዛነት ወደ ቀደመው ቦታቸው የተመለሱበት የድኅነት ጊዜ ናቸው። በቀራንዮ ከተደረገልን የማዳን ሥራ ወዲህ ስንወለድ አዳምና ሔዋን በዐራቱ ጊዜያት ከነበሯቸው የሕይወት ምዕራፎች ውስጥ የመጀመሪያውን ተሳብሰን ነው፤ ማለትም ልጅነት ባናገኝም ርግማንም አይኖርብንም። ለዚህ ጥሩ ማንጸሪያ በዘፍ.1:26 ስለ አዳም ነፍስ አፈጣጠር ሲብራራ፡- "ወነፍሐ ላዕሌሁ መንፈሰ ሕይወት" የሚለው ቃል በሊቃውንት የሚሰጠው ሁለተኛ ትርጓሜ ነው። ይህ ሐረግ በአንድ በኩል "ነባቢት ነፍስን ማሳደር" ተብሎ የተተረጎመ ሲሆን በአንድምታ እንደገና "በአርባ ቀን የመንፈስ ልጅነትን በጸጋ ማሳደር" ተብሎም ይተረጎማል።[91] ከዚህ አንጻር ትውፊታችን ጥምቀትን ከጥንተ አብሶ ይልቅ በጥምቀተ ክርስትና ከሚገኝ ዳግም ልደት ጋር ማያያዙን ነው የሚያተኩረው ወደ ማለቱ እጋድላለሁ። የትምህርተ ኀቡዐቱ ትርጓሜም ቀደም ሲል እንደ ተጠቀሰው አንድ ጊዜ በቀራንዮ ስለ ተደረገው ከፍዳና መርገም በደመ ክርስቶስ የመንጻት ብሒል ተሰጥቶ ቢተረጎም የቀና የሚሆን ይመስለኛል። የአገራችን ኦርቶዶክሳውያን መተርጉማን ጥምቀትን "ዳግም ልደት" ይሉና ዳግምነቱ ግን ለጥንተ አብሶ ድምሳሴ ሳይሆን፡- ከአረማዊነት

---

[91] መጻሕፍተ ብሉያት ክፍል፬: ገ.22። የመጽሐፈ ቅዳሴ ትርጓሜ: ገ.283፣327



ወደ አማኒነት፣ ከሥጋዊ ልደት ወደ መንፈሳዊ ልደት፣ ከኃጢአት ወደ ንስሐ ለሚደረግ መንፈሳዊ ጉዞ እንደ ሆነ ይነግሩናል።[92]

(2.7.5) ከክርስቶስ ስቅለት ወዲህ ለመዳንና ላለመዳን የተቀመጠው መስፈርት፡- ማመን ወይም አለማመን (ማር.16:16)፣ መጠመቅ ወይም አለመጠመቅ (ዮሐ.3:5)፣ ሥጋና ደሙን መቀበል ወይም አለመቀበል (ዮሐ.6:56)፣ የጽድቅን ሥራ ሠርቶ በቀኙ ለመቆም መዘጋጀት ወይም አለመዘጋጀት (ማቴ.25:32-46) እንጂ ጥንተ አብሶ መፈራረጃ የመሆን ዕድሉ ዛሬ ሕልው አይመስልም። ምሳሌዬ ህፁፅ ቢሆንም የቀደመው ዕፀ በለስን ማዕከል ያደረገ የመፈራረጃ ሕግ ተሽሮ ድኅነት ከቀራንዮ ጋር ከተቆራኘ በኋላ በጥንቱ የወንጀል ሕግ እንዳኝም (non-retroactivity of criminal law) ብዬ እምናለሁ፤ የወንጀል ሕጉ ተሻሽሏልና በተሻረ ሕግ አይፋረደንም። "ከክርስቶስ ስቅለት፣ ሞትና ትንሣኤ ወዲህ ሰዎች በአንዱ በእግዚአብሔር ልጅ ባለማመናቸው ይጠየቃሉ እንጂ በጥንተ አብሶ አይጠየቁም። ጥንተ አብሶ በክርስቶስ ስቅለት፣ ሞትና ትንሣኤ ተደምስሷል፤" የሚለው የመምህር ኃይለማርያም ላቀው ጽሑፍ (ጽሑፉ ከሊቀ ጉባኤ አበራ አቋም ጋር ባይገጥምም) ለንዑስ ርእሳችን አሳብ ሸጋ ማስረጃ ነው።[93]

አለቃ አያሌው ታምሩም "...በጽንስ በጀመረው የቤዛነት ሥራው ስለ ሻረውና ስለ አጠፋው ከጌታ ሰው መሆን [ጽንሰቱ] ወዲህ በማንኛውም የሰው ዘር ላይ ቁራኝነት የለም። የውርስ ኃጢአት የለም። ማንኛውም ሰው በራሱ ኃጢአት ከሚጠየቅ፣ ከሚከሰስ፣ ከሚወቀስ በቀር በአዳም በደል አይከሰስም፤ እንኳ ቢሆኑ አይወቀስም። ... እንግዲህ የውርስ ኃጢአት ሕጻናትም የሌለባቸው መሆኑን ማንም ሊገነዘበው ይገባል። ... ጌታ ሕጻናትን 'ወደ እኔ ይምጡ አትከልክሏቸው' ካለ በኋላ 'መንግሥተ ሰማያት እንደዚህ ላሉት ናትና' ማለቱ የውርስ ኃጢአት ላለባቸው ማለቱ ነውን?" ሲሉ ከጌታ ሥጋዌ ወዲህ ጥንተ አብሶ በየደረጃው ተደምስሶ አዲስ የድኅነት ሥርዓት መሠራቱን በቃለ ተግሳጽ ጽፈዋል።[94]

---

[92] የመጽሐፈ ቅዳሴ ትርጓሜ :ገ.50

[93] መ/ር ኃይለማርያም: ገ.172

[94] አለቃ አያሌው ታምሩ፣ ምልጃ፣ አርቅና ስላም:ገ.53።

"ወነአምን በአሐቲ ጥምቀት ለስርየተ ኃጢአት" በሚለው ንባብ ውስጥ ያለችው "ሥርየተ ኃጢአት" የምትል 'ነባር' ኃጢአትን ለመሳካት ሐረግ የምታመለክተው ካደጉና ከጎለመሱ በኋላ ተምረው፣ አምነው፣ ለመክር (የፈተና ጊዜ) አልፈው ለጥምቀተ ክርስትና የበቁ ንዑሰ ክርስቲያኖችን ወይም የንስሐ ጥምቀትን እንጂ በጌታ ስቅለት የተነሣ በታወጀልን የምሕረት ዘመን ለዓም ገነት ከመግባቱ በፊት በነበረው ንጽሐ ባሕርይ አምሳል የተወለዱ ሕጻናትን ወይም ጥንተ አብሶን አያመለክትም ብለን ብንከራከር ተገቢ ይመስለኛል። ኢትዮጵያውያን አበው ያስቀመጡልን የጸሎተ ሃይማኖት ትርጓሜ ስለ ጥምቀተ ክርስትና ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ መሆን ምንም ያስቀመጠው ሐተታ የለም። በበኩሌ ከእጓት አብያተ ክርስቲያናት ጋር ሕጻናትን ከማጥመቅ እስከ ንዑሰ ክርስቲያን (ከኑፋቄ/ ከአረሚነት/ የተመለሱና በእምነትና በትምህርት ገና ያልጠነከሩ አዳዲስ ክርስቲያኖች) ዳግም ልደት ባለው ጥምቀት አፈጻጸም ዶግማና ቀኖና ስለምንስማማ በጥንተ አብሶ ዙሪያ ያለችውን ልዩነት አግዝፎ ማየት እንደማይገባ በማመን የራሳችንን ትውፊት ብንወግን እመኛለሁ።



ስለ ነፍስ ተፈጥሮና ጥንተ አብሶ ትንታኔ ልዩ ልዩ አመለካከቶችን የሚያነጻጽር ሠንጠረዥ

| | ኦሪየንታል ኦርቶዶክስ (አለቃ ኪዳነ ወልድ) | ካቶሊክ | ምሥራቃውያን /ኦርቶዶክስ | ክፍት | የኢ/ኦ/ተ/ቤ/ክ ትውፊት ዝንባሌ | እቡነ መልከ ጸዴቅ[95] |
|---|---|---|---|---|---|---|
| ነፍስ ከወላጅ ትከፈላለች | X | X | X | √ | √ | √ |
| ነፍስ ጽንስ ሲፈጠር እም ኀበ አልቦ ኀበ ቦ ትፈጠራለች | X | √ | √ስለ ነፍስ ተፈጥሮ ማዕከላዊ አቋም ባይኖራቸውም | X | X | X |
| የሰው ሁሉ ነፍስ አስቀድማ ተፈጥራለች | √ | X | X | X | X | X |
| ኃጢአቱንና መርገሙን አንድ ላይ ወርሰናል | X | √ | X | √ | X | √ |
| የተሳለፈው መርገሙ ብቻ ነው | X | X | √ | X | √ | X |
| ጥምቀተ ክርስትና ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ | X | √ | X | √ | X | √ |
| ጥምቀተ ክርስትና ለዳግም ልደት | √ | √ | √ | √ | √ | √ |
| ኃጢአት (ጥንተ አብሶ) በዘር/ በሩካቤ ይተላለፋል | X | √ | X | √ | X | √ |

√ = ይቀበላሉ X = አይቀበሉም

[95] ማስታወሻ፡- የአቡነ መልከጼዴቅን አቋም በኦርቶዶክሳዊ ጥላ ስር ያለ አመለካከት አድርጌ ነው የማየው! ስህተት ነው እያልኩ አይደለም፣ ለማለትም አልችልም! ለንጽጽር ብቻ ነው ለንጠረዡን የተጠቀምኩት!!

# ምዕራፍ ሦስት

## የአንጽሖ ቡድን፡- "እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት፤ የጠፋላት በበስራቷ ጊዜ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነው!"

በዚህ ቡድን ውስጥ ከአገር ውስጥ እስከ ባሕር ማዶ ዘመነኛ ሊቃውንት፤ ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ፣ ከደጋርት እስከ ቀደምት፣ ከመነኮሴ እስከ ፓትርያርክ፣ ከቀዳስያን እስከ ሊቃውንት አባል ድረስ "እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት፤ የጠፋላት በብሥራቷ ጊዜ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነው፤" ብለው ያስተማሩ ሰዎች ጽሑፎችን እሳባቸው ቅኝቱን ሳይለቅ ግን በቀሊል አማርኛ እንደ ወረደ በክብር ለማቅረብ ይሞከራል። ቡድኑ 'አንጽሖ' ስለ ተባለ ሁሉም የቡድኑ አባላት አንድ ዓይነትና ፍጹም የተመሳሰለ አቋም አላቸው ማለት አይደለም። በዋናው አሳብ ላይ ስለሚስማሙ ብቻ በአንድ ርእስ ስር አጠቃለልኳቸው። አስቀድሞ ሁሉንም የሚያስተሳስራቸውን ቃል እንተርጉም - አንጽሖ!!!

"አንጽሖ" አስደራጊና አድራጊ ግስ ሲሆን ሥርወ ቃሉ "ነጽሐ" ነው። ትርጓሜው እንደየአገባቡ የተለያየ ፍች አለው። ለርእሳችን የሚጠቅሙንን ሁለቱን ፍቺዎች እንውሰድ። የመጀመሪያው ትርጉም "ንጹሕ መሆን" ነው። ሁለኛው ትርጉም "ልዩ መሆን" ማለት ነው፤ "ንጹሕ አነ እምደሙ ለዝ ብእሲ ጻድቅ ወኄር" የሚለውን የጲላጦስ ንግግር ስንጠቅስ "በምክራችሁ ላይ ተዐቅቦ አለኝ፤ ተለይቻለሁ!" ማለቱ ነው የሚገባን። በአማርኛ "ከደሙ ንጹሕ ነኝ!" የሚለው ብሒል ሁለተኛውን የነጽሐ ትርጓሜ ለመረዳት አጋዥ ነው። "አንጽሐ" በራሱ አድራጊና አስደራጊ ሊሰኝ የሚችል ግስ መሆኑ እንደ ተጠበቀ እዚህ ላይ ግን "ነጽሐ" ለሚለው ቃል አስደራጊ ተደርጎ ቢወሰድ የቀና ይሆናል። በእንግሊዝኛም "Sanctify" የሚለው ቃል ልክ እንደ አንጽሐ "to purify - ማንጻት" ተብሎ ይተረጎማል፤ በሌላም በኩል "to set aside for sacred use - ለቅድስና አስቀድሞ መለየት" የሚል ትርጉም አለው። በመጻሕፍት ልማድ ማንጻት ከሦስቱ አካላት አንዱ ለሆነው ለመንፈስ ቅዱስ



ይቀጸላል። "መንጽሒ (የሚያነጻ)፣ ናዛዚ (የሚያረጋጋ)፣ መጽንዒ (የሚያጸና)" ይባላል - መንፈስ ቅዱስ። ይህ ቅጽል "መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ" ከሚለው የቅዱስ ገብርኤል የሉቃ.1:35 ቃል ጋር ሲገጣጠም መንፈስ ቅዱስ ወደ እመቤታችን የመጣበት ምክንያት በአንደኛው ወገን የመጀመሪያውን የ"አንጽሐ" ትርጓሜ በመያዝ፡- መምጣቱ "መንጽሒ ነውና ከጥንተ አብሶ ለማንጻት እንጂ ሌላ ምክንያት የለውም!" ይባላል። በሌላኛው ወገን ደግሞ ሁለተኛውን የ"አንጽሐ" ትርጉም በመምረጥ፡- መንፈስ ቅዱስ መምጣቱ "መጽንዒ ነውና ገና ስትፀነስ የነበራትን ንጽሕና በዕቅበት አስጠብቆ የጌታን ሥጋ ከሥጋዋ፤ ነፍሷን ከነፍሱ ለማዋሐድ፤ እርሷን ለማጽናት ነው!" ይላል። የኋለኞችን "የዐቀባ ቡድን" ብዬቸዋለሁ፤ የፊተኞችን "የአንጽሐ ቡድን" አሁን ርእሳችን ስለ "አንጽሐ" ስለ ሆነ በየዘውጋቸው ማየታችንን እንቀጥል።

## 3.1 አንጽሐ፡- በካቶሊካዊው ቶማስ አኲናስ (St. Thomas Aquinas) እይታ

(3.1.1) ቀደም ሲል እንዳየነው ካቶሊካውያን ስለ ነፍስ አፈጣጠር ያላቸው አመለካከት በወንድና ሴት ተራክቦ ጽንሱ በሴቷ ማኅፀን ሲቀረጽ ወዲያውኑ ለእያንዳንዱ ጽንስ አዲስ ነፍስ "እምነበ አልቦ" ትፈጠርለታለች የሚል ነው። በዚህ መርሕ የሚያምነው ቶማስ አኲናስ (St. Thomas Aquinas) "እመቤታችን የተፀነሰችው በሕገ-ተፈጥሮ ነው፤ ከጥንተ አብሶ የነጻች አይደለችም፤...Virgin Mary was conceived in a natural way, she was not exempted from the law of Original Sin" ይላል - ለአንጽሖ ወግና የዐቀባ ቡድኖችን ሲቃወም።[1] እንደ ቶማስ አኲናስ በወንድና ሴት ዘር የሆነው የሥጋ ጽንሰት ሥጋ ከነፍስ ጋር ተዋሕዶ ከሚኖረው ሕላዌ /ሕይወት/ (animation) ይቀድማል። 'በጽንስ ጊዜ ሥጋ ከነፍስ ቀድሞ ነው - conception of the body precedes its animation።' የሚፈጠረው ሁለቱ (ሥጋና ነፍስ) በሚዋሐዱበት ጊዜ ከፍትወተ ሥጋ (concupiscence) በሚመነጭ ተራክቦ የተገኘው ግዘፈ ሥጋ መጀመሪያ ራሱ በተራክቦ ስለ ተገኘ

[1] Aba Paulos: Filseta; p.309

የኃጢአት ቁራኛ ይሆናል። በመቀጠል ነፍስ እንደ አዲስ ተፈጥራ ስትዋሐደው በቁራኝነቱ (በጥንተ አብሶ) ነፍስን ያረክሳታል።

(3.1.2) ይህን መርሕ ይዘን ወደ እመቤታችን ተፈጥሮ ስንሔድ ይላል ቶማስ አኩናስ እመቤታችን የተፀነሰችው በወላጆቿ ተራክቦ ነው። ስለዚህ፡-
(1) ገና ጽንስ ሆና በእናቷ ማኅፀን ሥጋና ነፍሷ ከመዋሐዳቸው (Infusion) በፊት እመቤታችን ከጥንተ አብሶ አልነጻችም። ነፍስ ያልተዋሐደው ግዑዝ ግዚፈ ሥጋ ብቻ ከኃጢአት (guilt) ሊነጻ አይችልም። "ምክንያቱም ማሰብና ማገናዘብ የሚችል ፍጥረት ብቻ ነው ኃጢአት ሊሠራ የሚችል - because only the rational creature is susceptible to guilt."
(2) እመቤታችን በማኅፀን ሐና ሳለች ገና ሥጋዋ ከነፍሷ ሳይዋሐድ ነጻች ካልን የክርስቶስን ሰውን የማዳን ሥራዎች ሐሳዊ እናደርጋለን፤ እርሷም በእርሱ ቤዛነት አልዳንችም ያሰኘብናል /ማቴ.1:2 እና 1ኛ ጢሞ.4/። እዚህ ላይ የቶማስ ጭንቀት ገና በጽንስ ደረጃ የነበረው የእመቤታችን ሥጋ ነፍስ ስላልተዋሐደው (ነፍስ ተዋሕዳው ሰው ስላልሆነ) ለድኅነት ዝግጁ አልሆነም ነው። እርሱ እንደሚለው ወትሮውንም ኃጢአት ያለነፍስ ተሳትፎ ስለማይሠራ ገና ስትፀነስ ነጻ ነበረች ቢባል አያስኬድም።
(3) የሚያስኬደው፡- "እመቤታችን ከጥንተ አብሶ የነጻች ገና ሥጋዋ ሲፀነስ ሳይሆን ሥጋን ሕያው የምታደርግ ነፍስ በማኅፀን ሐና ስትዋሐዳት ነው!" ይላል ካቶሊካዊው መነኩስ ቶማስ አኩናስ - "The sanctification of the blessed Vergin took place after her animation."[2]

(3.1.3) በአጭሩ የቶማስ አኩናስ አመለካከት "እመቤታችን ጥንቱን ስትፀነስ ከጥንተ አብሶ ነጽታ አልተፀነሰችም። ነገር ግን በእናቷ ማኅፀን ሥጋና ነፍሷ ተዋሕደው ሕላዌ ካገኙች በኋላ እዚያው በማኅፀን ሐና ሳለች ነጽታለች - She was tainted by Original Sin at the time of her conception, [but], rendered immaculate at some later point while still in her mother's womb" ነው የሚለው።[3] ቶማስ አኩናስን ደግፈው "sanctification after her animation - መንጻቷ ከሕላዌ ነፍሷ በኋላ" ብለው የቆሙ ካቶሊካውያን ቶማሳውያን /Thomists/ ወይም ዶሚኒካውያን

[2] Thomas Aquinas cited by Aba Paulos:Filseta, p.310
[3] Abe Paulos:Filseta, p.309



/Dominicans/ ሲባሉ ከጽንሰቷ ጀምሮ ጥንተ አብሶ ሳያገኛት ተፀንሳለች (Immaculate Conception - ጽንሰት ዘእንበለ አበሳ አዳም) የሚለውን የደን ስኮትስ /Duns Scotus/ የዐቀባ (preserved her) የሚደግፉ ደግሞ ስኮትሳውያን /Scotists/ ወይም ፍራንሲስካውያን /Franchiscans/ ተብለው ለሁለት ተጧድነው ከ12ኛው እስከ 19ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ሲከራከሩ ከቆዩ በኋላ በ1848 ዓ.ም. ጉዳዩን መርምሮ የመጨረሻ ውሳኔ አሳብ የሚያቀርብ ኮሚሽን ተቋቁሞ በ1854 ዓ.ም. የዐቀባ ቡድን አቋም በነቶማስ አኩናስ እንጽሐ አቋም ላይ የበላይ ሆኖ በሥልጣን ፖፕ ፒየስ 9ኛ በዶግማነት ታወጀ፤ የእንጽሐ ፋይል ተዘጋ።[4]

## 3.2. እንጽሐ፡- በእነ አቡነ ሺኖዳዋ የግብጽ ኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን

(3.2.1) ስለ እመቤታችን ቅድስና፣ አማላጅነት፣ ክብር፣ ምስጋና፣ ወላዲተ አምላክነት፣ ከምልአተ ኃጢአት (ጎልዮ፣ ነቢብ እና ገቢር) ንጽሕት መሆን ደጋግመው በመጻፍና በመናገር የሚታወቁት ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ሺኖዳ ሣልሳዊ ጥንተ አብሶን በሚመለከት ያላቸው አቋም ግን "እንጽሐ" ከሚሉት ወገኖች የሚደመር ነው። በጽሑፎቻቸው ቤተ ክርስቲያናቸው እመቤታችን ከጥንተ አብሶ የነጻች በግብረ መንፈስ ቅዱስ መሆኑን፤ ይኸውም መልአኩ ቅዱስ ገብርኤል "መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ" ባላት ጊዜ እንደ ሆነ፤ በእርሷ አስቀድሞ መንጻት ከእርሷ የሚወለደው ጌታ ያለጥንተ አብሶ እንደ ተፀነሰ፣ የእርሷ የግሏ (ከሐና እና ኢያቄም የሆነው) ጽንሰቷ ግን በጥንተ አብሶ እንደ ሆነ፤ ከዚህም በመነሳት መድኃኒት ሸታ በሉቃ.1:47 "ወትትሐሰይ፡ መንፈስየ፡ በአምላኪየ፡ ወመድኃኒየ" ማለቷን በመጥቀስ ቤተ ክርስቲያናቸው የካቶሊካውያኑን የዐቀባ ዶግማ እንደማትቀበል ገልጸዋል። የአቡኑን ቃል እንደ ወረደ እናቅርበው፡-
"The church believes that the Holy Spirit has sanctified the depository of the Virgin during the pregnancy with Christ...That was according to what the angel said to her 'The Holy Spirit will come upon you, and the power of the Highest will overshadow

[4] Ibid: p.312

you; therefore, also, that Holy one who is to be born will be called the Son of God' /Lk.1:35/….The Sanctifying by the Holy Spirit of her depository,makes the one born of her,be conceived without the impurity of the Original Sin.As for the Virgin Herself, her mother conceived, like all people, and so The Vergin said in her hymn 'My spirit has rejoiced in God my Savior' (Lk.1:47).That is why the [Coptic] Church does not agree that 'The Virgin was conceived without the impurity of the Original Sin,' as our brothers the Catholics believe - ቤተ ክርስቲያን መንፈስ ቅዱስ የድንግልን አበሳ ክርስቶስን በፀነሰች ጊዜ እንዳነጻ ታምናለች። ይኸውም ቅዱስ ገብርኤል 'መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ፤ ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ፤ ዘኒ ይትወለድ እምኔኪ ቅዱስ ውእቱ፤ ወይሰመይ ወልደ እግዚአብሔር ልዑል /ሉቃ.1:35/ ባላት ጊዜ ነው። … ከአበሳው በመንፈስ ቅዱስ መንጻቷ ከእሷ የተወለደውን ጌታ እንበለ ጥንተ አብሶ እንዲፀነስ አደረገው። የእርሷን ፅንሰት (መፀነስ) በሚመለከት ግን እናቷ (ቅድስት ሐና) እንደ ማንኛውም ሰው ነው የፀነሰቻት፤ ስለዚህ ነው ድንግል 'ወትትኀሠይ መንፈስየ በአምላኪየ ወመድኃኒየ' ያለችው። ለዚህ ነው (የኮፕት) ቤተ ክርስቲያን ወንድሞቻችን ካቶሊካውያን ድንግል እንበለ ጥንተ አብሶ ተፀነሰች ከሚሉት እምነት ጋር የማትስማማው።"[5]

(3.2.2) ኮፕቶች ስለ ጥንተ አብሶ ያላቸውን አመለካከት እንዲገልጹ "እንጽሖ" የሚለውን ብሒል ከሚደግፉት ኢትዮጵያውያን ቀሳውስት ቤተ ክርስቲያን ለቀረበላቸው ጥያቄ ሲመልሱ፡-

(1) ፅንሰቱ ያለጥንተ አብሶ የተከናወነ የጌታ ብቻ እንደሆነና እመቤታችን ግን በብሥራተ መልአክ ጊዜ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ከጥንተ አብሶ እንደ ነጻች፤

(2) እመቤታችንን ጨምሮ ሁሉም የአዳም ልጆች በጥንተ አብሶ እንደ ተጸነሱ፤

(3) እመቤታችን በራሷ እንደብት "መንፈሲ በአምላኪ በመድኃኒቴ ሐሴት ታደርጋለች" እያለች መድኃኒት ፈላጊ መሆኗ ጥንተ አብሶ የነበረባት መሆኑን እንደሚያመለክት፤

[5] Pope Shenouda III Series-2,1999,The Holy Vergin St.Mary,p.10



(4) እመቤታችን ያለጥንተ አብሶ ተፀነሰች የሚለው ብሒል የጌታን በደሙ የተፈጸመ የማዳን ሥራ ከቡርነት ዝቅ እንደሚያደርግና ያለደም በሆነ መቤዠት ጥንተ አብሶን ደምስሶ ማዳን ቢኖር ኖሮ ጌታ ጸጋውን ለሁላችን ተፈጻሚ ያደርገው እንደ ነበር፤

(5) እመቤታችን ለአምላክ እናትነት (ወላዲተ አምላክ ለመሆን) የበቃች ያለጥንተ አብሶ ከሐና እና ኢያቄም በመወለዷ ሳይሆን በእምነቷ፤ በታዛዥነቷ እና ለእግዚአብሔር ባላት ፍቅር መሆኑን በማብራራት እመቤታችን በአዳም መርገም ጥላ፤ በማኅፀነ ሐና በጥንተ አብሶ መፀነሷን እንደሚያምኑ በአደባባይ ገልጸዋል።[6]

የቅርቦቹ ግብጻውያን አበው ደጋግመው የሚገልጹት ከላይ የቀረቡትን አምስት ነጥቦች ስለ ሆነ ከዚህ በላይ አብረናቸው ብንቆይ አሳቡን ለማብራራት ካልሆነ በቀር የተለየ ነገር ስለማይነግሩን በዚሁ እንለናበታቸው።

## 3.3 እንጽሖ፡- በምሥራቅ ኦርቶዶክሳውያን አብያተ ክርስቲያናት

(3.3.1) በተለምዶ የምሥራቅ ወይም የግሪክ ኦርቶዶክሳውያን አብያተ ክርስቲያናት ከጥቂት ግብጻውያንና ሶርያውያን ጀምሮ ግሪክን፤ ራሺያን፤ ቆጵሮስን፤ ሰርቢያን፤ ቡልጋሪያን የመሳሰሉ ብዙኃን የምሥራቅ አውሮፓ ኦርቶዶክሳውያን አብያተ ክርስቲያናትን ያዳርሳል። አብያተ ክርስቲያናቱ "አንድ አካል፤ ሁለት ባሕርይ" በማለት ደንግጎ ቅዱስ ዲዮስቆሮስን ለግዞት የዳረገውን የቄልቄዶን ጉባኤ ስለሚቀበሉ[7] ደግማቸው "በተዋሕዶ አንድ

[6] አባ ሠረቀ ብርሃን ወልደ ሳሙኤል፤ እውነትና ንጋት፤ 2004 ዓ.ም.፡ ገ.64

[7] ሉሌ መላኩ፡ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ፡ገ.169፡፡ አቡነ ጎርጎርዮስ፤ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ፡ገ.154_ 160፡፡ "ኹለት ባሕርይ የሚሉት ልክ እኛ አንድ ስንል ልዩ አንድ እንደ ኾነና የንስጥሮስን ክሕደት ለመሬቅ እንደ ኾነ ኹሉ የእነርሱም ኹለት ቢሉም ልዩ ኹለት ነው፤ ይኸውም የአውጣኪን ክሕደት ለመሬቅ ነው፡፡ በዚህ ጉዳይ ላይ ያለን ልዩነት የቃላት አገላለጽ ባለፈ ውስጡ ምንም ልዩነት ያለው አይመስለም፡፡ የጉባኤ ኬልቄዶን ጉዳይ ከሃይማኖታዊ እንድምታው ይልቅ ፖለቲካዊ እንድምታው ያመዝናል" የሚሉም አሉ፡፡ የተካሄዱት ፐ/ር ጌታቸውም ከዚህ በምሥራቃውያንና ኦሪየንታል የጋራ ጉባኤያት በተደጋጋሚ የተነገረ ሁለት ባሕርይ ብሎ ንስጥሮስን ስለሚያወግዙ፤ የሚመሳሰል አቋም አላቸው፤ ምሥራቃውያኑ ሁለት ባሕርይ ብሎ እኛም አውጣኪን ስለምናወግዝ ቀና ልቡና ቢኖር የመግባባት እድል አለን ይላሉ፡፡ (ጌታቸው ኃይሌ፤ እንጻፍታ ሳውጋችሁ፤ 2006 ዓ.ም.፡ ገ.172-175፡፡)

አካል፤ አንድ ባሕርይ" ከምንለው ስድስቱ የኦሪየንታል አብያተ ክርስቲያናት ተለይቷል። ድንጋጌው በቁስጥንጥንያው ንጉሥ መርቅያን ጫና ስለ ፀደቀ "መለካውያን" ወይም ፈጸምያነ ፈቃደ ንጉሥ (አንዳንዴም ኬልቄዶናውያን) እንላቸዋለን። የግሪክ ወይም የምሥራቅ ኦርቶዶክሳውያን ስለ ጥንተ አብሶ ባላቸው አመለካከት ከአዳም መርገሙንና ቅጣቱን እንጂ ግላዊ ኃጢአቱን አልወረስንም እንደሚሉ ቀደም ሲል አይተናል (አሳቡን እኔም እርግት ለመቀበል በተዘጋጀ ልብ እጋራዋለሁ!) - "Because Adam sinned, all humanity shares not in his guilt but in the same punishment - በአዳም በደል የተነሣ የሰው ልጅ ሁሉ የሚጋራው በደለኛነቱን ሳይሆን ቅጣቱን ነው" የሚለውን አሳብ። ስለዚህ እነርሱ እንደሚሉት የካቶሊካውያን የጥንተ አብሶ ወይም ዐቀባ (preserved her) ዶግማ አላስፈላጊ ደጊመ ቃል (redundant) ነው። ምክንያቱም "በኦርቶዶክሳዊ እይታ እመቤታችን (ጥንቱን መርገምና ፍዳ እንጂ) መንጻት የሚጠብቅ ጥንተ አብሶ የለባትም - In Orthodox eyes, there is simply no original guilt for Mary to be made innocent of[8]

(3.3.2) የምሥራቅ /ግሪክ/ ኦርቶዶክሳውያን በጥንተ አብሶ ትርጓሜ ላይ ያላቸው አቋም ከካቶሊካውያንና ከግብጻውያን የተለዩ መሆናቸው እንደ ተጠበቀ ሆኖ እመቤታችን በመርገም ሥር ተወልዳ ከበደሉ ሳይሆን ከመርገምና ከፍዳው በብሥራተ መልአክ ጊዜ እንደ ነጻች ግን ያስተምራሉ - እንጽሐ! "ከጽንሰቷ ጀምሮ ከመርገም ተጠብቃለች የሚለው ዶግማ ከትውፊታችን ይጣረሳል፤ አባቶቻችን ካቆዩልን ብሒልም ይቃረናል፤ ምክንያቱም ትውፊታችን እንዳቆየልን፤ አባቶቻችንም እንደ ነገሩን እመቤታችን የነጻችው በማኅፀነ ሐና ሳይሆን ክርስቶስን ስትፀንስ ነው፤" ይላሉ - "This teaching [Immaculate Conception of St.Mary] contradicts ... Sacred Tradition, which is contained in numerous Patristic writings, where there is mentioned the exalted sanctity of the Virgin Mary from Her very birth, as well as Her cleansing by the Holy Spirit at Her conception of Christ, but not at Her own conception by Anna." በመቀጠልም "መንፈስ ቅዱስ ያነጻት

[8] http://www.antiochianarch.org.au/Orthodox-view-on-Immaculate-Conception.aspx



ከመርገም ብቻ ሳይሆን ከሴቶች ወርሐዊ ልማድም" እንደ ሆነ - He purified the female nature, rejected the bitter Eve and overthrew the laws of the flesh" ሲሉ ይጠቁሙናል።[9]

(3.3.3) የግሪክ /ምሥራቅ/ ኦርቶዶክሳውያን የእንጽሐ አመክንዮና መጽሐፋዊ መነሻ ባጭሩ በአምስት ክፍሎች ስለ ቀረበልን በወፍ በረር በራሳችን የቋንቋ ዘይቤ እናስቀምጠው።

(1) እመቤታችን ጥንቱን ስትጸነስ ከሐና እና ኢያቄም በሆነ ተራክቦ እስከ ሆነ ድረስ ከመርገሙ ልትነጻ አትችልም። በማኅፀነ ሐና ሳለች "መንፈስ ቅዱስ ዐቀባ" ካልን በብሥራተ መልአክ ጊዜ "መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ" መባሉ አላስፈላጊ ነበር ማለት ነው፤ ምክንያቱም ከማኅፀነ ሐና ጀምሮ የሚጠብቃት መንፈስ ቅዱስ ለብሥራቷ እንደ አዲስ መውረድ አይጠበቅበትም።

(2) በትውፊታችንም 'የእመቤታችን ጽንሰት እንበለ መርገም ነው' ብሎ ያስተማረ አባት አልሰማንም ይላሉ - ምሥራቃውያኑ።

(3) ንጹሐ ባሕርይ ክርስቶስ ምስጋና ለስሙ አጠራሩ ይሁንና ከመርገመ አዳም ነጻ ሆኖ እንዲፀነስ እመቤታችን ከማኅፀነ ሐና ጀምሮ እንበለ መርገም መፀነስ ነበረባት የሚለውን ብሒል ከተቀበልን የእርሷም ወላጆች በመርገም ሥር ሆነው እርሷ እንበለ መርገም ልትፀነስ ስለማትችል የእነርሱም ጽንሰት እንበለ መርገም ሊሆን ግድ ነበር፤ እንዲህ እያልን ከቀጠልን ደግሞ 'ክርስቶስ ሥጋ እንዲለብስ ሥጋ ለባሽ አበው ሁሉ እስከ አዳም ድረስ እንበለ መርገም መፀነስ አለባቸው' የሚል አዙሪት ውስጥ ልንወድቅ ነው ሲሉ ይሞግታሉ።

(4) ሙግታቸውን በመቀጠል ጌታ እመቤታችንን ብቻ ከሰው ልጆች ነጥሎ 'ዐቀባ፡ እምከርሠ፡ እሙ' ከተባለ 'ፈታሒ በጽድቅ ዘኢያደሉ ለገጽ' እያልን ለእውነተኛ ዳኝነቱ የምንሰጠው ቅጽል ሊፋለስብን ነው። ምን ነው? ቢባል 'እርሷን ለይቶ ከማኅፀን ጀምሮ ከመርገምና ፍዳ ካነጻት መንጻቱ ለሰው ዘር ሁሉ ይደርስ ነበር። ጭራሹን እንዲያ ማለት የሰው ዕጣ ፈንታ አስቀድሞ እንደ ተወሰኑና ሳይወለዱ የዳኑ እንዳሉ ማስመሰል ነው' ሲሉ - ይከራከራሉ።

[9] Archbishop John Maximovitch:The Orthodox Veneration of Mary the Birthgiver of God, p.21

(5) በመጨረሻም ከማኅፀነ ሐና ጀምሮ ንጹሕ ሆና ተፈጠረች ካልን የእርሷን ትሩፋትና ምግባረ ጽድቅ ማቃለላችን ነው፤ ጌታ መንፈስ ቅዱስ ከኃጢአት ከጠበቃት በራሷ ጥረት የሠራችው ትሩፋት የለም ሊባል ነው። እንደ እርሱ ደግሞ አያስኬድም፤ "አልቦ፡ ክብር፡ እንበለ ኃሳር - There is no victory without an adversary" ሲሉ ይደመድማሉ።[10]

## 3.4 እንጽሐ፦ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት

ጥንተ አብሶ ከቃሉ ጀምሮ በኢትዮጵያውያን ሊቃውንት ዘንድ ያን ያህል አከራካሪ ሆኖ የኖረ አይመስልም። ጥንተ አብሶ በሊቃውንት መካከል በስፋት ማነጋገር የጀመረው ካለፉት አርባ ዓመታት ወዲህ ይመስላል። አነጋጋሪነቱ ቅድስት ሥላሴ መንፈሳዊ ኮሌጅ ተከፍቶ የኮሌጁ ምሩቃን በተለያዩ የምሥራቅ፣ የኦሪየንታል እና የምዕራብ የሥነ መለኮት ኮሌጆች የመማር ዕድል ከማግኘታቸው ጋር ሳይያያዝ አይቀርም። ከሞላ ጎደል ሁሉም ሊባል በሚችል ደረጃ የ"እንጽሐ" ብሒልን ደግፈው የቆሙ ሊቃውንት ወይ በእነዚህ አህጉራት ተምረዋል፤ አልያም ቢያንስ ኖረዋል። ነባሩ ኢትዮጵያዊ ትውፊት ወደ "ዐቀብ" ያጋደለ ነው፤ የምእመኑና የሊቃውንቱ መንፈስም እንዲሁ። ባሕር ተሻግረው የተማሩ ጥቂት ሊቃውንት በእንጻሩ ወደ ኦሪየንታል አብያተ ክርስቲያናት በማጋደል ከካቶሊካዊ አስተምህሮ ለመሸሽ (በውጭው ባሉ እኅት አብያተ ክርስቲያናት ወንድሞች ፊት "ካቶሊካውያን" ላለመባል) "እንጽሐ"ን እንደ ኦርቶዶክሳዊ ብሒል ወስደው በአደባባይም ባይሆን በጽሑፎቻቸው ፊራ ተባ እያሉ አስፍረዋል። በሞተ ሥጋ በተለዩን ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ጀምረን በተራ እንያቸው!

(3.4.1) ነፍስኄር ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ በቃል ባይናገሩትም በዶክትሬት ማሙያ ጥናታቸው ለእንጽሐ ብሒል ወግነው ሲጽፉ እናገኛቸዋለን። በጥናታቸው መግቢያ፣ በገጽ 147 እና 306 የእንጽሐ ብሒል ደጋፊነታቸው በለዘበ እንግሊዝኛ ተቀምጠዋል። በገጽ 147 "She is not immaculate in the sense that she was born without sin, but in

[10] Ibid; p.21-23



the sense that she was specially prepared by the Holy Ghost - ንጽሕት ናት ማለት እንበለ አበሳ ተወልዳለች በሚል መንፈስ ሳይሆን በተለየ መልኩ በግብረ መንፈስ ቅዱስ (ለአምላክ ማደሪያነት) ተዘጋጅታለች (ነጽታለች) ማለት ነው" ሲሉ በብሥራት መልአክ ጊዜ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነጽታለች ብለው እንደሚያምኑ ፍንጭ ይሰጡናል። ይቀጥላሉ፦ "For the Ethiopian Orthodox Church the Virgin Mary is the example par excellence of obedience and faithfulness to God. She is two-fold Virgin, i.e, Virgin both in body and soul, who, though not 'immaculate' or free from Original Sin, yet was all-holy, pure and chose to actively participate in the saving work of God,his incarnation" ይላሉ።[11]

(3.4.2) ከላይ ያለው ጥቅስ ጠቅለል ብሎ በግርድፉ ሲተረጎም፦ "እንደ ኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ድንግል ማርያም ለእግዚአብሔር የመታዘዝና የማእምንትነት (አማኝነት) አርአያ ወአምሳል ናት። እመቤታችን በሁለት ወገን ድንግል ናት፤ በሥጋም በነፍስም። ጽንሰቷ እንበለ አበሳ አዳም ነው ወይም 'ከጥንተ አብሶ ነጻ ናት' ባንልም ቅሉ ቅድስተ ቅዱሳን፣ ንጽሕት፣ በእግዚአብሔር የማዳን ሥራና በሥጋዌው ሱታፌ ያላት ናት፤" ይሉናል። እዚህ ላይ አባታችን እንደ ጸሐፊ ሁለት ቅር የሚያሰኙ ነገሮችን ፈጽመዋል ብዬ አምናለሁ።
(1) ከላይ የተገለጸው መደምደሚያ ላይ ሲደርሱ በምንጭነት የተጠቀሟቸውን የቤተ ክርስቲያን መጻሕፍት መጥቀስ ነበረባቸው፤ አልጠቀሱም።
(2) ስለ ጉዳዩ ምንም ዓይነት ሲኖዶሳዊ አቋም ወይም አዝማሚያ ባልነበረበት ጊዜ (እ.ኤ.አ 1988 ዓ.ም.) በገዛ ሥልጣናቸው "For the Ethiopian Orthodox Church the Virgin Mary is ... - እንደ ኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ድንግል ማርያም..." እያሉ እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት የሚለው የእንጽሐ ብሒል በሲኖዶስ የፀደቀ ወይም በትውፊት የታወቀ የቤተ ክርስቲያኗ አቋም እንደ ሆነ አድርገው መጻፋቸው ቅር ያሰኛል። ደግነቱ ፓትርያርክ ከተቀመጡ ወዲህ በቤተ ክርስቲያኗ ላይ ርእሱን በመንዘረ ከመምከር ይልቅ ውሳኔውን ለሊቃውንት ትተውታል። ይህን ዝቅ ለመመኘን ብለን እንመለስበት።

[11] Aba Paulos: Filsota; p.306

(3.4.3) ሌላኛው በእንጽሐ ብሒል መስመር ተሰልፈው የጻፉ ሊቅ የሊቃውንት ጉባኤ ሰብሳቢ የነበሩት መጋቤ ብሉይ ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስ ናቸው። መጋቤ ብሉይ የእመቤታችንን ቅድመ ጸኒስና ድኅረ ጸኒስ በሁለት ወገን ማለትም በሥጋም በነፍስም ድንግል መሆን፣ በሐልዮ፣ በነቢብና በገቢር ከኃጢአት የንጻች ፍጽምት መሆን፣ ክብርና ምስጋና እንደሚገባት፣ መልዕልተ ፍጡራን፣ መትሕተ ፈጣሪ መሆኗን፣ ወላዲተ አምላክነቷን፣ አማላጅነቷን፣ ትንግሊዋንና ዕርገቷን በሰፊው ያትታሉ። ጥንተ አብሶን በሚመለከት ግን፣ "አንዳንዶች እመቤታችን አድፎ የነበረው የአዳም ጠባይ ወይም ጥንተ አብሶ እንደሌለባት ያስተምራሉ፤ ነገር ግን ይህ ትምህርት በኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችን ተቀባይነት የለውም፤ ምክንያቱም እመቤታችን ከኢያቄምና ከሐና በሩካቤ ዘበሕግ የተገኘች ናት፤ ካሣ የማያስፈልጋትም ሳትሆን ክርስቶስ በደሙ ከዋጃቸው ካሣም ከተከፈለላቸው ወገን ናት፤ ሆኖም እንደ አዳምና ሔዋን የምኞት የመናገርና የገቢር ኃጢአት ፈጽሞ የለባትም፤" ብለው ጽፈው ነበር።[12] ሆኖም መጽሐፉ በዚሁ ይዘቱ የተነሣ በቅዱስ ጳውሎስ መንፈሳዊ ኮሌጅ ተማሪዎች ለቅዱስ ሲኖዶስ ቅሬታ ቀርቦበት ቅሬታው በጊዜው በአለቃ አያሌው ታምሩ ሰብሳቢነት ይመራ ወደ ነበረው የሊቃውንት ጉባኤ ከተላለፈ በኋላ መጽሐፉ ከስርጭት እንዲቋረጥ ተወስኗል።[13] እንደ አቡነ ጳውሎስ ሁሉ መጋቤ ብሉይም ምንጭና በጉዳዩ ላይ እንደ ኢ/ኦ/ተ/ቤ/ክ. ለመናገር የሚያስችል መነሻ ሳይጠቁሙን አቋማቸውን የተቋሚ አቋም አድርገው ማቅረባቸው ቅር ያሰኛል። በ1990ዎቹ በመጋቤ ብሉይ ሰይፈ የአጭር ጊዜ ሥልጠና የመውሰድ ዕድል ገጥሞኝ ጥያቄው ተነሥቶላቸው መልስ ሳይሰጡበት አልፈዋል። ኋላ ወደ ዐቀባ ቡድን ስንሔድ እንደምናየው ግን መጋቤ ብሉይ ይኼን ጽሑፍ ካወጡበት ጊዜ በፊትም ሆነ በኋላ "ዐቀባ" የሚለውን ወገን ወግነው የተሰለፉበት አጋጣሚም አለ።

(3.4.4) ግብጽ እና ግሪክ የተማሩ የአገራችን የሥነ መለኮት ሊቃውንት በጥንተ አብሶ ጉዳይ የተማሩበትን አገር ብሒል ወርሰው እንደሚመለሱ በንዑስ ርእሱ መግቢያ ገልጫለሁ። ዓሥራት ገብረ ማርያም ከዚህ ብሒል ደጋፊዎች መካከል መሆናቸውን በ1983 ዓ.ም. ባሳተሙት ትምህርተ

---

[12] መ/ብ ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስ፣ መሰረተ ሃይማኖትና የካሕናት ተልእኮ፣ 1982 ዓ.ም፡ ገ.29
[13] ሥምረት አያሌው ታምሩ፣ አባቴና እምነቱ፣ 2007 ዓ.ም.፡ ገ.117



መለኮት መረዳት ይቻላል፤ ሆኖም የ1983 ዓ.ም. አቋማቸውን በ1991 ዓ.ም. እትም ከመጽሐፋቸው ፍቀው ከ"እንጽሐ" ቡድን ገሸሽ ብለዋል። 'ሞኙና ወረቀት...' እንዲሉ የመጀመሪያዋ አሳባቸው ለታሪክም ቢሆን ተሰንዳለች። እናቅርባት! "በቤተ ክርስቲያን እምነት መሠረት በሉቃ.1:38 ላይ (እመቤታችን) የመልአኩን ብሥራት ተቀብላ 'እነሆኝ የጌታ ባሪያ እንደ ቃልህ ይሁንልኝ' ብላ እምነቷን በእግዚአብሔር ላይ ባሳረፈች ጊዜ ጌታን ከመውለድዋ በፊት መንፈስ ቅዱስ እመቤታችንን ቀድሶና አንጽቶ 'የጥንቱን የአዳምን ኃጢአት አስወግዶላታል'። ...በሌላ በኩል ደግሞ የቀድሞው የአዳም ኃጢአት የሚወረሰው በወንድ ዘር አማካይነት ልጅ በሚወለድበት ጊዜ ከአባት ወደ ልጅ በመሆኑና ጌታ ግን የተወለደው 'መንፈስ ቅዱስ የጥንቱን ኃጢአት ካስወገደላት' ከእናት ብቻ ስለ ሆነ ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን የጥንቱን የአዳም ኃጢአት አልወረሰም" /አጽንዖቱ የኔ ነው/።[14] ይህ ጥቅስ ያለበትን ገብጻዊ ቃና ከላይ አቡነ ሺኖዳ ካቀረቡት ትንታኔ ጋር በማነጻጸር በቀላሉ መረዳት ይቻላል፤ ተወራራሽ ነው።

(3.4.5) ሌላኛው የግሪክ ተማሪ የኔታ ዓለማየሁ ሞገስ በ1987 ዓ.ም. በታተመ "ሁሉም ሁሉን ይወቅ" የተሰኘ መጽሐፋቸው ጥንተ አብሶ አለባት የሚለውን አሳብ እንጸባርቀዋል። እንደ እውነቱ ይኼ መጽሐፍ ጥንተ አብሶውን ትተን ባነሣቸው ሌሎች የቀኖና እና የዶግማ ጽንሰ አሳቦችም ብዙ ሕጸጾች የነበሩበት ነው። ለእርሱ (እስመ ጎጻም፣ ለጎጻም ፀሩ! እስከንል ድረስ) መምህር ኪዳነ ማርያም ጌታሁን ምላሽ ስለ ሰጡ መነካካት አያስፈልግም፤ የኔታ ዓለማየሁ ጥንተ አብሶ ስለ ጥንተ አብሶ የጻፉትን ብቻ እጠቅሳለሁ። የኔታ ዓለማየሁ ጥንተ አብሶ ስለ ጥንተ አብሶ የጻፉትን ብቻ እጠቅሳለሁ። "...ዘለዓለማዊ አልነካትም የሚሉ ወገኖችን መከራከሪያ ወረፍ ካደረጉ በኋላ "...ዘለዓለማዊ ድንግልናዋ በነቢያት ሲነገር ከጥንተ አብሶ ግን ነጻ ናት ያለ አንድም ነቢይ ስለ ሌለ መልአኩም መንፈስ ቅዱስ ይጸልልሻል ብሎ እንደሚያነጻት ተናገረ ስለ ሌለ መልአኩም መንፈስ ቅዱስ ይጸልልሻል ብሎ እንደሚያነጻት ተናገረ? ስትለው ስለ ያለጥንተ እንጂ እኔ ወንድ አላውቅም እንዴት ይሆንልኛል? ስትለው ስለ ያለጥንተ አብሶ መወለዱን ለመናገር ምቹ ጊዜ ሳለው የመንፈስ ቅዱስን ማንጻት ተናግሮ ነው ያለፈው፤" ይሉናል።[15] በመቀጠልም "እንጺሖ ሥጋሃ፣ ቀዲሶ ኪያሃ ... ነፍሳ ቀድስከ ወሥጋሃ አንጻሕከ" የመሳሰሉ ቃላትን ከድጓ፣

---

[14] ዓሥራት ገብረማርያም፣ ትምህርተ መለኮት፣ 1983 ዓ.ም.፡ ገ.96
[15] ዓለማየሁ ሞገስ፣ ሁሉም ሁሉን ይወቅ፣ 1987 ዓ.ም.፡ ገ.157

ከዝማሬ፣ ከቅዳሴ ያዕቆብ ዘሥሩግ፣ ከሃይማኖተ አበው ዘጎርጎርዮስ፣ ከግብረ ሕማማት ስትግቡዕ በማድረግ (በማሰባሰብ) እንዲሁም በእመቤታችን ሐረገ ትውልድ ወደ ላይ የሚቈጠሩት እንደ ዳዊትና ሰሎሞን ዓይነት ነገሥታት አመንዝሮች ስለ ነበሩ እርሷ በየትም አልፋ ከጥንተ አብሶ ልትነጻ እንደማትችል እያተቱ ይከራከራሉ። በምንባባቱ ላይ እመለስባቸዋለሁ። የኔታ ዓለማየሁ ክርክራቸው ሥሩ ግሪካዊ ቢሆንም በአገር ውስጥ የትውፊት ማስረጃ ለመደገፍ መሞከራቸው መልካም ጅምር ነው። ስማቸውን ለመጥቀስ ይፍሩ እንጂ አብዛኞቹ የዛሬ ዘመን የአንጽሐ ቡድኖች ማጣቀሻ እርሳቸው ናቸው። የአባ ሠረቀ እና የቀሲስ አስተርአየ የአንጽሐ መከራከሪያዎች የየኔታ ዓለማየሁ ሞገስ ተጽዕኖ ያለባቸው ሆነው ይታዩኛል።

(3.4.6) የግሪክ ተማሪዎች ቀጥለዋል! መቼም ምንም አልን ምን፣ አቡነ መልከ ጼዴቅ ለኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ሥነ ጽሑፍ እና የስብከት ዘዴ ያበረከቱትን ትሩፋት መካድ ይከብዳል። በግሌ ይኼን ሳልመሰክር ባልፍ የምወደው አባቴ አርጌ መደርደሪያ ላይ ከማንም ጳጳስ በላይ የተደረደሩት ቀደምት መጻሕፍቶቻቸው ይወቅሱኛል። በተወሰኑ ባሕርያቶቻቸው፣ ንግግሮቻቸው፣ ጽሑፎቻቸውና እርምጃዎቻቸው ቅሬታ ቢኖረኝም ቅሬታዬ ትውልድ ተሻጋሪ አሻራዎቻቸውን እንዳላይ እንዳልፍ አያስችለኝም። አከብራቸዋለሁ። አሁን ስለ ጥንተ አብሶ ወደ አነሡት ነጥብ ልሻገር። አቡነ መልከ ጼዴቅ የአንጽሐ ብሒል በኢትዮጵያ አገር እንዲተከል አድርገዋል የሚል ሐሜታ ይሰነዘርባቸዋል። እርግጥ በሥራዎቻቸው በግልጽ "እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት!" ብለው እንደ ሳይኞቹ ጸሐፍያን አያስፍሩም። ነገር ግን ስለ ጥንተ አብሶ ሲተርኩ "ሮሜ.5:14 'የበደለውንም ያልበደለውንም ሞት ገዛው፤' አለ እንጂ አገሴና አገሲት ብቻ ወይም ከአገሴና ከአገሲት በቀር ብሎ ለይቶ የተናገረለት የለም" ሲሉ እመቤታችንን ለይተው ሳያወጡ በኢርቱዕ (ቀጥተኛ ባልሆነ) አገላለጽ ቀላቅለው ያልፏታል።[16] ከጊታ ልደት በተገናኘ ስለ እመቤታችን ሲገልጹም "ቅድስት ማርያምን መንፈስ ቅዱስ አንጻት፤ ቀደሳትም፤ እንዲሁም አካላዊ ቃልን በማኅፀኗ ትሸከመው ዘንድ አፀናት፤ አስቻላት፤ ሁሉን ለማድረግ ችሎታ ያለው መንፈስ ቅዱስ ነውና ጸለላት፤ ማለትም በድንግልና ፀንሳ በድንግልና እንድትወልድ

[16] አባ መልከ ጼዴቅ፣ የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ እምነትና ሥርዓት፣ ገ.146



አደረጋት። ጸለላት… አነጻት … ቀደሳት ማኅደረ መለኮት እንድትሆን አዘጋጃት፤" ሲሉ በ1984 ዓ.ም. ያወጡትን "ትምህርተ ክርስትና ፡ ሁለተኛ መጽሐፍ" አሳብ በ1994 ዓ.ም. ባሻሻሉበት መጽሐፋቸው ገጽ 155 አጽንተውታል።

(3.4.7) አቡነ መልከ ጼዴቅ የቅዱስ ጳውሎስ መንፈሳዊ ኮሌጅ ዲን ሳሉ እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት ብለው አስተምረዋል የሚል አቤቱታ ለቅዱስ ሲኖዶስ ቀርቦ ጳጉሜ 2 ቀን 1984 ዓ.ም. ጵጵስናቸውን እስከ መያዝ ተኪዶ እንደ ነበር በምስል ታግዘው የተሰቀቁ መረጃዎች ይጠቁማሉ።[17] ስማቸው እንዳይጠቀስ የሚፈልጉ የቀድሞ ተማሪያቸው እንዲሁ አቡነ መልከ ጼዴቅ እመቤታችን ከጥንተ አብሶ ነጻ ናት ከማለት ይልቅ በቃል ሲያስተምሩ "አለባት" ወደሚለው አጋድለው እንደሚያስተምሩ፣ በሌላ በኩል በጽሑፎቻቸው "አለባት"ም "የለባት"ም ሳይሉ በተዘዋዋሪ ግን "ከክርስቶስ በቀር ያለጥንተ አብሶ የተፀነሰ የለም" በማለት እንደሚጽፉ፣ ለምን እንዲህ አሉ የሚል ወቀሳ ሲደርስባቸው "የታለ 'አለባት' ብዬ የጻፍኩት?" እያሉ ይከላከሉ እንደ ነበር ይናገራሉ። የጥንተ አብሶ ጉዳይ አነጋጋሪ በነበረበት በ1985 ዓ.ም. የወጣው የቤተ ክህነቱ ማዕዶት መጽሔት አቡነ መልከ ጼዴቅን ለመንካት በሚመስል መልኩ "ቅዱስ ያሬድ 'እንዚአ፡ ሥጋሃ፣ ቀዲሶ፡ ኪያሃ፤ ኀደረ ላዕሌሃ - ሥጋዋን አንጽቶ ቀድሶ በእርሷ ላይ አደረ' ያለው እርሷ የለበሰችው አካለ ሥጋ ርስሐት [የኃጢአት ጉስቁልና] ኑሮበት ሳይሆን ጥንተ መሠረቷ የነጻ የውርስ ኃጢአት የሌለባት ንጽሕት ድንግል መሆኗን ነው። የመናፍቅነት ውርስ ኃጢአት በዘር የተላለፈባቸው ጸረ ማርያሞች በንጽሐ ድንግልናዋ ላይ ያላቸው ጥርጣሬ እስከ መቼ ድረስ ይወገድ ይሆን?!" ሲል አቡኑ ላይ አዳንቆ ጽፎባቸዋል።[18]

(3.4.8) የአንጽሐ ወይስ ዐቀባ ክርክር ያሲጋው ቅዱስ ሲኖዶስ በብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ የበላይ ጠባቂነት ሊቃውንትና ጳጳሳት የተካተቱበት ንባቤ አዋቅሮ በ1988 ዓ.ም. "መንፈስ ቅዱስ ዐቀባ እምከርሠ እም" የሚል ወይም

[17] https://www.youtube.com/watch?v=Yons6s314rc https://www.facebook.com/1505173966444656/videos/vb.1505173966444656/1520922464869806/?type=2&the

[18] መ/ር ዳንኤል ዓለሙ፣ 1985 ዓ.ም.፣ ማዕዶት፣ ቍጥር 38፣ ገ.55-56

መንፈስ የተከተለ የዶግማ መግለጫ መጽሐፍ በአማርኛና እንግሊዝኛ እንዲወጣ ሆነ። ሆኖም መጽሐፉ በወቅቱ እጅግ ተሰሚ የነበሩት አለቃ አያሌው ታምሩ ከአቡነ ጳውሎስና ከቤተ ክህነቱ ተጋጭተው ቅዱስ ሲኖዶስን ሳይቀር ያወገዙበት ጊዜ ነበርና የታሰበውን ያህል እንዳይነበብ ሆነ። ክርክሩም ቡታና ሰው ቀይሮ ቀጠለ። በተለይ በ1997 ዓ.ም. በአሜሪካ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ማኅበረ ካህናት" በተሰኘ የካህናት ጉባኤ የእንጽሐ ብሒል በይፋ መድረክ ወጥቶ በመሰበኩ ውዥንብር ተፈጠረ። ማኅበረ ካህናቱ በአንድ በኩል ከኢትዮጵያ ሲኖዶስ ውሳኔ አሳብ ጠይቀው እርሱ ሲዘገይ ወደ ግብጽ ሳኩና የአቡነ ሺኖዳ ብሒል "እንጽሐ" ነው፤ የእኛም እንዲያ ነው ማለት ቃጣቸው። "አነጻት ... አዘጋጃት" የሚል ምንባብ ያለባቸው ከላይ የተጠቀሱት ኢትዮጵያውያን ሥራዎችን ጨምሮ የአለቃ አያሌውን ወላዲተ አምላክ በኢትዮጵያ[19] እና የመልአከ ብርሃን አድማሱ ጀንበሬ መድሎተ አሚን[20] እግረ መንገድ የተነሡ ሐረጋትን በመጥቀስ ለእንጽሐ በመወገን ይጻፍ፣ ይሰበክ ጀመር።

(3.4.9) የእንጽሐ ብሒል ደጋፊ ወገኖች ከጠቀሷቸው ተደጋጋሚ የመጻሕፍት ምንባባት የተወሰኑትን እንደ ወረዱ እናቅርባቸው፦

(1) "... [መዝ.131:7] የሚያስተምረን እግዚአብሔር ማደሪያ ላደረጋቸው ለቅዱሳን ይልቁንም መርጦ ከኃጢአት አንጽቶ በመንፈስ ቅዱስ ቀድሶ ሥጋዋን ለተዋሐዳት ለእመቤታችን ድንግል ማርያምና ለተሰቀለበት መስቀል እንድንሰግድ ነው።"[21]

(2) "...መብሥር መልአክ ገብርኤል ወደ እመቤታችን... መጥቶ 'መንፈስ ቅዱስ ያድርብሻል፤ የልዑል ኃይልም ይጸልልሻል...' አላት። በዚህ ቃል... ሥጋዋም ነፍስዋም በመንፈስ ቅዱስ ተቀደሰ፤ አዲስ ሕይወት አገኘ፤ ...ለእግዚአብሔር እናት በመሆን ታደለች፤ በዚህ መሠረት 'ሰውነቱ በአምላኬ በመድኃኒቴ ደስ ይላታል' ብላ ለመናገር በቃች። ሉቃ.1:35-46።"[22]

(3) አባ ጳውሊ የተባለ ኢትዮጵያዊ ልዮን ለተባለ ካቶሊካዊ "ክርስቶስ አምላክ የሆነው ከጥምቀተ ዮርዳኖስ ወዲህ ነው!" ብሎት የመለሰውን መልአከ

[19] አለቃ አያሌው፤ ወላዲተ አምላክ በኢትዮጵያ፤1979 ዓ.ም.፡ ገ.27
[20] መልአከ ብርሃን አድማሱ ጀንበሬ፤ መድሎተ አሚን ገ.15-16
[21] ሊቀ ጠበብት አያሌው ታምሩ፤ የኢትዮጵያ እምነት በሦስቱ ሕግጋት፤ 1953 ዓ.ም.፡ ገ.205
[22] አለቃ አያሌው ታምሩ፤ ወላዲተ አምላክ በኢትዮጵያ፤ ሐምሌ 1979 ዓ.ም.፡ ገ.27



ብርሃን አድማሱ በመድሎተ አሚን ገጽ 16 ሲገልጹ አብ ለአጽንዖ፣ ወልድ ለለቢሰ ሥጋ፣ መንፈስ ቅዱስ ለአንጽሖ በእመቤታችን እንደ አደሩ ከተናገሩ በኋላ ቀጥለው ሲያብራሩ "አብ ለአጽንዖ ማለትም፦ ሰማይ ምድር የማይወስኑትን ምሉዕ፣ ስፉሕ፣ ረቂቅ መለኮትን እመቤታችን በጠባብ ማኅፀን እንድትችለው አፀናት ማለት ነው። መንፈስ ቅዱስ ለአንጽሖ ማለትም፦ ትስብእትን ከአዳም መርገም አንጽቶ ቀድሶ ለተዋሕዶተ መለኮት የበቃ አደረገው ማለት ነው።... እንጂ... ሠላሳ ዘመን መንፈስ ቅዱስ ተለይቶት ኖሮ በዮርዳኖስ አደረበት ማለት አይደለም አለ። (ያ! ሮማዊ መልስ አጥቶ ዝም አለ)።" ይህቺን በምሥጢረ ሥጋዌ አንጻር የተጻፈች ምንባብ ተሐድሶዎች እንዳልሆነ አድርገው አጣምመዋታል - ጊላ እንምጣበት!

(4) ከሃይማኖተ አበው "መንፈስ ቅዱስ አንጽሐ ሥጋሃ ለማርያም፣ ወረሰያ ድሉተ ለተወክፎ ቃለ አብ... መንፈስ ቅዱስ የማርያምን ሥጋ አነጻ፤ ቀደሰ፤ የአብ አካላዊ ቃልንም ለመፅነስ የበቃች አደረጋት። ማቴ.1:18-21። ሉቃ.1:34-37።"[23]

(5) ከቅዳሴ "...ገሊላዊት ሐቀፈተከ... ነፍሳ ቀደስከ ወሥጋሃ አንጻሕከ... ገሊላዊት አቀፈችህ፤ ነፍስዋን አከበርህ ሥጋዋንም አነጻሕ።"[24]

(6) በድጓ በተለይም በነሐሴ ኪዳን ምሕረት ድጓ ከገጽ 381-389 ብቻ "አንጺሖ ሥጋሃ፣ ቀዲሶ ኪያሃ፣ ኃደረ ላዕሌሃ፣ ወተወልደ እምኔሃ" የሚሉ ሐረጋት በብዛት አሉ።

(7) የግብረ ሕማማት የሐሙስ 9:00 ሰዓት ምንባብ ላይ እንዲሁ በኢሳይያስ 61 ስለ ቅብዕ የተነገረ ቃል "ይተረጐም በእንተ ቅብዐት ካዕበ በመንፈስ ቅዱስ ዘወረደ ላዕለ ማርያም ወአንጽሐ ሥጋ ዚአሃ፤ ለተወክፎ አምላክ... ቀብቶ ሳከኝ የሚለው... አካላዊ ቃል አምላክን በድንግልና ለመፅነስ እንድትችል በድንግል ማርያም ላይ በወረደው ከሦስቱ ግብራትም 'በከለከላት' መንፈስ ቅዱስ ስለ ሆነው ተዋሕዶ ይተረጐማል" ይላል።[25]

[23] ሃይማኖተ አበው ዘጎርጎርዮስ፡ ገ.125
[24] ቅዳሴ ያዕቆብ ዘሥሩግ ቁ 21፡ ገ.393
[25] ግብረ ሕማማት፤ 2005 ዓ.ም.፡ ገ.518

ስለ እንጽሖ ብሒል የሚከራከሩ የአሜሪካ ኗሪ ኢትዮጵያውያን ቀሳውስት ከላይ ያሉትን ምንባባት በመጥቀስ ተቺዎቻቸውን ሞገቱ፤ ብዙኃኑ ቢያፈገፍጉም የተወሰኑት ዛሬም ይሞግታሉ።

(3.4.10) በዚህ ሒደት የአሁኑ ፓትርያርክ ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ማትያስ ዐቀባ ለሚለው ብሒል በመቅናት የአንጽሖን ብሒል በድፍረት ሰብከዋል ያሏቸውን ቀሲስ አስተርአየ ሥልጣነ ክህነት ያዙ። ውዝግቡ ናረ፤ የሁለቱም ብሒል ደጋፊዎች አለን የሚሉትን ሁሉ ወረወሩ። የሚገርመው በ1988 ዓ.ም. "እመቤታችን ጥንተ አብሶ የለባትም" የሚለው መግለጫ በሲኖዶስ ትእዛዝ በተቋቋመው ኮሚቴ ቀርቦ ሲጸድቅ (የኮሚቴው) አባል የነበሩት አባታችን ብፁዕ አቡነ ገብርኤል በዚህ እሰጥ አገባ ወቅት በተሳትፎ ያጸደቁትን መግለጫ ተተው፦

(1) እመቤታችን ጥንተ አብሶ እንደሌለባት ነቢያትና ሐዋርያት ስላልተናገሩ፣
(2) ሲኖዶሳችን ስላልወሰነ፤
(3) የእኅት አብያተ ክርስቲያናት በተለይ ግብጽ "ከበረባት፤ ግን አነጻት" ስለምትል የዶግማ አንድነታችን እንዳይፋለስ "አንጽሖ" ብንል ይሻላል የሚል አንድምታ ያለው ጽሑፍ ከአቡነ ጳውሎስ ባለመስማማት በሔዱባት አሜሪካ በ1997 ዓ.ም. አስነበቡ። በራሺያ ፒ.ኤች.ዲ የሠሩትና 'የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን የሥርከ ስብከተ ወንጌል ጉባኤ አባት' ሊሰኙ የሚችሉት የአቡነ ገብርኤል ትንታኔ ለአሜሪካው የአንጽሖ ቡድን ታላቅ ቡራኬ ተደርጎ ተወሰደ።[26]

(3.4.11) ዘግየት እሉና ቀሲስ አስተርአየ ፅጌ በአቡነ ማትያስ የተላለፈባቸውን ውግዘት በነፍስ ኄር አቡነ ይስሐቅ አስፈትተው ከኤርትራም እንደ እርሳቸው "አንጽሖ" እያሉ በይፋ ከሚያስተምሩት አቡነ መቃርዮስ ግንባር ፈጥረው በጽሑፍ፣ በድምፅና በምስል የአንጽሖን ብሒል ለማስረጽ ከሚሊኒየሙ መባቻ ጀምሮ ይደክሙ ጀመር። ከግራ ቀኙ የሚመጣባቸው ነቀፌታ በመበርከቱ የተነሣ ወደ ጽርፈቱ ቢያጋድሉም ለሐሳባቸው አስረጅ ለመጥቀስ አልቦዘኑም። ለምሳሌ፦ "ቡርክት አንቲ እምአንስት - ከሴቶች መካከል

[26] አባ ሠረቀብርሃን፡ ገ.67



የተባረክሽ ነሽ" የሚለውን የመልአኩ ቃል "እመቤታችን ከእርሷ በፊትና ከእርሷ በኋላ ካሉት ሴቶች የተለየችው ከዚህ በታች በሰፈሩት ምስክሮች እንጅ ያለጥንተ አብሶ ተጸንሳ በመወለዷ አይደለም።

ሀ. ገብርኤል 'አንቺ ከሴቶች መካከል የተባረክሽ ነሽ' (ሉቃ.1፡28)
ለ. ራሷ እመቤታችን 'ወንድ ሳላውቅ እንዴት ይሆናል' (ሉቃ.1፡34)
ሐ. ኤልሳቤጥ 'አንቺ ከሴቶች መካከል የተባረክሽ ነሽ' (ሉቃ.1፡42)
ከሦስቱም የመነጩትን ምስክሮች አባቶች የሚተረጉሙት 'ልማደ አንስት' ማለትም ሴቶች ጽንሶ ለመውለድ ከሚያስፈልጋቸው የተፈጥሮ ሕግ ውጭ በመሆኗ ገብርኤልም ኤልሳቤጥም 'ከሴቶች የተለየሽ ነሽ' እያሉ ተናገሩ እንጅ ከሰው የተለየሽ ነሽ አላሉም" ሲሉ በኢንተርኔት በለቀቁት ጽርፈት በርከት ብሎ የታየበት ጽሑፋቸው ተከራክረዋል።[27] አክለውም ከላይ ለአንጽሖ ከነ ወግነው የጻፉ ኢትዮጵያውያን ሊቃውንትንና እኅት አብያተ ክርስቲያናትን ከነ መከራከሪያዎቻቸው ምስክር ቈጥረዋል። ምስክርነት ከቈጠሯቸው ሊቃውንት መካከል አለቃ አያሌው "ቀሲስ አስተርአዩ ያላሉትን አሉ" ሲሉ በግላጭ ተቃውመዋል።[28] ቀሲስ አስተርአየ እንደሚሉት እመቤታችን ከእኛ የምትለየው ያለጥንተ አብሶ በመወለዷ ሳይሆን፦
(1) የኀልዮ፣ የነቢብና እና የገቢር ኃጢአት (ምልአተ ኃጢአት) ስለሌባት፣
(2) በእግዚአብሔር በመመረጧ፣
(3) በዘለዓለማዊ ድንግልናዋ እና
(4) የአምላክ እናት በመሆኗ ነው።

(3.4.12) ወደ አገር ውስጥ ስንመለስ የአሜሪካው ማኅበረ ካህናት አባልና የአንጽሖ ብሒል ደጋፊ የነበሩት አባ ሠረቀ ብርሃን ወልደ ሳሙኤል የአንጽሖ ብሒል ደጋፊ የነበሩት ሰንበት ትምህርት ቤቶች ማደራጃ ኢትዮጵያ ገብተው የጠቅላይ ቤተ ክህነት ሰንበት ትምህርት ቤቶች ማደራጃ መምሪያ ኃላፊ ሆኑ። ከማኅበረ ቅዱሳን ጋር ተጋጩ። እርሳቸው ግጭቱ 'የማኅበሩ ሕግና መዋቅር ያልጠበቀ አካሔድ የወለደው ነው' አሉ፤ ማኅበሩ 'የማኅበሩ ሕግና መዋቅር ያልጠበቀ አካሔድ የወለደው ነው' አሉ። በዚህ በበኩሉ ግጭቱ ከሥራ ግንኙነትም ባለፈ 'ሃይማኖታዊ ነው' አለ። በዚህ መካከል አባ ሠረቀ ብርሃን በአንጽሖ ብሒል አራማጅነት አቤቱታ ቀርቦባቸው

[27] ቀሲስ አስተርአየ ጽጌ፤ nigatuasteraye@yahoo.com፤ ታህሳስ ፳፻፫ ዓ.ም.፤ "የሰይጣን መፈክር በዋሽንግተን ዲሲ ቅድስት ማርያም ቤተ መቅደስ"
[28] ሥምረት አያሌው ታምሩ፡ ገ.120

ጉዳዩ ከሲኖዶስ ደረሰ። አባ ሠረቀም ጥንተ አብሶን ደግፈውም ሆነ ተቃውመው ስላለመስበካቸው የገለጹበትንና የቅዱስ ሲኖዶስን ውሳኔ ለመቀበል ዝግጁ መሆናቸውን ለሊቃውንት ጉባኤ ያብራሩበትን ባለ 5 ገጽ የክስ መልስ አስገቡ።[29] የክስ መልሱ ሚያዚያ 25 ቀን 2004 ዓ.ም. ገብቶ፣ ሰኔ 8 ቀን 2004 ዓ.ም. አባ ሠረቀ ላይ የቀረበውን ክስ ያየው ኮሚቴ "ነጻ ስላደረጋቸው" በአቡነ ጳውሎስ መመሪያ ሰጭነትና በወቅቱ የቅዱስ ሲኖዶስ ጸሐፊ በብፁዕ አቡነ ሕዝቅኤል ፊርማ ከክሱ ነጻ መሆናቸውን የሚገልጽ ደብዳቤ ደረሳቸው።[30] እዚህ ላይ የአጣሪ ኮሚቴው በመጋቤ ብሉይ ሠይፈ ላይ ቀደም ሲል እንዳደረገው ሁሉ ክሱን እንደ ክስ መቀበሉ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን በቅዱስ ሲኖዶስ ደረጃ በግልጽ በምልአተ ጉባኤ ተደንግጎ "እመቤታችንን ጥንተ አብሶ አለባት የሚል ውጉዝ ይሁን!" ባይባልም በገቢር ግን አስተምህሮው ለክስ እንደሚያበቃ መረዳት ይቻላል ብንል መላ ምታችን 'ምክንያታዊ' ከመባል አይታገድም - ፍንጭ ያለው መላ ምት ነው!

[29] http://eotcssd.org/images/stories/PDF/melash%20to%20liqawente%20betkrstyan.pdf

[30] http://eotcssd.org/images/stories/PDF/ethiopian%20orthodox%20tewahedo%20church%20patriarchate%20head%20office%20sunday%20school%20department%20www.pdf



**የአንጽሐ ቡድኖችን ልዩ ልዩ አመለካከት የሚያነጻጽር ሠንጠረዥ**

| | ቶማስ አኵናስ | ምሥራቅ/ ኦርቶዶክስ | ኮፕት | ተሐድሶ | ኢትዮጵያዊ የአንጽሐ ብሒል |
|---|---|---|---|---|---|
| በማኅፀን ሐና (ተጸንሳ ሳለች) ነጻች | √ | x | x | x | x |
| በብሥራተ መልአክ ጊዜ ነጻች | x | √ ከኃጢአቱ ሳይሆን ከውጤቱ (consequence of Original Sin/ guilt) ብቻ | √ | x | √ |
| ከብሥራተ መልአክ (ጌታን ከጸነሰች) በኋላም ከጥንተ አብሶ አልነጻችም | x | x | x | √ | x |
| የነጻችው ከኃጢአት እና ከመርገም ነው | √ | x | √ | x | √ |
| የነጻችው ከመርገም ብቻ ነው | x | √ | x | x | x |
| ከወላጆቿ ጥንተ አብሶንና መርገምን አንድ ላይ ወርሳለች | √ | x | √ | √ | √ |
| ከወላጆቿ ኃጢአትን ሳይሆን መርገምን ብቻ ወርሳለች | x | √ | x | x | x |
| ከሴቶች ወርኃዊ ልማድ እስከ መጨረሻ ነጻ ናት | √ | √ | √ | x | √ |
| የሀልዮ፣ የነቢብና የገቢር ኃጢአት የሌለባት በነፍስና በሥጋዋ ሁልጊዜም ድንግል | √ | √ | √ | x | √ |

X አይቀበሉም

√ ይቀበላሉ

# ምዕራፍ አራት

## የዐቀባ ቡድን፡- "ስትፀነስ ጀምሮ መንፈስ ቅዱስ ከጥንተ አብሶ ጠብቋታል፤ አበሳው አልነካትም!"

ንጽሐ" የሚለው ግስ ካሉት ትርጉሞች አንዱ "መለየት" ('ለ' ይጠብቃል) ነው ብለናል - መታቀብ። "ዐቀባ" የሚለውን ቃል ለዚህ ርእስ መግለጫነት መጠቀሜ አንድም የእንጽሐ ምሥጢራዊ ፍችን ስለሚሸከምልኝ ነው፤ እንዲያም ሲል በአገራችን ኦርቶዶክሳዊ የትርጓሜ መጻሕፍት የእመቤታችን ከኃጢአት ሁሉ ንጹሕ መሆን ማሳረጊያ እና ማጣቀሻ ቃል "መንፈስ ቅዱስ፡ ዐቀባ፡ እምከርሠ እማ" የሚል ከሃይማኖተ አበው ዘሳዊሮስ የተወሰደ ጥቅስ (ቃል በቃል ባይሆንም) በመሆኑ ቁልፉን ቃል መዘዝኩት - ዐቀባ። የቃላትን ትርጉም ከግስ ሳይሆን ከዘር (ስም) እየተነሡ የሚተነትኑት ሊቁ አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ "ዐቂብ፡- መጠበቅ፣ መከልከል፣ ጠንቅቆ ማቆየት፣..." ሲሉ ይፈቱታል።[1] በርእሳችን ለሚብራራው "ዐቀባ" የእንግሊዝኛ አቻ ትርጉሙ "Preservation" ነው። Preserve - to protect, to keep, to maintain the condition of። በነፍስ አፈጣጠር ብሒሳቸውና መርገም ብቻ ሳይሆን ኃጢአትም በዘር ይተላለፋል ብሒላቸው ቢለዩም በዐቀባ ትንታኔ ከኢትዮጵያውያን የዐቀባ ብሒል ጋር የተቀራረበ አተራረክ ያላቸው ካቶሊካውያን እንደ ኮፕቶች "እንጽሐ /Sanctify her/" ከማለት ይልቅ "ዐቀባ /Preserve her/" ማለት ይቀናቸዋል። ሁሉንም በተራ እናያለን። በዚህ ርእስ የካቶሊካውያንን አቋምና ለእንጽሐ ብሒል የተሰጡ ምላሾች፤ የኢትዮጵያና የኤርትራ ኦርቶዶክሳውያን የዐቀባ ብሒል መነሻዎችና ለእንጽሐ ብሒል የተሰጡ ምላሾች፣ ቢጻፉም ለብሒሉ ማጠናከሪያነት ያልዋሉ የምላቸውን ጥቅሶችና ትውፊቶች ለመዳሰስ እሞክራለሁ።

[1] ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፡ ገ.604



### 4.1. የካቶሊካውያን የዐቀባ ብሒል ምን ይመስላል?

(4.1.1) ጥንተ አብሶ /Original Sin/ ተብሎ የሚታወቀውን ስምና ጽንሰ ሐሳብ አስፋፍቶና አምልቶ በመግለጽ ረገድ አውግስጢኖስ (St.Augstine) ስሙ ከፍ ብሎ እንደሚጠራ ቀደም ሲል ተገልጹዋል። ኃይለ ቃሉን አቡነ ጳውሎስ "Since the fall, the human fetus was contaminated through paternal generation which affects the rational soul at its infusion – [አዳም] ከቀደመ ክብሩ ከተዋረደ ጀምሮ በማኅፀን ያለ ሰብአዊ ጽንስ ሁሉ የነፍስን ነጻ ፈቃድ በሚያጎድፍ የዘር ቁራኝነት [ጥንተ አብሶ] አድፎ ነበር" ሲሉ በውብ ቋንቋ ሰድረውታል።[2] ከእመቤታችን ጋር በተያያዘ በካቶሊካውያኑ ዘንድ ስለ ጥንተ አብሶ የነበረው ክርክር 'ከተፀነሰችበት ጊዜ ጀምሮ (ስትፀነስ) ንጹሕ ነበረች? ወይስ በማኅፀን ሐና ነው በኃይለ መንፈስ ቅዱስ የነጻች?' በሚል ሲቀርብ የኖረው እስጥ አገባ "Mary was exempt from hereditary sin from the very moment of her conception - ማርያም ጥንቱን ስትፀነስ በዘር ውርስ ከሚመጣው ኃጢአት ተጠብቃለች፤" በሚል ተቋጨ።[3]

(4.1.2) የካቶሊካውያኑን አሳብ ከስቅለት በፊት ድኅነት የተደረገ ስለሚያስመስል ከፊሉ ጋሬው ያሰኛል - an act before man - ሲሉ የሚተቹት አቡነ ሺኖዳ ስለ ጽንሰት እንበለ አበሳ (Imaculate Conception) "ደኅ ስትስ እንደሚያብራራው" ይላሉ፡- "ደኅ ስትስ ተጠይቀው ሲመልሱ፡- "ደኅ ስትስ እንደሚያብራራው" ይላሉ፡- "ደኅ ስትስ ተጠይቀው ሲመልሱ፡- ክርስቶስ በሁለት መንገድ ማዳን ይቻለዋል። አስቀድመው እንደሚያብራራው ክርስቶስ በሁለት መንገድ ማዳን ይቻለዋል። አስቀድመው በኃጢአት ተሰናክለው የወደቁትን ይቅር ብሎ ከኃጢአት ያነጻቸዋል። እንዲሁ ገና ወደ ኃጢአት ያልገባውን ንቡዑ ከመተዳደፍ (ከኃጢአት ቁርኝት) አስቀድሞ ይታደገዋል። የኋለኛውን በዕቀበት መታደግ - Redemption by Preservation - ይለዋል። በዚህም እመቤታችንን ያዳናት ኃጢአት ከተቆራኛት በኋላ ሳይሆን አስቀድሞ እንዳይቆራኛት በመታደግ (በመጠበቅ) ነው" ይሉና ብሒሉን (የዐቀባን) እንደሚያውቁ ገልጸው ትችታቸውን

[2] Aba Paulos, p.307
[3] Ibid: p.310

ያስከትላሉ::[4] ለጊዜው የካቶሊካዊው ዐቀባ ብሒልን ማሳየት እንጂ የእርሳቸውን ትችት እዚህ ላይ ማቅረብ ዓላማችን ስላልሆነ እንለፈው፤ ቀድመን አይተነዋል:: ባይሆን ካቶሊካውያን ለዐቀባ ብሒል መነሻ የሚሏቸውን ምክንያቶችና በብሒሉ የተነሣ ለሚቀርብባቸው ትችት የሚሰጡዋቸውን መልሶች በወፍ በረር እንይ::

(4.1.3) እመቤታችን እንበለ አበሳ አዳም /ያለጥንተ አብሶ/ ተፈጥራለች (ተፀንሳለች) ሲሉ ካቶሊካውያን ከሚያቀርቧቸው መጽሐፍ ቅዱሳዊ መነሻዎች ውስጥ:-

(1) ዘፍ.3፡15 "በአንተና በሴቲቱ፣ በዘርህና በዘርዋ መካከል ጠላትነትን አደርጋለሁ፤ እርሱ ራስህን ይቀጠቅጣል አንተም ሰኮናውን ትቀጠቅጣለህ" ይህ ጥቅስ በካቶሊካውያን ሲተነተን:- ሴቲቱ - እመቤታችን፤ ዘርዋ - ጌታ ነው:: በሴቲቱና በእባብ (ሰይጣን) መካከል ጠላትነት ሰፍኗል:: ሴቲቱ የተባለችው እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት ካልን ለሰይጣን ተቃራኒ መሆን አትችልም ነበር:: ስለሌለባት ለሰይጣን ተቃራኒ ሆናለች[5]፤ በዘሩና በዘርዋ መካከል ጠላትነት ተደርጓል::

(2) ሉቃ.1፡28 "ደስ ይበልሽ፤ ጸጋ የሞላብሽ ሆይ!" የዚህ ቃል አቻ የእንግሊዝኛ ትርጉም "Full of Grace" ነው:: የእንግሊዝኛው ሥርወ ቃል በግሪክ አነጋገር "κεχαριτωμένη - kechariotomene" ሲሆን ትርጓሜውም "The One who has received the totality of grace - የተትረፈረፈ ጸጋ የሞላባት" ማለት ነው:: አንቀጹ perfect passive participle በመሆኑ የጸጋ ስጦታዋ በኃላፊው ጊዜም፤ ዛሬም፤ ወደ ፊትም ጸጋ በጸጋ ላይ ሲጨመርላት

[4] https://www.suscopts.org/q&a/index.php?qid=511&catid=203

[5] በተፈሥሒ ማርያም የኪዳን ጸሎት "ተፈሥሒ ማርያም ዘእልባሰ ንጽሕኪ ምንታዌ፤ ዘእምሰጠኪ ትድመ እምቲሐት ኅምዙ ለአርዌ - የንጽሕና ልብስሽ (ጸጋሽ) መንታ (የነፍስና የሥጋ) የሚሆን፤ ከአውሬው (የመርገም) ትፋት ያመለጥሽ ማርያም ሆይ ደስ ይበልሽ" የሚለው ንባብ ከዚህ የሚቀራረብ ይመስላል::



እንደሚኖር ያስረዳል - She was graced in the past but with the continuing effect in the present ይላሉ::[6]

(3) "የእስራኤልንም አምላክ የእግዚአብሔርን ታቦት ያመጡ ዘንድ ካህናቱና ሌዋውያኑ ተቀደሱ:: (1ኛ ዜና.15:14)::" ታቦት የተባለ ጌታ ነው:: ታቦት ከማይነቅዝ ዕንጨት እንደሚቀረጽ ጌታም ከአዳም የሆነው ንቅዘተ ኃጢአት ከማይነካካት እመቤታችን ተወልዷል:: ቅዱሱን ታቦተ ሕግ ለመሸከም ካህናቱ ተለይተው ሊቀደሱ ግድ ከሆነ አማናዊውን ታቦትና የቅድስና ምንጭ የሆነውን ጌታ የተሸከመችው እመቤት'ማ እንዴታ! አስቀድም ተቀድሳ ተፈጥራለች እንጂ - ይናገራሉ ካቶሊካውያን::

(4) ጥበ.1:4 "ዲያብሎስ በተተነኰላት ሰውነት ጥበብ አታድርም::" ጥበብ የተባለ ጌታ ነው:: ማደሪያው እመቤታችን ናት:: በእርሷ ላይ መርገም /ቁራኝነት/ ቢኖር አያድርባትም ሲሉ የዐቀባ ብሒል መጽሐፍ ቅዱሳዊ መነሻዎቻቸውን ይደረድራሉ፤ እመቤታችን ጥንተ አብሶ አልነበረባትም ይላሉ::[7]

(4.1.4) ከአንጽሖ ብሒል ደጋፊዎች ለሚሰነዘርባቸው ትችት ይመልሳሉ:: መጽሐፍ ቅዱስ ተጠቅሶ ለሚቀርብባቸው ነቀፋ ከሚሰጡት መልስ እንጀምር:-

(1) ቅዱስ ጳውሎስ "ሁሉ ኃጢአትን ሠርተዋልና" ሲል በሮሜ.3:23 የተናገረው ቃል እመቤታችንን አያካትትምን? ሲባሉ መልሳቸው አያካትትም ነው:: ምክንያታቸው "ሁሉ" የሚለው ቃል መቶ በመቶ /100%/ ለማለት አይደለም፤ ለምሳሌ:- ሕፃናት ንጹሐን ስለሆኑ (ሮሜ.9:11) በዚህ "ሁሉ" የሚል ቅጽል አይካተቱም:: ጌታችን እንዲሁ ንጹሐ ባሕርይ ስለ ሆነ (ዕብ.4:15) "ሁሉ" የሚለው ቃል እርሱን አያካትትም:: ስለሆነም ሮሜ.3:23 ልዩ ሁኔታ (exception) አለው:: 'በዚህ አምሳል የሐዲስ ኪዳኑ ዳግማይ አዳም መድኅን ክርስቶስ እንበለ ኃጢአት ተወለደ' እንደምንለው ሁሉ 'የሐዲስ

[6] ይህ ብሂል በእኛ ትውፊትም የጸና ነው፡፡ቅዱሳን ውዳሴ ማርያም (ተፈሥሒ እ ምልዕተ ጸጋ፤ ድንግል በእንበለ ርኩስ) እንደምታ፥ ገ.107

[7] http://catholicbridge.com/catholic/mary_conceived_without_sin_immaculate_conception.php

ኪዳና ዳግሚት ሔዋን ልክ ሔዋን በጥንተ ተፈጥሮ እንደ ነበረችው እንበለ ኃጢአት ተገኝታ ጌታን አስገኘች መባሉ ኢመጽሐፋዊ አይደለም ይላሉ።

(2) ኃጢአት የለባትም ካልን ሰው አይደለችም፤ ከእግዚአብሔር ተካከለች እያለኸብንም ወይ? ሲባሉ መጀመሪያ አዳምና ሔዋን ከድቀት በፊት በገነት ሲኖሩ ኃጢአት አልነበረባቸውም። ግን ኃጢአት አለመሥራታቸው ከሰውነት አውጥቶ ከእግዚአብሔር አላስተካከላቸውም። መላእክት እንዲሁ እንበለ ኃጢአት ንጽሕናቸውን ጠብቀው ይኖራሉ። ሆኖም መላእክት እንበለ ኃጢአት 'ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ' እያሉ ስለሚኖሩ የተጎናጸፉት ንጽሕና ከእግዚአብሔር አላስተካከላቸውም። ኃጢአተኛ መሆን የሰብአዊነት ማረጋገጫ አይደለም፤ ሰውን ሰው ያደረገው ኃጢአት አይደለም - Sinning does not make one human:: ስለሆነም እመቤታችን እንበለ ኃጢአት ተፀነሰች ብንል አምላክ ናት ማለታችን አይደለም - ይሞግታሉ ካቶሊካውያን።[8]

(4.1.5) ዶግማው ከ1854 ዓ.ም. ወዲህ የመጣ አስተምህሮ ነው ለሚሏቸው ሲመልሱ፦ ዶግማ በሁለት ምክንያት ይደነገጋል። መጀመሪያ መጥራት ያለበት ሃይማኖታዊ ብዥታ ሲኖር ነው። ሁለተኛ ቀድሞ ለነበረው እምነት የተለየ ትኩረት በመስጠት ምእመኑን ለማጽናት ሲፈለግ ነው። የ1854 ዓ.ም. ዶግማ የተደነገገው እመቤታችንን ከጥንተ አብሶ ንጽሕት ስላለመሆኗ የተንሰራፋ ጥርጣሬ ኑሮ ሳይሆን ሲኖዶሱ ምእመኑን በነባሩ እምነት ለማጽናት ሲል ነው ይላሉ - ዶግማው መደንገጉ። ሁለቱንም ያስተባበረ ምሳሌ እንስጥላቸው። ጉባኤ ኒቅያ በ325 ዓ.ም. "ወልድ ፍጡር ሳይሆን ፈጣሪ ነው" ብሎ ደንግጎ ዶግማ ሠርቷል። ይህ ዶግማ በ325 ዓ.ም. ተደነገገ ማለት እስከ 325 ዓ.ም. ድረስ ባለው ክርስትና "ወልድ ፍጡር" ተብሎ ይታመናል ማለት አይደለም። የ1854 ዓ.ም. እመቤታችን ከጽንሰቷ ጀምሮ ከጥንተ አብሶ ተጠብቃለች የሚለው ካቶሊካዊ ዶግማም ነባሩን "ጽንሰታ ለማርያም እንበለ አበሳ - Immaculate Conception of St.Mary" ብሒል ያፀና እንጂ አዲስ አስተምህሮ ያመጣ አይደለም - ይከላከላሉ።[9] ካቶሊካውያን ጽንሰታን በእነርሱ ታኅሣሥ (December) 8 "ጽንሰታ፡ ለማርያም፡ እንበለ ጥንተ አብሶ" ብለው ያከብራሉ። እኛ ጽንሰታን (አበው "ቁጽረታ" ይሏታል ዕለቷን) ነሐሴ 7 እናከብራለን፤ ሆኖም "እንበለ ጥንተ አብሶ" የሚለውን እንደ እነርሱ አናነሳም። ካቶሊካውያን "Immaculate Conception of St.Mary" በሚል ስያሜ ቤተ ክርስቲያን፣ ሆስፒታል፣ ትምህርት ቤት… ይሰይማሉ፤ ልክ እኛ ለልደታና ለበዓታ እንደምናደርገው።

[8] ዝኒ ከማሁ
[9] ዝኒ ከማሁ



(4.1.6) ግሪካውያንና ግብጻውያን ከላይ በተራ ቁጥር 4.1.4እና 4.1.5 ካቶሊካውያን መልስ የሰጡባቸውን ጥያቄዎች እያነሱ 'በኛ ትውፊት ስለሌለ የዐቀባ ብሂላችሁን እንቀበላችሁም' ይሏቸዋል - ካቶሊካውያንን። ካቶሊካውያን በበኩላቸው ከምሥራቅና ከኦሪየንታል አብያተ ክርስቲያናት ሐሳባቸውን የሚደግፉላቸውን አበው ምስክርነት ይጠራሉ። ምስክሮቹ ጥንተ መሠረቱ ከግብጽ ኮፕቲክ የነበረና ኋላ "እመቤታችን ያለጥንተ አብሶ ተፀንሳለች" የሚለውን ብሒል የተቀበለ ሰው ለማስረጃነት የቈጠራቸው ናቸው። አስረዝሜ ሳቅርበው - ቁልፍ ቃሉን ብቻ እተረጉመዋለሁ፦

(1) St. Gregory Thaumaturgus in the 3rd century taught that even before the Annunciation, even before the death and resurrection of our Lord, Mary was already "in possession of the incorruptible citizenship," and that she had "a body made purer than any gold - እመቤታችን ቅድመ ብሥራት መልአክ ከጌታ ሞትና ትንሣኤ በፊት ያልተዳደፈ ባሕርይ ነበራት፤ እርሷ ከወርቅ የጠራ አካል ነበራት።"

(2) St. Ephraim in the 4th century taught that before their respective decisions, Eve and Mary were "utterly equal - ሔዋንና እመቤታችን ከውሳኔያቸው በፊት (ሔዋን በለስ ከመብላቷ፣ እመቤታችንም 'ይኩነኒ' ከማለቷ በፊት) ፍጹም እኩል ነበሩ።"

(3) St. Theodotus of Ancyra in the 5th century taught that Mary was "included in woman's sex, but without a share in woman's fault - እመቤታችን በሴት ባሕርይ ተፈጥራለች፤ ሆኖም በሴቶች መርገመ ኃጢአት ሱታፌ የላትም።"

(4) St. Proclus of Constantinople, likewise in the 5th century taught that Mary was "made without any stain - እመቤታችን እንበለ አበሳ ተፈጥራለች።"

(5) St. Severus of Antioch in the 6th century taught that Mary was "of the same essence as we, although she was pure from all taint and immaculate - ዛሬ እኛ በደመ ክርስቶስ እንደነጻነው እመቤታችንም ከአደፍ ጉድፍ ነጻ ነበረች።"

(6) St. Sophronius of Jerusalem in the 7th century taught that Mary, "holy, immaculate in soul and body, entirely free from Every Contagion- እመቤታችን ቅድስት፣ በነፍስ በሥጋ ንጽሕት፣ ሙሉ ለሙሉ በዘር ከሚተላለፈው ማናቸውም በደል (Contagion) የነጻች ናት።"

(7) St. John Damascene in the 8th century taught that Mary was "hidden from the fiery dart of Satan, dwelling in a bridal chamber of the spirit, preserved without stain as the Spouse and Mother of God - እመቤታችን ነበልባላዊ ከሆነው የሰይጣን ፍላጻ ተሠውራ የመንፈስ ቅዱስ ሙሽራ ሆና በሚገኘው (በመቅደሱ) ኖረች፤ የእግዚአብሔር ሙሽራ እና እናት እንበለ አበሳ በተዐቅቦ ኖረች።"

(8) St. Photius in the 9th century taught that Mary was sanctified ek brephous in the womb of St. Hannah - that is, from the first instance of her existence in her mother's womb - የተቀደሰችው በማኅፀን ሐና ስትፀነስ (ሕላዌ ስታገኝ) ጀምሮ ነው።"

(9) St. Euthymes of Constantinople in the 10th century taught that God built His "fully sanctified" tabernacle on the day Mary was conceived - (ልዑል) ከማርያም ጽንሰት ጀምሮ ማደሪያውን በምልዐት ቀደሰ።"



(10) St. Gregory Palamas in the 14th century taught that Mary was created with flesh that was "both new and ours - እመቤታችን እኛን በመሰለ አዲስ ተፈጥሮ ተፈጠረች።"

(11) Patriarch Scholarios in the 15th century taught that Mary was "all pure from the first moment of her existence - ስትፈጠር ጀምሮ ንጽሕተ ንጹሐን ናት።"

(12) Patriarch Cyril Lukaris of Constantinople in the 17th century taught that Mary "was wholly sanctified from the very first moment of her conception - ጥንቱን ስትፀነስ በኹለንታሃ (በሁለንተናዋ) ተቀድሳለች።"

(13) Patriarch Gerasimo of Alexandria, likewise in the 17th century, taught that Mary "was not subject to the sin of our first father - እመቤታችን በቀደሙ አባቶቻችን መርገም አልተገዛችም።"[10]

ከላይ ከተጠቀሱት ቀዳምያን አበው በተጨማሪ ሄሬኔዎስ የተባለ በ2ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የነበረ አባትም እመቤታችን ዳግሚት ሔዋን ስለሆነች ተፈጥሮዋ እንበለ ጥንተ አብሶ ነው በሚል ስብከቱ ይታወቃል - c. 180 A.D. - St. Ireneaus of Lyon, a disciple of the early Greek father St. Polycarp of Smyrna, who was a disciple of the Apostle John himself, speaks of Mary's sinlessness, comparing it with the original sinlessness of Eve before the Fall።[11]

(4.1.7) ጥንተ አብሶ ከሌለባት "በእምላኪየ በመድኃኒቴ" ብላ በሉቃ.1:46-47 ለምን ጸለየች? ሲባሉ ስለ ድኅነት ያላቸውን ጽንሰ አሳብ እንድንረዳ

[10] O.R.Vassal-Philips, The Mother of Christ, or, The Blessed Virgin Mary in Catholic Tradition, Theology, and Devotutio, 2nd edition, 1922, p.23-48 ወይም http://tasbeha.org/community/discussion/9357/immaculate-conception

[11] http://catholicbridge.com/catholic/mary_conceived_without_sin_immaculate_conception.php

ይጋብዙናል። አሳባቸው እንዲህ ነው፡- ጌታ እኛን ያዳነበት መንገድ ከጥንተ አብሶና ከምልአተ ኃጢአት መፈወስ ነው - curatively። እርሷን ግን ኃጢአት ሳይነካት በጥበቃ /በትድግና/ ነው ያዳናት - preventively። ብዙ ጊዜ ምሳሌ የሚያደርጉት ጉድጓድ ውስጥ የገባን ሰው ማውጣትና ገና ያልገባን ሰው መታደግን ነው። ጉድጓድ ውስጥ የገባን ሰው ማውጣት "ማዳን" ይባላል። ገና ወደ ጉድጓዱ ያልገባን ሰው እንዳይገባ ማትረፍም "ማዳን" ይባላል። የእርሷ "መድኃኒቴ" ማለትም እንዲያ ነው። በፍዳው እንዳትያዝ ስላዳናት "መድኃኒቴ - my savior" ትለዋለች። ይህን ለእመቤታችን የተደረገ ከጥንተ አብሶ የማዳን ተእምር ካቶሊካውያን "አስቀድሞ ማዳን - Redemption by Anticipation" ይሉታል። ካቶሊካውያንን በዚሁ አመስገንን ተሰናበትናቸው!

## 4.2 ኢትዮጵያዊው "ዐቀባ እምከርሠ እማ" ብሒል

### 4.2.1 የዐቀባ ብሒል መሠረቱ በኢትዮጵያውያን ሊቃውንት ሲገለጽ

(4.2.1.1) ኢትዮጵያዊውን የአንጽሖ አመለካከት በፓትርያርክ አቡነ ጳውሎስ አቋም እንደ ጀመርነው ሁሉ የዐቀባ ብሒልን እንዲሁ በብሒሉ ታማኝና ተቆርቋሪ ፓትርያርክ አቡነ ማትያስ አቋም እንጀምረው። አቡነ ማትያስ በሉቃ.1:28-38 ያሉትን የቅዱስ ገብርኤል ብሥራታዊ ቃላት በኃላፊና በትንቢት የግስ ዐመላቸው በመዘርዘር የዐቀባን መሠረትነት ያስረግጣሉ። "ጸጋን የተሞላሽ ሆይ" የሚለው ቃል በኃላፊ (past tense) እንጂ በትንቢት (future tense) አልተነገረም፤ ማለትም "ወደፊት ጸጋን ይሞላብሻል፤ ከሴቶችም ሁሉ የተባረክሽ ትሆኛለሽ" አላላትም። እንደ ገና መልአኩ በሰላምታው መደንገጥዋን አይቶ "ማርያም ሆይ በእግዚአብሔር ፊት ጸጋ አግኝተሻል አትፍሪ!" አላት። አሁንም የመልአኩ ማረጋጊያ ዐረፍተ ነገር ኃላፊ እንጂ ትንቢት አይደለም፤ "አግኝተሻል" አላት እንጂ "ወደ ፊት ታገኛለሽ" አላላትም። ይህ ሁሉ የሚያሳየው ከመፀነሷ በፊት ወይም ወደዚህ ዓለም ከመምጣቷ በፊት ጀምሮ መርገመ ሥጋ፣ መርገመ ነፍስ ያልነበረባት መሆኑን ነው ይላሉ አቡነ ማትያስ።[12] አባታችን እንደሚሉት መልአኩ "መንፈስ ቅዱስ ባንቺ ላይ ይመጣል" ያላት "ትወልጃለሽ" ሲላት "ወንድ

[12] አባ ሠረቀ፣ አውንትና ጉጋት፣ ገ.43



ሳላውቅ እንዴት ይሆንልኛል?" ስትል ላቀረበችው ጥያቄ ነው። ይህም የመንፈስ ቅዱስ በእርሷ ላይ መምጣት "ለፅንስ[13] እንጂ ለአንጽሖ እንዳልሆነ" የእርሷ ጥያቄና የመልአኩ መልስ ያረጋግጣል።[14] የግሪክ ኦርቶዶክሳውያን "መንፈስ ቅዱስ አስቀድሞ ከማኅፀን ከጠበቃት ለምን በብሥራት ጊዜ ዳግም መጣ?" ማለታቸውን እዚህ ላይ የሚጠቅስ ቢኖር ታዲያ በሐዋ.1:14 እንደ ተገለጸው ጌታ ባረገ በንምሳኛው ቀን ከሐዋርያት ጋር ሳለች ከእነሱ ጋር የወረደላት መንፈስ ቅዱስ እንዲሁ ለማንጻት ነው ልንል ነው? ምጽአተ መንፈስ ቅዱስ ለአንጽሖ ብቻ ነው እንዴ? በዘፍ.1፡2 እንደተጻፈ ዓለም ሲፈጠር በውኆች ላይ የሰፈፈው የእግዚአብሔር መንፈስ ውሃውን ለማንጻት ኖሯልን? እያልን በተጠየቅ እንሞግታለን።

(4.2.1.2) አቡነ ማትያስ፡- "ኤርምያስን 'በሆድ ሳልሠራህ ዐውቄሀለሁ፤ ከማኅፀንም ሳትወጣ ቀድሼሀለሁ፤ ለአሕዛብም ነቢይ አድርጌሀለሁ' (ኤር.1:5) ሲል ለነቢይነት ለመረጠው ኤርምያስ ይህን ያህል ክብር የሰጠ አምላክ ለእናትነት የመረጣትን ቅድስተ ቅዱሳን ድንግል ማርያምን ከእናቷ ማኅፀን ጀምሮ አንጽቶ ቀድሶ ለመጠበቅ ምን ይሳነዋል?" ሲሉ ተከራካሪዎቻቸውን ያዳንቁባቸዋል።[15] ከቅዱሴ ማርያም "ንጽሕናሽን ባወቀ ጊዜ መልአኩን ላከ" አለ እንጂ "ሊያነጻሽ መልአኩን ላከ" አላለም ይላሉ። ከሃይማኖተ አበውም ቅዱስ ኤራቅሊስ የዮሴፍን የእመቤታችን ንጽሕና አለመረዳት ሲገልጽ "ከንጹሕ ዘር የተፈጠረች ድንግል የእግዚአብሔር ማደሪያ እንድትሆን አላወቀም!"[16] ቅዱስ ቄርሎስ "ቢሥጋ ከመጀመሪያው ሰው ከአዳም፣ ከአብርሃም፣ ከዳዊት ከተገኘ ባሕርይዋም ኃጢአት የሌለበት በነፍስ በሥጋ ፍጹም የሆነ አካልን ሊዋሐደው ፈጠረ" እንደሚል በመጥቀስ የእመቤታችን ንጽሕና ጥንቱን በማኅፀነ ሐና ስትፈጠር ከጽንሰቷ ጀምሮ እንጂ ከመልአኩ

[13] አባታችን "የመንፈስ ቅዱስ መምጣት ለፅንስ ነው" ሲሉ ክብር ይግባውና መንፈስ ቅዱስ ሥጋ ለብሶ ተፀነሰ ለማለት አይደለም። ጌታ እንዘበ ዘርዐ ብእሲ (ያለ ወንድ ዘር) ከእመቤታችን የተወለደበት ሒደት በትውፊታችን "ገባሬ መንፈስ ቅዱስ ከእመቤታችን ዘር ነሣ፤ የሚያዋሕድ፤ የሚከፍል መንፈስ ቅዱስ ነው።" የሚሉ ምንባባት ስላሉ በዚህ መንፈስ ነው።

[14] ዝኒ ከማሁ፥ ገ.44። እርግጥ "መንፈስ ቅዱስ የመጣው ለአንጽሆ ነው" የሚሉ ደረቅ ምንባባትም በዛት አሉ። ነገር ግን "አንጽሐ/ አንጽሐ/ አንጺሖ" የመሳሰሉ ቃላት ከእመቤታችን አንጻር የሚተረጎሙት "መለየትና መከልከል" በሚል ትርጓሜያቸው ነው።

[15] ዝኒ ከማሁ፥ ገ.40

[16] ሃይ.አበ.ዘኤራቅሊስ 48 ቁ 31

ብሥራት ወዲህ እንዳልሆነ ይናገራሉ።[17] አክለውም አለቃ አያሌው ታምሩ "ምልጃ፣ ዕርቅና ሰላም" በተሰኘ መጽሐፋቸው ገጽ 49 "ለእናትነት የመረጣት ማደሪያውን ከእናቷ ማኅፀን ጀምሮ ከኃጢአት፣ ከርኵሰት፣ ከእድፈት፣ ሁሉ ጠብቋታል። የሰው ልጆች የተያዙበት በአዳም በደል ወይም በራሳቸው በደል ምክንያት የረከሱበት የኃጢአት ቅሪት መርገመ ሥጋ፣ መርገመ ነፍስ የለባትም፣ አላገኛትም። ምክንያቱም እርሱ ለራሱ ማደሪያ አድርጎ ስለ መረጣት ነው" ማለታቸውን ጠቅሰው አቋማቸውን በአለቃ አቋም አጠናክረዋል።[18]

(4.2.1.3) የእሁኑዎቹ አንጋፋ ቀሳውስት የዚያን ጊዜዎቹ ለግላጋ ዲያቆናት እሸቱ ታደሰና ደጀኔ ሺፈራው በጋራ በመሆን በ1987 ዓ.ም. ባሳተሙት "ወላዲተ አምላክ በመጽሐፍ ቅዱስ" የተሰኘ መጽሐፋቸው ገጽ 15 እመቤታችን "ቅድመ ዓለም በአምላክ ሕሊና ታስባ የኖረች፣ የአዳም ኃጢአት ያልነካት፣ ለአዳም ድኅነት ምክንያት የሆነች፣ ንጽሕተ ንጹሐን፣ ቅድስተ ቅዱሳን በመሆኗ በሥጋም በነፍስም ፍጽምት ትባላለች። ፍጽምት ማለት እንከንና ጉድለት የሌለባት ማለት ነው፤" ሲሉ ጽፈዋል። ይህ ጽሑፍ በወቅቱ ስለ ጥንተ አብሶ በወጣት የቤተ ክርስቲያን ልጆች አካባቢ መረዳት እንደ ነበርና ለዐቀባ ብሒል ያለውን ተቀርቋሪነት ያሳያል፤ ብቻ መጽሐፉ ስለ ጥንተ አብሶ መናገሩ መልካም ሆኖ ሳለ በማጣቀሻ አለመዳበሩ ማጣቀሻነቱን ቀለል ሳያደርገው አይቀርም። ሌላኛው የእኛ ትውልድ ፊር ቀዳጅ ኦርቶዶክሳዊ ጸሐፊ ብርሃኑ ጎበና "ዓምደ ሃይማኖት" በተባለች ምጥን ግን በይዘቷ ጥብቅ ያለች መጽሐፉ ገጽ 101 "አንዳንዶች እመቤታችንን የአዳም ኃጢአት አለባት፣ ስለዚህም በደሙ ከተዋጀች ወገን ናት ይላሉ። ነገር ግን እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም የአዳም ኃጢአት የሌለባት በሥጋም በነፍስም ንጽሕት በመሆንዋ መንፈስ ቅዱስ ከእናትዋ ማኅፀን ጀምሮ ያ! በዘር የሚተላለፍ የመጀመሪያ ጥፋት[19] ወደ እርስዋ እንዳይተላለፍ ጠብቋታል። ሉቃ.1:28፣ መኃ.4:12" ሲል አስፍሯል። ከዚያ ጊዜዎቹ ዲያቆናት እሸቱ እና ደጀኔ አንጻር ብርሃኑ ማጣቀሻ ማስቀመጡ ያስመሰግነዋል። ነገር ግን "እመቤታችን በደሙ ከተዋጁት ወገን" እንዳልሆነች የሚያስመስልና ምናልባት

[17] አባ ሠረቀ፣ እውነትና ንጋት፡ ገ.44
[18] ዝኒ ከማሁ
[19] "ጥፋት" ከሚለው "መርገም" ቢለው የቀና ይሆናል።



መጋቤ ብሉይ ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስን ለመንካት ተብሎ የቀረበው ንባብ ለፀጉር ሰንጣቂ በር የሚከፍት ነው። ባይሆን (በእኔ ለመታረም ዝግጁ የሆነ ትሑት እይታ) "እመቤታችን በደሙ ተዋጅታለች፤ ይሁን እንጂ መዋጀቷ እንደ ሌሎች አሪታውያን ከጥንተ አብሶ ለማንጻት ሳይሆን ልክ አዳምና ሔዋን ሲፈጠሩ እንደ ነበረው ሁኔታ አስቀድሞ የተደረገላትን የንጽሐ ባሕርይ ተፈጥሮ ጥበቃ (ዕቅበት /ትድግና/) ለማጽናት ነው!" ቢባል የቀና ይሆናል።

መምህር አንዱ ዓለም ዳግማዊ ድርሳነ ማርያምን ጠቅሰው "...እኮ ዘመጽአ ላዕሌሃ መንፈስ ቅዱስ ዘከመ መጽአ ላዕለ ነቢያት ወሐዋርያት ወላዕለ ኵሎሙ መሃይምናን ለቀድሶ ነፍሶሙ ወሥጋሆሙ ... ለማርያምሰ እምከርሠ እማ ቀደሳ ወአንጽሐ መንፈስ ቅዱስ በቅዳሴ ወንጽሕ ዘኢይትነገር - መንፈስ ቅዱስ በእመቤታችን ማደሩም በቅዱሳን ነቢያትና ሐዋርያት እንዲሁም በምዕመናን ሁሉ ነፍሳቸውንና ሥጋቸውን ለማንጻት ... እንደመጣው አይደለም ... ድንግል ማርያምን ... መንፈስ ቅዱስ ከእናቷ ማኅፀን ጀምሮ ይህ ነው ተብሎ ሊገለጽ በማይቻል ቅድስናና ንጽሕና አንጽቷታል፤ ቀድሷታል" ሲሉ ያቀረቡት ንባብ ለዐቀባ የትድግና ብሒል ግሩም ማስረጃ ነው።[20]

(4.2.1.4) መጋቤ ብሉይ ሠይፈን ካነሳን በ1982 ዓ.ም. የአንጽሐ ብሒልን ደግፈው ከመጻፋቸው በፊት በ1971 ዓ.ም. ለዐቀባ ወግነው የጻፉትን መጣጥፍ እንቆንጥር። እንዲህ ብለው ነበር፦ "ማርያም ቅድስት ድንግል ከኃጢአት ሁሉ ንጽሕት እንደሆነች ቤተ ክርስቲያን ታምናለች። ለዚህም መልአኩ 'ምልዕተ ጸጋ ሆይ! ደስ ይበልሽ!' ኤልሳቤጥም 'ቡርክት ነሽ' በማለት የተናገሩት ቃል መሠረታዊ ማስረጃ ነው። ሉቃ.1:28-41። ቅዱስ ያሬድ (500 ዓ.ም.) ድንግል ማርያም ኃጢአት እንደሌለባት ሲናገር 'ማርያም ግን በአዳም ባሕርይ ውስጥ ከጥንት ጀምሮ እንደነጭ እንቁ ታበራለች' ይላል[21]" ብለው ነበር።[22] ሊቀ ጉባኤ አባ ግርማ ርእየቱ የተባሉ የብሉይና የሐዲስ መምህር ባሳተሟት "ታኦዶክስ" የተሰኙች አነስተኛ ግን ቁም ነገሯ የበዛ መጽሐፍ "ገና በማኅፀን ከመፈጠሯ አስቀድሞ ከኃጢአት፣ ከርኵሰት፣ ከጥንት

[20] አንዱ ዓለም ዳግማዊ (መምህር)፣ ወላዲተ አምላክ በነገረ ድኅነት፣1998 ዓ.ም.፡ገ.128-129
[21] ድጓ ዘልደታ
[22] መ/ብ ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስ፣ ትንሣኤ መጽሔት ቍጥር 23፣ 1971 ዓ.ም.፡ ገ.4 እና 6

አብሶና ከምልአተ ኃጢአት ጠብቋታል። ከአባቷ ከኢያቄም አብራክ በዘርነት ወደ እናቷ ማኅጸን ስትላክ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ባወቀ ከኃጢአት፣ ከበደል፣ ከርኵሰት፣ ከልማደ አንስት፣ ከእደፍና ከጉድፍ አጥልሏታል። የተዋሕዶ ሊቃውንት ሉቃ.1:35 ላይ ያለውን ኃይለ ቃል 'ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ፦ የልዑል ኃይል መንፈስ ቅዱስ ከኃጢአት፣ከርኵሰት፣ከጥንተ አብሶና ከምልአተ ኃጢአት አጠለለሽ እያሉ ይተረጉሙታል፤" ይሉናል ሃይማኖተ አበው ዘሶሐንስ አፈወርቅ ምዕራፍ 66 ቁ 14'ን ጠቅሰው።[23] "አጠለለሽ" የምትለዋ አማርኛ ላይ ተዐቅቦ አለኝ፤ እመለስባታለሁ። "ከኃጢአት ጠብቋታል" የሚል አገላለጻቸውም ቢሆን ኃጢአት በዘር ይተላለፋል ብዬ ለማመን ምንታዌ ስለሚይዘኝ እንዲሁ ተዐቅቦ አደርጋለሁ።

(4.2.1.5) መምህር ኃይለ ማርያም ላቀው "ሐውልተ ስምዕ" በተባለ ውብ መጽሐፋቸው ከገጽ 170-181 እመቤታችን ከጥንተ አብሶ ንጽሕት መሆኗን ለማስረገጥ እስከ አሁን ባየናቸው ጸሐፍያን ያልተጠቀሱ ሦስት ዋና ዋና ማስረጃዎችን አቅርበዋል፦

(1) መዝ. 46:5 "ልዑል ማደሪያውን ቀደሰ፤ እግዚአብሔር በመካከልዋ ነው አትናወጥም" ይህን ቃል ትርጓሜ ዳዊት "እግዚአብሔር ማደሪያው እመቤታችንን በድንጋሌ ሥጋ፣ በድንጋሌ ነፍስ አፀናት። ...በዘመዶቿ ፍዳ እንዳትያዝ እግዚአብሔር በማኅፀኗ አደረ፤" ሲል ይፈታዋል።[24]

(2) ቅዱስ ያሬድ በነሐሴ ኪዳን ምሕረት ድጓ "ዘእንበለ ይትፈጠር ሰማይ ወምድር ወዘእንበለ ትሣረር ምድረ ገነት ሀለወት ስብሕት ቅድስት ወቡርክት ማርያም ... የተመሰገነች፤ በንጽሕና በድንግልና የተለየችና የተባረከች እርሷ ማርያም ሰማይና ምድር ሳይፈጠር፣ የገነት ምድር ሳይጣል የተመሰገነች ነበረች" ይላታል።

(3) ኢሳ.1:9 "የሠራዊት ጌታ እግዚአብሔር ዘርን ባያስቀርልን ኖሮ እንደ ሰዶም በሆንን፣ እንደ ገሞራም በመሰልን ነበር" የብሉይ መተርጉማን የኢሳይያስን ቃል "አሸናፊ እግዚአብሔር እመቤታችንን ከመርገመ ሥጋ፣ ከመርገመ ነፍስ ያስቀረልን ባይሆን እንደ ሰዶም በሆን ነበር፤ ገሞራንም በመሰልን ነበር፣ እነዚያ የነፍስ አማላጅ አጥተው እንደጠፉ እኛም እንጠፋ

[23] ሊቀ ሥልጣናት? ሊ/ት አባ ግርማ ርእዩ፣ ታእዶከስ፣ 2003 ዓ.ም.፣ ገ.10

[24] መዝሙረ ዳዊት ንባቡና ትርጓሜው፣ ገ.248



ነበር"[25] ሲል ይተረጉመዋል። እግረ መንገድ ከዚሁ የተዛመደ የአባ ፅጌ ድንግል ድርሰት ስላለ ከማኅሌተ ጽጌ ማጠናከሪያ እንጨምር፦

ከመ ሰዶም እምኮነ፣
ወከመ ገሞራ እመሰልነ፣
እግዚአብሔር ኪያኪ እመ ኢያትረፈ ለነ፣
በትረ ተአምር ማርያም አንተ ጸገይኪ መድኅነ፣
ዘይቤ ኢመጻእኩ እጸውእ ጻድቃነ
አላ ለንስሐ ኃጥአነ።

ትርጉም፦ "ጻድቃንን ልጠራ አልመጣሁም፤ ኃጥአንን ለንስሐ ልጠራ እንጂ የሚለውን መድኅን ያፈራሽልን ተአምራዊት (የአሮን) በትር ሆይ! እግዚአብሔር አንቺን ለዘር ባያተርፍልን እንደ ሰዶም በሆንን፤ እንደ ገሞራም በመሰልን ነበር።"

(4.2.1.6) የዐቀባ ብሒል ማለትም መንፈስ ቅዱስ ዐቀባ እምከርሠ እማ ይትበሀል ወይም "እመቤታችን ጥንተ አብሶ የለባትም" የሚል እምነት "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን እምነት፣ ሥርዓተ አምልኮና የውጭ ግንኙነት" የተሰኘው በ1988 ዓ.ም. (እ.ኤ.አ. 1995 ዓ.ም.) አቡነ ጳውሎስ በሰጡት መመሪያ በስድስት ጳጳሳትና በአስራ አንድ የሊቃውንት ጉባኤ አባላት በጠቅላላ አስራ ሰባት ጳጳሳትና ሊቃውንት ተሰባስበው ተዘጋጅቶ አርትዖቱ በዐራት የሐዲሳትና የብሉያት መምህራን በአማርኛና በእንግሊዝኛ ተሠርቶ በቅዱስ ሲኖዶስ ተመርምሮ በታተመው መጽሐፍ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ እንዲዘጋ ባለመ መልኩ ተደንግጎ ወጥቷል። በጉባኤው፦ አቡነ መቃርዮስ፣ አቡነ ናትናኤል፣ አቡነ በርተሎሜዎስ፣ አቡነ ሳሙኤል (ከላይ የተዘረዘሩት ሁሉም አሁን በሕይወተ ሥጋ የሉም)፣ አቡነ ገብርኤል፣ አቡነ ገሪማ ከጳጳሳት ወገን፤ መልአከ ታቦር ተሾመ ዘሩሁን፣ (ነፍሰ ኄር) ሊቀ ካህናት ክንፈ ገብርኤል አልታዬ፣ መልአከ ሰላም ዳኛቸው ካሳሁን፣ (ነፍሰ ኄር) መጋቤ ብሉይ ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስ፣ ሊቀ ካህናት ብርሃኑ ገብረ አማኑኤል፣ ወዘተ... ከሊቃውንት ወገን፤ በአርታዒነት መምህር ገብረ ሕይወት እና መምህር ስብሐት የሐዲሳት መምህራን እንዲሁም (ነፍሳተ

[25] መጋቤ ምሥጢር ጌራወርቅ ጥበቡ፣ ትንቢተ ኢሳይያስ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997፣ ገ:10

ኄራን) መልአከ ገነት ገብረ ሥላሴ እና መጋቤ ብሉይ መዘምር የብሉያት መምህራን ተሳታፊ ነበሩ።

(4.2.1.7) የጉባኤው ውሳኔ በአማርኛ (ከመጽሐፉ ገጽ 10 የተወሰደ) እንደ ወረደ፡- "አምላክን በድንግልና ፀንሳ በድንግልና የወለደች እመቤታችን ድንግል ማርያም ከአዳም ዘር የተላለፈ ኃጢአት[26] /ጥንተ አብሶ ያላገኛት/፣ መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌለባት፣ ከመወለዷ አስቀድሞ በአምላክ ሕሊና ታስባ ትኖር የነበረች፣ በሰው ልማድና ጠባይ ከሚደርሰው ሥጋዊ አሳብና ፈቃድ ሁሉ የተጠበቀች፣ ከተለዩ የተለየች፣ ንጽሕት ቅድስተ ቅዱሳን ናት። መኃ.4:7። "ምልዕተ ጸጋ፣ ምልዕተ ክብር ሆይ! ደስ ይበልሽ!" ተብላ በመላእክት አንደበት በቅድስናዋ ትመሰገናለች /ሉቃ.1:28-30/። እመቤታችን በውስጥ በአፍአ፣ በነፍስ በሥጋ ቅድስት ስለ ሆነች እግዚአብሔር ለልጁ ማደሪያ መርጡዋታል። አምላክን ለመውለድ ያስመረጣት፣ ያበቃት፣ ድንግልናዋ ንጽሕናዋ ነው /ሕርያቆስ ቅዳሴ፣ መዝ.131:13/። ንጽሐ ሥጋ፣ ንጽሐ ነፍስ፣ ንጽሐ ልቡና ለእመቤታችን ገንዘቦቿ ናቸው።"

(4.2.1.8) የጉባኤው ውሳኔ በእንግሊዝኛ (ከመጽሐፉ ገጽ 10 የተወሰደ) እንደ ወረደ፡- "Our Lady, the virgin Mary, who conceived and begot Christ in virginity is free from the original sin derived from the descendants of Adam, clean from any sins of the flesh or soul; embedded in the conscience of God before the time of her birth, free and protected from human desires and [frailty]; and the choicest from among the chosen. Such is the Virgin Mary–Pure and Holy of Holies. Song 4:7."

እዚህ ላይ መታወቅ ያለበት ጉዳይ አለ። ይህ አቋም የተላለፈው በጉባኤ ሊቃውንት (ኮሚቴ) ደረጃ ነው። እያንዳንዱ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል ድምጽ ሰጥቶበትና ፈርሞበት የፀደቀ አይደለም። ስለዚህ ውሳኔው ቤተ ክርስቲያኗ እንደ ተቋም ያላትን አመለካከት በማንፀባረቅ ወደር አይገኝለትም ቢባልም "በዚህ ጊዜ (1988 ዓ.ም.)፣ በዚህ (አቡነ ጳውሎስ በሚመሩት) ሲኖዶስ የፀደቀ

[26] እዚህም ላይ ኃጢአት ተላላፊ እንደ ሆነ በሚያስመስል መልኩ የቀረበው ቃል ያስጨንቃል።



ዶግማ ሊሰኝ ግን አይችልም። ውሳኔው በእንግሊዝኛ ጭምር ቢዘጋጅም ለአኃት አብያተ ክርስቲያናት ዶግማችን "ጽንሰታ ለማርያም እንበለ አበሳ አዳም - Imaculate Conception of St.Mary" ተብሎ እንዲያውቁት አለመደረጉን የጉባኤው አባል አቡነ ገብርኤል በ1997 ዓ.ም. በተዘዋዋሪ አረጋግጠዋል።[27] አክለውም አቡነ ገብርኤል ጉዳዩ ተጠንቶ በዶግማ ደረጃ ሲደነገግ እንደሚገባና ከተቻለም ከግብጻውያን የአንጽሖ ብሒል እንድንተባበር መክረዋል። በብፁዕነታቸው አሳብ ከአክብሮት ጋር ልዩነት አለኝ። ልዩነቴን ለብቻው እመለስበታለሁ። ከዚያ በፊት ብሔራውያን ሊቃውንት አንጽሖን ወክለው ያቀረቧቸውን መከራከሪያዎች በትውፊትና በትርጓሜ መጻሕፍት መነጽርነት ንባቤ በፈቀደልኝ መጠን መሞገትን መርጫለሁ - በዚያውም ለየትኛው ብሒል ልቤ እንደሚሸፍት መግለጼ ነው።

## 4.3 የኢትዮጵያውያን ሊቃውንት የአንጽሖ ብሒል በኢትዮጵያዊ ትውፊት ሲፈተሽ

መወድስ ላስቀድም። መወድሱ የደብረ ወርቁ አለቃ ኀበዜ ነው። ትርጓሜው፡- "መንፈስ ቅዱስን በባሕርይዋ ንጽሕት የምትሆን ድንግልን ከነውር ቢያነጻ ከቶም አናደንቀውም። በተግባር ላደፈ (መንጽሒ) ይፈለጋል እንጂ ለጽዱ መነናጸፊያ (መንጽሒ እንዲሆን) ሳሙና ይፈለጋልን? (ኃጢአትን እንደ ሳሙና ሙልጭ አድርጎ የሚያጸዳው መንፈስ ቅዱስ) እኛን (ካጨቀየ) የበደል እድፍ ቢያነጻ ነበር ማድነቅንስ የምናደንቀው።..." ይላል። ምሥጢሩ፡- እመቤታችን እንደ እኛ ያደፈች ሳትሆን ጥንቱን ንጽሕት ስለ ሆነች የመንፈስ ቅዱስ ወደ እሷ መምጣት ለማንጻት አለመሆኑን ያመለክታል። አለቃን እንስማቸው፡-

መወድስ!

"ኢናነክር ኀዲጠ፣ ለመንፈስ ቅዱስ፣
ለንጽሕተ ባሕርይ ድንግል፣ እመ አንጽሐ እምነውር፣
መሐፒልኑ ይትኀሠሥ፣ ለአንተ ጸዕደወ ጸምር፣

[27] አባ ሠረቀ፡ ገ.67

ለርሱሕ፣ ዳዕሙ፣ ይትኀሠሥ በግብር፣
እንክርስ ናነክር፣
እመ እንጽሑ፡ ኪያነ፣ እምርስሐተ ጌጋይ ጽቡር።..." እያለ ይሔዳል።
እመ እንጽሑ፡ ኪያነ፣ እምርስሐተ ጌጋይ ጽቡር።..." እያለ ይሔዳል። እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነው። ከግራ ቀኝ ጥቅስና አመክንዮ እናስተውል! ርእሳችን ጥንተ አብሶ ነው። ከግራ ቀኝ ጥቅስና አመክንዮ በእያሌው የሚደረደርለት ርእስ! እንዲያ ሲሆን ከሁለት አንዱን (እውነት አለበት የሚሉትን) መርጦ መያዝ ግድ ይሆናል። ይህ የነገረ ሃይማኖት ጉዳይ ነው፤ ሦስተኛ አማራጭ መንገድ ይሉት ዘይቤ አያስኬድም። በአንድ ጭንቅላት ሁለት ቆብ ማጥለቅ አይሞከርም። በግሌ እንዲህ ስወጠር፣ ተገዳዳሪ ብሒል በርከቶ አእምሮዬን ሲያናውጸኝ ያደግሁበትን ብሒል መጠለያ አድርገዋለሁ። ያደግሁበትን ብሒል ለመልቀቅ ደግሞ አንድም የያዝኩት ብሒል ስሕተት መሆኑን አቅሜ በፈቀደ መርምሬና አነጻጽሬ መወሰን አለብኝ። በተጨማሪም ሌላኛው ተገዳዳሪ ብሒል ከኖርኩበት ብሒል በተሻለ መልኩ ከመጽሐፍና ከትውፊት የተስማማ መሆኑን ማረጋገጥ እሻለሁ። በዚህ አንጻር እኔ ያደግሁት "መንፈስ ቅዱስ፡ ዐቀባ፡ እምከርሠ እማ" በሚለው ብሒል ነው። መሠረቴ እሱ ነው። መሠረቴን ሲነኩት እንዳቅሜ ባለችኝ የቃለ እግዚአብሔር ትጥቅ መልስ እሰጣለሁ። ይሄን ማድረጌ ለክፋትና ለውግዘት አይደለም፤ እማኝ ልቡናዬ እንዲበረታልኝ ብቻ! በዚህ መንፈስ ሆኜ ከኢትዮጵያውያን ሊቃውንት ለተሰነዘሩ የአንጽሖ ብሒል መከራከሪያዎች የበኩሌን መልስ ለመስጠት እሞክራለሁ። በቀድሞው ቅዱስ ፓትርያርካችን ልጀምር፦

(4.3.1) ለአቡነ ጳውሎስ ፍቅርና አክብሮት አለኝ። በዘመናቸው ስሕተት አልተሠራም ብዬ ባልከራከርም እርሳቸውን የያዝንበት ርኅራኄ የተለየው መንገድ አስደስቶኝ አያውቅም። ስለሆነም እርሳቸው ላይ የሚሰነዘርን ሐሜት ሳላጣራ አልቀበልም። በዚህ ሁኔታ ሳለሁ "እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት!" ብለው ጽፈዋል ማለትን ሰማሁ። የሦስተኛ ዲግሪ ማሙያ (ፒ.ኤች.ዲ) ጥናታቸውን አነበብኩ። ማለታቸውን አረጋገጥኩ። ሁለት ጊዜ አዘንኩ። የመጀመሪያው ኀዘኔ ያን የመሰለ ጽሑፍ በዚህች እርሳቸው ነገሬ ብለው ባሳብራሯት አሳብ የተነካ ሙሉ ለሙሉ እንዳይነበብ ሆኖ ተጥላልቶ መቅረቱ ነው። እመቤታችን ጥንተ አብሶ እንዳለባት የሚገልጹ የአቡነ ሺኖዳ መጻሕፍት እየታረሙ ኢትዮጵያዊውን ትውፊት እንዳይጋፉ ተደርገው ተተርጉመው በስፋት ሲነበቡ እንዳላየን ያን የመሰለ እመቤታችን



በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ማኅበረሰብ ትውፊትና መንፈሳዊ ጽሑፎች ያላትን ሥፍራ በጥልቀት የዳሰሰ ጥናት በዚህች ስርዋጽ ጽሑፋቸው ተጥላልቶ መቅረቱ ያሳዝናል። ሁለኛው ኀዘኔ ራሳቸው አቡነ ጳውሎስ "ጥንተ አብሶ የለባትም" የሚል ኢትዮጵያዊ ምንጭ አስነብበውን ሲያበቁ ተመልሰው ምንም ማጣቀሻ ሳያቀርቡ "ጥንተ አብሶ አለባት" የሚለው ብሒል የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. አቋም እንደ ሆነ አድርገው ማቅረባቸው ነው። ከመጽሐፈ ብርሃን ወስደው በጥናታቸው ያስቀመጡት ኢትዮጵያዊ ብሒል "from the womb of Her mother Hanna, the creater of Adam created, purified and sanctified Mary in order that He might wear Her flesh as His own - አምላከ አዳም ገና ከእናቷ ሐና ማኅፀን ጀምሮ ሥጋዋን ሥጋው አድርጎ ይነሳው (ይለብሰው) ዘንድ ማርያምን አንጽቶ፣ ቀድሶ ፈጠራት" የሚል ነበር።[28] ይህን ጥቅስ ሳይተቹ ነው እንዳለ አስቀምጠውት እመቤታችን ከጥንተ አብሶ ነጻ ነች ብለው እንደማያምኑ በተደጋጋሚ በጥናታቸው ያመላከቱት። ደግነቱ ኋላ በመንበሩ ከተሰየሙ ወዲህ ጉዳዩ በሊቃውንት ደረጃ እንዲመከርበት አድርገው ነባሩን ትውፊት ያፀና ውሳኔ በ1988 ዓ.ም. ተላልፏል፤ እንጂ በጥናታቸው ያስፈሯት የጥንተ አብሶ ንባብስ ታውካለች።

(4.3.2) በእኔ እምነት ከኢትዮጵያውያን የአንጽሖ ብሒል ደጋፊዎች መከራከሪያቸውን ባልቀበለውም በ"ሁሉም ሁሉን ይወቅ" መጽሐፋቸው ከገጽ 157 ጀምሮ የተሻለ ማስረጃ በብዛት ጠቅሶ በማቅረብ ዓለማየሁ ሞገስ ቀዳሚ ናቸው። የማልቀበላቸው ማጣቀሻዎቻቸው በስሱ ይዳሰሱ፦

(1) "ቅዱስ ገብርኤል መንፈስ ይጸልልሻል ብሎ እንደሚያነጻት ተናገረ እንጂ ያለጥንተ አብሶ ትወልጃለሽ አላላትም!" ይላሉ። ለዚህ አሳብ ከላይ አቡነ ማትያስ (በተራ ቍጥር 4.2.1.1) የሰጡት ትርጓሜ በቂ ምላሽ ይመስለኛል። "ይጼልለኪ - ይጸልልሻል" የሚለውን ቃል ትርጉም ወረድ ብለን ለብቻ እናየዋለን።

(2) የቅዱስ ያሬድ "አንጺሖ ሥጋሃ፣ ቀዲሶ ኪያሃ፣ ኀደረ ላዕሌሃ" ተደጋግሞ ይጠቀሳል። ሆኖም ቅዱስ ያሬድ "አንጽሖ" የሚለውን ቃል በዐቀባ

[28] Aba paulos:p,105

ምሥጢራዊ ትርጓሜ ስለት ነው የተናገረው ብለን መናገር ይቻላል:: ያም ቢሆን ደግሞ ቅዱስ ያሬድ "እንጺሖ፡ ሥጋሃ" የሚለውን ቃል የአንጽሖ ቡድኖች ቤሉሉን በሚተርኩብትና የጌታ ሰው መሆን በሚዘክርበት የትስብእት ጸመ ድጓ[29] አይደለም የሠራው:: እንዲያውም በትስብእት ጸመ ድጓ "ለልየ፡ በእዴየ፡ ለሐኰዋ፡ ለድንግል ... ድንግልን እኔው ራሴ በገዛ እጄ አበጀኋት (ማለትም በማኅፀን ሐና አዘጋጀኋት)" ነው የሚለው:: ስለዚህ "እንጺሖ" ማለት በዐቀባ መንፈስ ሆኖ እሱም በጊዜ ጽንሰቷ (ገና በማኅፀን ሐና ዘርና ደም ተዋሕዶ ነሐሴ 7 ቀን ስትፀነስ ጀምሮ) ስላለመሆኑ ማስረጃ የለም:: ቃሉ የግድ ለብሥራቷ ጊዜ ተወስና እንዲነገር አልተባለም፤ በዚያ መልኩም ቅዱስ ያሬድ አልሠራውም::

(3) ከግብረ ሕማማት የጠቀሱት "መንፈስ ቅዱስ ዘወረደ ላዕለ ማርያም አንጽሖ ሥጋ ዚአሃ ለተወክፎ አምላክ" የሚል ንባብ ትርጉም እርሳቸው እንዳሉት አይደለም:: በሊቃውንት ጉባኤ ታይቶ በ2005 ዓ.ም. በታተመው ግብረ ሕማማት "አንጽሖ" የተተረጎመው "ከሦስቱም ግብራት ከለከላት" ተብሎ ነው:: ሦስቱ ግብራት፦ ዘር መቀበል፣ ሩካቤ እና ሰስሎተ ድንግልና (የድንግልና ተፈትሖ) ናቸው::[30] "አንጽሖ" ማለት ከነዚህ ግብራት "ከለከላት" ማለት ነው::

(4) ከቅዳሴ ያዕቆብ ዘሥሩግ የጠቀሱት "ገሊላዊት ሐቀፈተከ ... ነፍሳ ቀደስከ ወሥጋሃ አንጻሕከ" ትርጓሜው ዓለማየሁ ሞገስ በሚሉት መንገድ አይደለም:: አባቶች ይህን ንባብ ሲተረጉሙት "ገሊላዊት እመቤታችን በክንዷ ታቅፋ ያዘችህ ... በነፍስ በሥጋ አነጻሐት::... ጥንቱን ንጽሕት አይደለችምን? ከምን አነጻት? ቢሉ፤ እንዳይቀርባት 'ከለከላት' ሲል ነው" እያሉ 'አንጽሖ'ን መከልከል፣ መታደግ፣ ዐቅቦ ማቆየት በሚል በሚል መንፈስ በሐተታቸው አብራርተውታል::[31]

[29] መጋቢት 29 ቀን
[30] ሃይማኖት አበው ዘሱኑትዩ፤ ምዕ.110፡29፡ ገ.511:: ቅዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.70
[31] መጽሐፈ ቅዳሴ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.435



(5) "አባቶቿ እነ ዳዊት ስለሆኑ በየት አልፋ ከፍዳ እና መርገም ትነጻለች?" ላሉት በአዲስ መስመር እንመለስበት::

(4.3.3) አለቃ አያሌው የሰውን በተራክቦ መባዛትና የመላእክትን እንበለ ሩካቤ የሆነ ተፈጥሮ በማነጻጸር ከአንጽሖ ወገኖች የሚቀርብ ክርክር ሲሞግቱ፦ ... "ብሰዎች ኃጢአት እንደ ተገኘ በመላእክትም አመፃና አመፅኛ ተገኝተዋል:: (እመቤታችን) ከሰማይ የወረደች መልአክ አይደለችም የሚለውም አሳብ ወይም ከሰዎች ከተገኘች የግድ በደለኛ መሆን አለባት ብሎ መፍረድ ትክክለኛ አስተሳሰብ አይደለም ይላሉ::[32] መቼም መፍቀርያን እንስት የሆኑት የዳዊት እና የሰሎሞን ዘር መሆኗ እመቤታችንን ከብሥራተ መልአክ፣ ከብፅዕና እና ከዘለዓለማዊ ድንግልና አላገዳትም:: አባቶቻችንም በዘመዶቿ ፍዳ እንዳልተያዘች በትርጓሜዎቻቸው ማተታቸው ተመልክቷል::[33] ሐተታውን እንደግመውም:: ይልቅስ እመቤታችን በእነ ዳዊት ፍዳ እንዳልተጨመረች ለማስረገጥ የታላቋን ሊቅ የእማሆይ ገላነሽ ዋዜማ ምስክር እንጥራ::

**ዋዜማ!**

ሳዶቅ ወብእሲቱ፤
እመ ወለዱ ሕጻነ፤ እስመ አልቦሙ ውሉድ፣
ለሕጻን፤ ሐቀፋ፤ ሱራፌ በእድ፣
ወኢሐቀፋ ዳዊት፤ ዘመደ ሥጋሃ ዋሕድ፣
አኮኑ ይኄይስ፤ ቅሩብ ባዕድ፣
እምርትቅ፤ ዘሥጋ ዘመድ::

ትርጓሜውን እንለፈው:: ምሥጢሩ ግን፦ "በቤት ውስጥ ሌሎች ልጆች ወይም ረዳት የሌላቸው ወላጆች ልጅ በሚወልዱበት ጊዜ እናትየዋ ሥራ ስትይዝ ባዕድ ቢሆንም የጎረቤት ሰው ሕጻንዋን ሊታቀፋት ይችላል:: እንደዚሁም ሳዶቅ የተባለው ኢያቄም (ሳዶቅ የኢያቄም ሌላ ስም ነው) እና ሐና ልጅ የሆነችው ቅድስት ማርያም ሱራፌ የተባለው መልአክ ታቀፋት፤ ማለት ቅድስት ማርያም እንደ መልአክ ንጽሕት ናት:: ዳዊት ግን አልታቀፋትም፤ ሲባል ቅድስት ማርያም ከዳዊት ዘር ብትወለድም የዳዊት

[32] አለቃ አያሌው፤ ምልጃ ዕርቅና ሰላም፡ገ.57
[33] ከላይ በተራ ቁጥር 4.2.1.5 ያለውን ተመልከት

በደል የለባትም እንደሆነ ሊቅዋ አመስጥረዋል።"[34] ከወጣቶቹ የነገረ መለኮት መምህራንም አንዱ ዓለም ዳግማዊ "ምንም እንኳ እመቤታችን ከአዳም ባሕርይ የተገኘች ዘርዐ አዳም ብትሆንም የአዳም ገንዘብ የሆነው የኃጢአት ዝንት ከጽርየቷ (ከንጽሐ ባሕርይዋ፣ ከቅድስናዋ) አላሳደፋትም። ምክንያቱም የዕንቁን ባሕርይ የተገኘበት ቦታ ጽርየት አይለውጥምና ነው!" ብለዋል።[35] በሌላ አገላለጽ፦ ወርቅ ከአፈር ውስጥ ስለተገኘ የግድ አፈርነት አለው አይባልም እንደ ማለት ነው።

(4.3.4) ከኢትዮጵያውያን የአንጽሖ ብሒል አራማጆች በተደጋጋሚ የሚሰነዘረው፦ እመቤታችን ጥንተ አብሶ የለባትም የሚል አነጋገር ካቶሊካዊ ነው፣ የቢላግዮስ አስተሳሰብ ነው፣ አለቃ ታዬ በጣሊያን ጊዜ ወደ ኢትዮጵያ ያስገቡት አዲስ ብሒል ነው' የሚል ነው።[36] ቢላግዮስ በመሠረቱ የጥንተ አብሶን ብሒል ሙሉ ለሙሉ የማይቀበል ሰው በመሆኑ በሁሉም አብያተ ክርስቲያናት በ431 ዓ.ም. የተወገዘ መሆኑ ተገልጹዋል። ኢትዮጵያውያን የዐቀባ ብሒል ደጋፊዎች ከጌታና ከእመቤታችን በቀር በሌላው ሰው ላይ ጥንተ አብሶ አልነበረም አይሉም። ስለዚህ እነርሱን "ቢላግዮስ" ማለት ቅንነት ማጣት ነው። አለቃ ታዬ በካቶሊካዊነት አይታሙም፤ ባይሆን የፕሮቴስታንት ሚሽነሪዎች ተከታይ የነበሩ መሆናቸው በአደባባይ የተነገረ ነው።[37] ስለሆነም አለቃ ታዬ በካቶሊካዊ መንፈስ በኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ላይ ተጽዕኖ የሚያሳርፉበት ዕድል አልነበረም።

(4.3.5) የዐቀባ ብሒል በአንጽሖ ብሒል ደጋፊዎች እንደሚባለው ካቶሊካዊ ሳይሆን የራሱ መጽሐፋዊና ትውፊታዊ መሠረት ያለው መሆኑን ፕ/ር ጌታቸው ይገልጻሉ። ቃላቸውን እንዋስ! "Ethiopian Tradition clearly stated that M[ary] was free from any sin. This can be understood as some equivalent of the Cahtholic doctrine of the Immaculate Conception with out ... however implying the Western teaching about the Original Sin, which is not found in Ethiopia" -

[34] ሊቀ ኅሩያን በላይ መኮንን፣ የቅኔዋ ንግሥት፣ 2006 ዓ.ም.፤ ገ፣41
[35] ወላዲተ አምላክ በነገረ ድኅነት፣ገ.173።
[36] ሊ/ብ አስተርአየ፣ ከላይ በ3.4.11 የተጠቀሰው እና አባ ሠረቀ፣ ገ.46
[37] መርስዔ ኀዘን ወልደ ቂርቆስ፣ ትዝታዬ፡ ስለ ራሴ የማስታውሰው፣ 2002 ዓ.ም.፤ ገ.146



"ኢትዮጵያዊው ትውፊት በግልጽ ማርያም እንበለ ኃጢአት እንደ ነበረች ይገልጻል። ይህም በኢትዮጵያ የማይገኘውን የምዕራባውያን የጥንተ አብሶ ብሒል ባያጣቅስም [ኢትዮጵያዊውን የዐቀባ ብሒል] በመጠኑ ከካቶሊኮች ጽንሰታ [ለማርያም] እንበለ አበሳ [አዳም] ጋር አነጻጽሮ/ አመሳስሎ መረዳት ይቻላል" ሲሉ አባ ሕርያቆስ በቅዳሴው "እ ድንግል እኮ በፍትወተ ደነስ ዘተፀነስኪ" ያለውን ጠቅሰው አስፈርዋል።[38]

(4.3.6) በተጨማሪነት "መንፈስ ቅዱስ ዐቀባ እምከርሠ እማ" ካቶሊካዊ ብሒል ነው የሚለውን በሚመለከት አቡነ ማትያስ ለነ ሊቀ ብርሃን አስተርአየ በተቃውሞ የጻፉትን ምላሽ እንደ ወረደ ላቅርበው፦

"የ ... Immaculate Conception ትክክለኛ ትርጉም... the Virgin Mary was conceived free of Original Sin ... ሲሆን ወደ አማርኛ [ሲመለስ] 'ድንግል ማርያም ከጥንተ አብሶ (በዘር ይተላለፍ ከነበረው የውርስ ኃጢአት) ነጻ ሆና ነው የተፀነሰችው' የሚል ሆኖ ይገኛል። የእኛስ አባባል ከዚህ የተለየ ነው ወይ? በፍጹም የተለየ አይደለም።[39] እንግዲህ እዚህ ላይ ስለ ድንግል ማርያም ንጽሕናና ቅድስና ያለን አስተሳሰብ ከካቶሊኮች ጋር በትርጉም ስለ ተገናኘ እኛ ኦርቶዶክሶች ነን ካቶሊክ የሆነው? ወይስ ካቶሊኮች ናቸው ኦርቶዶክሶች የሆኑት? እንግዲህ ልብ በሉ፤ ቅድስት ድንግል ማርያም የአዳም ውርስ ኃጢአት አላገኛትም የሚለውን እምነታችንን ካቶሊኮች ተቀብለውታልና የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያንን አባባል ለመለየት ሲባል

[38] Encyclopaedia Aethiopica, Volume 3, 2007, p.809.
[39] የኛ ብሂል እንደ ካቶሊኮች፦ (1) ኃጢአት ይወረሳል የሚል ሆኖ አይታይም። (2) ነፍስ ከወላጆ ትከፈላለች የሚለው ብሒላችን ለእያንዳንዱ ዕንስ ነፍስ ትፈጠርና ከሥጋ ስትዋሐድ አበሳው አብሮ ይቆራኛታል ከሚለው ካቶሊካዊ ብሒል ጋርም አይጣጣምም። (3) የሕጻናት ጥምቀት ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ ነው የሚል ባህል አናንፀባርቅም። ስለሆነም የዐቀባ ብሒላችን እንደ መርሕ ከካቶሊክ ጋር ይቀራረባል ይባል እንደ ሆነ እንጂ አባታችን እንደሚሉት "ተመሳሳይ ነው" ለማለት ይከብዳል። እርሳቸው ብቻ ሳይሆኑ ፕ/ር ጌታቸውም ከላይ በተጠቀሰው ምንጭ ገጽ 810 ላይ በ1988 ዓ.ም. ጉባኤ የወጣውን ጥንተ አብሶ የተመለከተ ጽሑፍ በማመሳከር የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. "ሙሉ ለሙሉ ከካቶሊኮች የተመሳሰለ አቋም" እንደ ያዘች ገልጸዋል። ሆኖም በእኛና በካቶሊኮች መካከል የተጠቀሱት ልዩነቶች ስላሉ ሙሉ ለሙሉ ተመሳሳይ ብሂል እንከተላለን ማለት ይከብዳል።

ድንግል ማርያም የውርስ ኃጢአት ነበረባት ነው የቀሲስ አስተርአየ ትምህርት አይገርምም?" እያሉ በግርምት ይጽፋሉ አቡነ ማትያስ።[40]

(4.3.7) ትርጓሜ ወንጌለ ማቴዎስ "እንጽሐ"ን "ከለከላት" ብሎ ይተረጉመዋል። እንዲህ። ማቴ.1:18 "ዘእንበለ ይትቃረቡ ተረክበት ጽንስተ እንዘ ባ ውስተ ማኅፀና እመንፈስ ቅዱስ ... (ለዮሴፍ በታጨች ጊዜ) ሳይገናኙ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ፀንሳ ተገኘች[41]፤" ይላል። ስለሆነ፦ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ፀንሳ ተገኘች ማለት ምን ማለት ነው? ትርጓሜው መልስ አለው። "እመንፈስ ቅዱስ' ቢል በመንፈስ ቅዱስ ተከፍሎ [ክብር ይግባውና ተባዕታይ ዘር ማመንጨት] ኑሮበት አይደለም፤ አነጻት ሲል ነው እንጂ ... አነጻትም ቢል ኑሮባት አነጻት ማለት አይደለም፤ ከለከላት ሲል ነው እንጂ ..." በማለት የእንጽሐን ምሥጢራዊ ትርጉም አስቀድሞ ከኃጢአትና ተራክቦ "መከልከል" አድርጎ ፈትቶታል።[42] በመጻሕፍቶቻችን በተለይም በሃይማኖተ አበው በተደጋጋሚ እመቤታችን ጌታን "በግብረ መንፈስ ቅዱስ ፀንሳ ተገኘች" ተብሎ ተቀምጧል። ይህም ማለት፦ ትስብእትን ከእርሷ ሥጋዊ ባሕርይ ከፍሎ ከመለኮቱ ማዋሐድ ለመንፈስ ቅዱስ ተሰጥቶ ስለሚነገር ነው "ወእናሚ ሁኑ (ሠሪውም) መንፈስ ቅዱስ" እንዲል።[43]

(4.3.8) ነገረ ማርያምን ከምሥጢረ ሥጋዌ አዛምዶ በጠራ ቋንቋ በመግለጽ የውዳሴ ማርያም ንባብና ትርጓሜ አስደማሚ ነው። እንሒድበት። በማክሰኞ ውዳሴ ማርያም "ተፈሥሂ አ! መዓዛ እንተ አልባቲ ነውር ፍጽምት ዘእልባ ርስሐት" የሚለውን ንባብ አበው በትርጓሜ "አደፍ ጉድፍ የሌለብሽ ንጹሕ የሽቱ ዕቃ!... ደስ ይበልሽ። የሽቱን ዕቃ ጢስ እንዳይተንበት፣ ትቢያ እንዳይበንበት ቤት ሰፍተው፣ ሰቅለው፣ ተንከባክበው ያኖሩታል። እርስዎንም 'መንፈስ ቅዱስ፡ ዐቀባ፡ እምከርሠ እማ' ይሏታልና"[44] ከዚሁ ከማክሰኞ ውዳሴ ማርያም እንጨምር። "ኮንኪ፡ አጽቀ፡ ንጹሐ"ን አበው ሲተረጉሙልን "ያቺ (የአቤሜሌክ በለስ) ስሳ ስድስት ዘመን ቅጠሏ ሳይጠወልግ፣ ደሟ



ሳይንጠፈጠፍ እንደ ተገኘች እመቤታችንም በስሳ ስድስተኛው ትውልድ ንጽሐ ጠባይዕ ሳያድፍባት ተገኝታለችና። 'ወበከመ ነፋሕኩ ውስተ ገጹ ለአዳም ከማሁ አንቲኒ ሀሎኪ ወኢረሳሕኪ (በአዳም ፊት እፍ እንዳልኩበት እንዲሁ አንቺም ሳትተዳደፊ አለሽ)" ይሏታል - ባሕርይዋን አዳም ከመውደቁ በፊት ከነበረው ንጽሐ ባሕርይ ጋር እያነጻጸሩ።[45]

(4.3.9) አባ ጊዮርጊስ ደግሞ ንጽሕናዋን ከሔዋን ርግማን ጋር በማነጻጸር እመቤታችንን "... ስለ ተሰጣትም የእግዚአብሔር ጸጋ የሔዋን መርገም በእርሷ ላይ ተቋረጠ። እንዲህ ያለ ስጦታ ለአዳምና ለዘሩ እስከ ዘላለም ለሌላ አልተሰጠም" በማለት ይገልጸታል።[46] ቅዱስ አትናቴዎስ እንዲሁ "ሥጋችንን ሥጋው አደረገ። ከወንድ ዘር በሆነ ተራክቦ ያልተዳደፈ ሥጋን ነውር ከሌለባት፣ አበሳ ከማያውቃት ድንግል ነሳ። የፍጥረታት ሁሉ አስገኝ ልዑል አምላክ [እግዚአብሔር ወልድ] መቅደሱ ይሆነው ዘንድ ይህን [በተራክቦ ያልተዳደፈ] ሥጋ ለራሱ አዘጋጀ ... He took our body, and not only so, but He took it directly from a spotless, stainless virgin, without the agency of human father–a pure body, untainted by intercourse with man. He, the Mighty One, the Artificer of all, Himself prepared this body in the virgin as a temple for Himself." በማለት የድንግልን ቅድመ ጽንሰተ ክርስቶስ የነበረ ንጽሕናና ቅድስና ይመሰክራል።[47]

(4.3.10) የዐቀባ ብሒል ከ1984 ዓ.ም. ወይም ከአለቃ ታዬ ወዲህ ነው የመጣው የሚለውን ክርክር ከላይ የቀረቡት ትርጓሜዎች ይሞግታሉ። በአቤሜሌክ ምሳሌ ላይ ወስጋ ተወልደው፣ ጎጃም ኤልያስ ላይ ጉባኤ ዘርግተው እነ አቡነ ቴዎፍሎስንና ቀኝ ጌታ ዮፍታሔን የመሳሰሉ ሊቃውንት በማፍራት ለአገርና ለሃይማኖት የተረፉት እና በ1938 ዓ.ም. ያረፉት ቀንዲላችን የኔታ ገ/ሥላሴ ከንቱ ያደረጉትን ሥላሴ ቅኔ ሰሙን ከወርቁ አንጥረን ተረድተን ብንጨምርበት "በስንበት ላይ ደብረ ዘይት" ይሆንልናል። ይቀጥሉ የኔታ፦

[40] አባ ሠረቀ፡ ገ.40
[41] መጽሐፈ ምስጢር፡ገ.163
[42] ወንጌል ቅዱስ ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.54
[43] ቅዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.38
[44] ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.63

[45] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.46
[46] መጽሐፈ ምሥጢር፡ ገ.163
[47] አትናቴዎስ፣ በተራ ቍጥር 2.5.8 የተጠቀሰው፡ ገ.15

ሥላሴ!

እኮነት ምሳሌሃ፤
ዐጽቀ አቤሜሌክ ለድንግል፤
እስመ ዘአቤሜሌክ ዕፅ፤ ዐቃቢተ ርእሱ እንስሳ፣
በከየት፤ ብኪያተ ደም፤ ክራማተ ስድሳ፣
ባሕቱ ድንግል፤ ንጽሕተ ኵሉ አበሳ፣
አርአየት ደመ፤ እምቅድመ ጽንሳ፣
እስከ አመ ወለደት ወልደ፤ ፍሬ ከርሳ፣
ዐቃቢሁ፤ እመኒ ለርእሳ።

የቅኔው መልእክት፡- "የአቤሜሌክ (የተቆረጠች) የበለስ ዐጽቅ (ቅጠል) የእመቤታችን ምሳሌ ልትሆን አትችልም። ምክንያቱም በለሷ ስሳ ስድስት ዘመን ደሟ ሳይደርቅ ቆይታለች። 'ንጽሕተ ኵሉ አበሳ' የሆነች እመቤታችን ግን ደም አሳየችም ማለት የሴቶች ልማድ (ወርሐዊ ግዳጅ) የለባትም። ለእርሷ ጠባቂዋ እርሱ ነውና" ማለት ነው።[48] ሊቁ በውዳሴ ማርያም እንድምታ የተጠቀሰችው የአቤሜሌክ ዕፅ በእመቤታችን መመሰል ሕፁፅ ቢሆንባቸው፤ ባያጠግባቸው ከምሳሌው በላይ አስቀምጠዋት ስለ ንጽሕናዋ ተቀኙ። "ንጽሕተ ኵሉ አበሳ" የሚለው ሁለንተናዊ ቃል የዐቀባን ትውፊት በሊቃውንቶቻችን ዘንድ ጥልቅ መሠረት መያዝ ያሳያል።

## 4.4 እመቤታችን ጥንተ አብሶ "አለባት/ የለባትም" ስንል ማንጠር ያለብን ቁልፍ ቃላት

እንጽሐ እና ዐቀባ ያላቸውን ትርጓሜ በዐበይት አርእስቱ ሥር ለማየት ተሞክሯል። ከእነርሱ በተጨማሪ በጥንተ አብሶ የግራ ቀኝ ብሒሎች ላይ በስፋት የሚነሡ ቁልፍ ቃላትን በዚህ ንዑስ ርእስ ሥር ለመዳሰስ ይሞከራል።

### 4.4.1 "ጸለለ!"

[48] የኢትዮጵያ ቋንቋዎች አካዳሚ፤ የግእዝ ቅኔያት የሥነግጥም ቅርስ፤ 1984 ዓ.ም.፤ ገ.118



(4.4.1.1) በኢትዮጵያውያን ሊቃውንት እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት/ የለባትም በሚለው ክርክር ውስጥ አጨቃጫቂው ሐረግ በሉቃ.1፡35 የተቀመጠው "መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ፤ ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ" የሚል ንባብ ሲሆን ቁልፉ ቃል ደግሞ "ጸለለ - ይጼልለኪ" ነው። ቃሉ ሲጠብቅና ሲላላ ሁለት ፍችና የግስ እረባብ መንገድ አለው። በግእዝ የግስ አረባብ ዘዴ ስምንት ዓይነት ዐመሎች (የግስ አርእስት/ ቤቶች/) አሉ። "ጸለለ" ሲላላ ቤቱ "የቀተለ ቤት" ይባላል። የቀተለ አረባብ፡- "ቀተለ - ገደለ፣ ይቀትል - ይገድላል፣ ይቅትል - ይገድል ዘንድ፣ ይቅትል - ይግደል፣ ቀቲል/ ቀቲሎት - መግደል፣..." እያለ ይሔዳል። "ጸለለ" ሲላላ (ሁለቱ የ"ለ" ፊደሎች ሳልተው ሲነበብ) አካሄዱ ከ"ቀተለ" ጋር ተመሳሳይ ነው ('ጸ' ፊደል ላይ ነጠላ ትእምርተ ጥቅስ ስላደረኩባት ልዩነቱን ለማወቅ የፊደሏን መልክ አቀያየር ማስተዋል ይገባል)። "ጸለለ፣ ይጼ'ልል፣ ይጽልል፣ ይጽልል፣ ጸሊል/ ጸሊሎት፣ ጸሊል፣ ምጽላል..." እያለ ይረባል። "ጸለለ" ላልቶ ሲነበብ ትርጓሜው፡- "መዋለል፣ መጥራት፣ በአየር ወይም በውኃ ረቦ ተዘርግቶ መሄድ ... አጽለለ፡- አጠራ፣ አጠለለ፣ አሰፈፈ፣ አንጓለለ፣..." ይሆናል።[49] ግሱን በቅርብ የአንዲት ሴት አንቀጽ (2ኛ መደብ/ 2nd person singular/) ስናረባው "ጸለልኪ፣ ይጼ'ልለኪ፣ ይጽልልኪ..." ይሆናል አካሄዱ። ይሄ ደግሞ በሉቃስ ወንጌል 1:35 እና በአዋልድ መጻሕፍቶቻችን የሰፈረውን "ይጼልለኪ" አያስገኝም። ስለዚህ ሌላ መንገድ እንፈልግ።

(4.4.1.2) "ጸለለ"ን አጥብቀን እናውርደው። ሁለቱ የ"ለ" ፊደሎች ጠብቀው ሲነበቡ ግሱ "የቀደሰ ቤት" ይሆናል። "ቀደሰ - አመሰገነ፣ ይቄድስ - ያመሰግናል፣ ይቀድስ - ያመስግን ዘንድ፣ ይቀድስ - ያመስግን፣ ቀድሶ/ ቀድሶት - ማመስገን፣ ቅዱስ - የተመሰገነ፣ ቅዳሴ - ምስጋና" ጸለለ ጠብቆ ሲወርድ "ጸለለ፣ ይጼ'ልል፣ ይጸልል፣ ይጸልል፣ ጸልሎ/ ጸልሎት፣ ጽሉል፣ ጽላሌ..." ከቀደሰ ጋር ተመሳሳይ ነው። ትርጓሜውም፡- "መጽለል፣ በላይ ሆኖ ማጥላት፣ ጥላ መሆን፣ ማልበስ፣ መከደን፣ መሸፈን፣ መከለል፣ መጋረድ፣..." እያለ ይሔዳል።[50] በቅርብ የአንዲት ሴት አንቀጽ (2ኛ መደብ ወይም /2nd person singular/) አረባብ ስንጠቀም "ጸለልኪ፣ ይጼ'ልለኪ፣

[49] ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፡ ገ.755 ፡፡ "ላ" የምትል ፊደል አለች አላልተህ አንብብ ለማለት፤
[50] ዝኒ ከማሁ፡ ገ.756፡፡ "ጥ" የምትል ፊደል አለች አጥብቀህ አንብብ ለማለት፤

ይጸልለኪ፣..." ነው እኮሌዱ። በሉቃ.1:35 ባለው የቅዱስ ገብርኤል "ይጼ'ልለኪ" አነጋገር የሚስማማው አረባብ ሁለተኛው በቀደሰ ቤት ጠብቆ የወረደው የ"ጸለለ" ግስ መሆኑ ግልጽ ነው። ጸለለ ጠብቆ የሚሰጠውን ትርጉም በሉቃ.1:35 ተክተን ስናነበው "የልዑል ኃይል 'ይጋርድሻል፣ በላይ ሆኖ ያጠላልሻል፣ ጥላ ይሆንሻል፣ ያለብስሻል፣ ይከድንሻል፣ ይሸፍንሻል፣ ይከልልሻል" የሚል ትርጉም ይሰጣል። "ማንንጻል፣ ማጥራት፣ ማጥለል" የሚል ግስ እና ካልአይ አንቀጽ (ይ'ጸ'ልለኪ) ለእመቤታችን በፍጹም አይነገርም፤ ከተነገረም ኢመጽሐፋዊ ነው።

(4.4.1.3) ግእዝ በብዛት ሲጠቀስ "ተረት ተረት" ለማለት የሚፋጡት "አፈ ሊቃውንት" አሉ። ስለዚህ የእንግሊዝኛውን አቻ ትርጓሜ እናምጣ - ያውም የእንግሊዛዊው ንጉሥ ያዕቆብ እትም የሚባለውን - King James Version (KJV):: ሉቃ.1:35 በእንግሊዝኛ "The Holy Ghost shall come upon you thee, and the Power of the Highest shall 'overshadow' thee" ተብሎ ሰፍሯል። ለ"ይጼ'ልለኪ" የእንግሊዝኛው አቻ ትርጉም "overshadow" ነው። ይኸውም፡- to shelter, to protect - ጥላ መሆን፣ (አስቀድሞ) መጋረድ ተብሎ ይፈታል። ስለዚህ "ይጼ'ልለኪ" ማለት እመቤታችን የቀደመ መርገም ኑሮባት በኃይለ ልዑል መንጻቷን ሳይሆን በኃይለ ልዑል "ጽላሌ" (መጋረድ) መጠበቋን፣ መሸፈኗን፣ ከኃጢአት መከለሏንና መከልከሏን ነው የሚያሳየው። ይህም "ይጼልለኪ" ከእንጽሖ ይልቅ ለዐቀባ ብሒል እንደሚቀርብ ያሳያል። ለዚህ ቃል ትርጓሜ ተጨማሪ ተዛማጅ ማመሳከሪያ ካስፈለገ ዘጸ.40:32፣ ማቴ.17:5፣ ማር.9:7 ሉቃ.9:34 ማየት ይቻላል። ሁሉም ጥቅሶች "ጸለለ፣ ጸለሎሙ" የሚለው ግስ መጋረድ ወይም መከለል (overshadow) ተብሎ የሚፈታባቸው ናቸው።

ሉቃ.1:35 ላይ ሌላ ነጥብ አለ። ለመሆኑ እመቤታችንን ለመጋረድ /ለመጠበቅ/ ለመጸለል ይመጣል ሲል ቅዱስ ገብርኤል የተናገረለት "የልዑል ኃይል - ኃይለ ልዑል" ማን ነው? መተርጉማን ወንጌል እግዚአብሔር ወልድ ነው ይላሉ።[51] በሌላ በኩል ቀደም ሲል እንዳየነው ድጓው፣ ቅዳሴ ያዕቆብ ዘሥሩግና ግብረ ሕማማት "ይጼልለኪ" ማለትን ለመንፈስ ቅዱስ ሰጥተው

[51] ቅዱስ ወንጌል ንባቡና ትርጓሜው፡ ገ.330



ይናገሩታል። አይጣላምን? ብንል አይጣላም። ከሦስቱ አካላት ሥጋ ሰብእን የለበሰው እግዚአብሔር ወልድ ብቻ መሆኑን እስካላፋለስን ድረስ መከለል /መጋረድ/ እንዱ ከአንዱ ተለይቶ የሚሠራው ሥራ ስላልሆነ አይጣላም፤ "አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ይኬልሉ" እንዲል።[52]

(4.4.1.4) ይህን ቃል በታትኖ ለማየት አስፈላጊ የሆነው አሁን ላይ ልቡ ሸፍቶ ተሐድሶ ለተባለው ኢ-ኦርቶዶክሳዊ አስተሳሰብ ያደረ የቀድሞ ወንድማችን "ጸለለ" የሚለውን ግስ የአወራረድ ባሕርይ በቅጡ ሳያጤን የመጀመሪያውን ላልቶ ሲነበብ የሚገኝ ትርጉም አንጠልጥሎ "እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት፤ መንፈስ ቅዱስ የማጥለል፣ የማጣራት፣ የማንንጻል ተግባር ካከናወነ በኋላ እርሷ ያው የውርስ ኃጢአተኛ፣ ከእርሷ የሚወለደው ግን ቅዱስ ሆኗል!" ሲል ያልተባለ ብሒል በማምጣቱ ነው። ወንድማችን "ጸለለ" ሲጠብቅና ሲላላ ያለውን ልዩነት ፍንትው አድርገው ከነ አረባቡ የገለጹትን አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ በማስረጃነት ይጠቀማል። ሆኖም "ይ'ጸ'ልለኪ" እና "ይ'ጼ'ልለኪ" ያላቸውን ልዩነት ባለማየቱ "ዐይን: በሙ: ወኢይሬእዩ" ብለን እናልፈዋለን። ሰውየው ብዙ ነገር ቢስተም ከስህተቱ የሚማር ከሆነ መምህር ኃይለ ማርያም ምሥጢረ ሥጋዌ ሳይቀር የሚያፋልስ እንጉል መራቀቁን ተችተው ሸጋ ምላሽ ሰጥተውታል።[53]

ይህ ሰው ያመጣው ብሒል ከላይ ካየናቸው የየትኛውም የእንጽሐ ብሒሎች አይገጥምም። እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት የሚሉ የአገራችን ሊቃውንትም ቢሆኑ ከብሥራተ መልአክ በኋላ እመቤታችን "ያው የውርስ ኃጢአተኛ ሆና ቀይታለች" ሲሉ አልሰማንም። "እንጓለለ፣ ተንጓለለ" የሚል እንጎለሌ ውስጥ ሲገቡ አላየንም። በዚህስ ማርቲን ሉተርም አላማት። እሱ'ማ "... so that while the soul was being infused, she would at the same time be cleansed from original sin ... And thus, in the very moment in which she began to live, she was without all sin - ነፍሷ ከሥጋዋ በተገናኘች ቅጽበት ከጥንተ አብሶ ነጽታለች፤ ስለሆነም ሕላዌ ካገኘችበት ጊዜ ጀምሮ (ሕላዌ የሚጀምረው ከጽንስ መሆኑ ግልጽ ነው)

[52] ቅዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው ቁ 64
[53] መምህር ኃይለ ማርያም፣ "ሐውልተ ስምዕ"፡ ከገ. 174-179

ከኃጢአት ሁሉ ንጽሕት ነበረች፤" ነው የሚለው::[54] ይህን አልፎ እላፊ መናገር ሐዋርያው በሮሜ.1:21 "ወተጸለለ ልቦሙ በኢያእምሮ" ያለውን በራስ ላይ ለማስተርጎም ይሆናል።

4.4.2 "ፈጠረ!"

(4.4.2.1) የእመቤታችን ጽንሰት እና የጌታ ከሰማይ ወርዶ በተዋሕዶ ሰው መሆን በሃይማኖተ አበው በተደጋጋሚ "ፈጠረ" በሚል ግስ ይገለጻል። ምሳሌዎች እሉን። እንያቸው፦

(1) "ከንፁሕ ዘር የተፈጠረች ድንግል" ይላታል ቅዱስ ኤራቅሊስ::[55]

(2) "ከሥጋ ከመጀመሪያው ሰው ከአዳም ከአብርሃም ከዳዊት ከተገኘ ባሕርይዋም ኃጢአት የሌለበት፤ በነፍስ በሥጋ ፍጹም የሆነ አካልን ሊዋሐደው ፈጠረ"[56] የቅዱስ ቂርሎስ ቃል በመልእክ ብርሃን አድማሱ መድኅኑ እሚን[57] ተሸሽገው ደረቅ ንባብ በመያዝ ለስም አጠራሩ ምስጋና ይሁንና "የንጹው ትስብእት" ነው ለሚሉ ሽጋ መደሻ ነው፤ ምክንያቱም እሷም (ጌታን ከመፀነሰዋ አስቀድሞም) በንጽሐ ባሕርይ እንደ ነበረች ይናገራል።

(3) "ጌታ የዚህችን ድንግል ንጹሕ ሥጋዋንና ንጹሕ ነፍስዋን ባገኘ ጊዜ ነፍስ ያለችውን ሥጋ ሊዋሐደው ፈጠረ::"[58]

(4) "ከፈጠራት ጀምሮ በምንም በምን ከድንግልናዋ አልተለወጠችም::"[59]

ከላይ የተገለጹት ምንባባት ቁልፍ ቃል የሆነው "ፈጠረ" ትልቁ መልእክት ወይም ምሥጢራዊ ፍቺ "ጽንሰት" ነው። እመቤታችን "ተፈጠረች" ስንል

[54] Martin Luther's Works, vol 4, p. 694 ወይም http://catholicbridge.com/catholic/mary_conceived_without_sin_immaculate_conception.php
[55] ሃይማኖተ አበው ዘኤራቅሊስ ምዕ.48:31፥ ገ.157
[56] ሃይማኖተ አበው ዘቂርሎስ ምዕ. 70:20፥ ገ.237
[57] መልእክ ብርሃን አድማሱ፤ መድኅኑ እሚን፡ገ.16
[58] ሃይማኖተ አበው ዘዮሐንስ አፈወርቅ ምዕ.66:14፥ ገ.237
[59] ሃይማኖተ አበው ዘቴዎዶጦስ ምዕ.53:22፥ ገ.174



ተጸነሰች ማለት ነው። የሰው ሕላዌ ተጀመረ የሚባለው ሲጸነስ መሆኑን ደጋግመን ተናግረናል። ነቢዩ ኢሳይያስ "የፈጠረህ ከማኅፀንም የሠራህ የሚረዳህም እግዚአብሔር" ማለቱ ጽንሰት እንደ ፍጥረት ስለሚታይ ነው (ኢሳ.44:2)። ኢሳይያስ በምዕራፍ 49:5 "ከማኅፀን ጀምሮ የሠራኝ ሲል ከአባቱ ዘር፣ ከእናቱ ደም አዋሕዶ በሥጋና ነፍስ የወላጆ ክፋይ ሰው አደረገኝ ማለቱ ነው።

(4.4.2.2) የ"ፈጠረ" ትርጓሜ ፈጠራ እንዳይመስልብን አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌን ጠርተን ቃሉን ያፍረጥርጡት። "ፈጠር፦ መፍጠር፣ ማስገኘት፣ ካለመኖር ወደ መኖር ማምጣት፣ ግብር እምግብር መሥራት፣ ማድረግ፣ ማበጀት፣ ማዘጋጀት፣ አዲስ ነገር ማውጣት፣ መውለድ" ይሉናል::[60] የሰው ሥጋና ነፍስ አዳምን በመፍጠር፣ ሔዋንን በመሥራት ከተከናወነ በኋላ በቀጠለው ሒደት ሌላው ትውልድ የተገኘው፦ በመራባት፣ በመዋለድ፣ ግብር እምግብር፣ በዘር እየተባዛ እንጂ ከስድስት ቀናት የሥነ ፍጥረት ክንውን ውጭ ፈጣሪያችን ዐዲስ ፍጥረት አለመፍጠሩን በመግቢያችን ስለ ጥንተ ነፍስ ስናወጋ ተነጋግረናል። ይህ ሕገ ተፈጥሮ ለእመቤታችንም ይሠራል። "ተፈጠረች" ስንል ከኢያቄም ዘር፣ ከሐና ደም ተከፍሎ በተከናወነው ጽንሰት ነፍሷም እንደ ሥጋዋ አብራ በተከፍሎ ተገኝታ ተጸነሰች ማለት ነው። ስለዚህ "ሥጋዋን ሊዋሐደው ፈጠረ፣ ከፈጠራት ጀምሮ ድንግልናዋ አልተለወጠም፣ ድንግል ፈጣሪዋን ወለደችው፤ እርሱም እናቱን ፈጠረ..." ሲባል ከጽንሰቷ ጀምሮ በቅድስና በንጽሕና እንደ ተጠበቀች ያሳያል። ሆኖም አፈጣጠሯ ከሰው በተለየ ሁኔታ ያለእናት እና አባት የተከናወነ ነው እንልም፤ "በሩካቤ፡ ዘበሕግ፡ እምሐና ወኢያቄም ተወለድኪ" እንላታለን እንጂ::[61]

(4.4.2.3) ተሐድሶዎች ባመጡት ፈሊጥ ጌታ ከእመቤታችን የነሣውን ሥጋ ብቻ አንጽቶ እርሷን ግን በጥንተ አብሶ ትኖር ዘንድ እንደ ተዋት ይተርካሉ። ይህችን ቅሰጣቸውን አስቀድሞ የተረዳ የሚመስለው ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ ግን "ጌታችን የዚህችን ድንግል ቅዱስ ሥጋዋንና ንጽሕት ነፍሷን ባገኘ ጊዜ ነፍስ ያለውን ሥጋ በመንፈስ ቅዱስ ፈጠረላት" ብሎ ንጽሕናዋና ቅድስናዋ

[60] አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፥ ገ.721
[61] ቅዳሴ ማርያም ቁ.38

ከጌታ ሰው መሆን በፊትም የነበረ እንጂ ከጌታ ሰው መሆን ወዲህ ሆኖ እርሱም ደግሞ ለራሱ አንጽቶ እንደ ጎዳሪና ማኅደር በማኅፀኗ ዘጠኝ ወር ከአምስት ቀን ከርሞ ወጣ አይልም። "የፈጠረውን ሥጋ ተዋሐደ" ማለት ከነፍሷ ነፍስ፣ ከሥጋዋ ሥጋ የነሳውን ባሕርየ ሰብእ ከመለኮቱ በገዛ ሥልጣኑ አዋሐደው ማለት ነው። ለዚህ ነው ቅዱስ ያሬድ በጥር ማርያም ድጓ "መለኮቱ ወልድ ውስተ ሥጋሃ ደመረ" የሚለው። ሥጋና ነፍሱ ከሰማይ የወረደ አይደለም፤ ከእርሷ የነሳው ነው (ዕብ.2:15-16፣ ገላ.4:4)። "ፈጠረ" ቃሉ ለትስብእት ሲነገር፦ እግዚአብሔር ወልድ በተለየ አካሉ በማኅፀነ ማርያም እንበለ ዘርዐ ብእሲ (ያለ ወንድ ዘር) ከእሷ ሥጋና ነፍስ ነሣ፤ በተዋሕዶ ተፀነሰ' ቢባል የቀና ትርጓሜ የሚሆን ይመስለኛል።

(4.4.2.4) ይህን ታላቅ የተዋሕዶ ምሥጢር የተከናወነበትና ጌታን ያሕል ጽንስ ከእትብት በሆነ መግቦት የተሸከመ ማኅፀን ዛሬ ከመቅደሳችን የከበለሉ ወንድሞቻችን '(ጌታ በተዋሕዶ ሰው ከሆነበት በኋላም) የውርስ ኃጢአት አለበት' ይላሉ። 'ቅዱሱ ጌታ ባልተቀደሰ ማኅፀን ተፀነሰ' ብለው ደፍረው ይጽፋሉ። አንዳንዶቹ'ማ ቢችሉ ኖሮ ዕትብቱን ቆርጠው እናትና ልጁን መነጠልን የሚመኙ ሆነው ይታያሉ። ልብ እስኪገዙ በጸሎት እያሰብን ባሉበት እንተዋቸው። ኤራቅሊስ ይናገር። ታላቁ አባት "ለሰው ሁሉ ከመገዛት የንጻነት መጽሐፍ የተጻፈባት ማኅፀን ወዮ እንደ ምን ያለች ናት?!" ይላታል።[62] አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫም "የዚህ ዓለም እድፍ ባላገኘው ማኅፀኗ አደረ። ንጹሕ ቃል የሆነ የእግዚአብሔር ቃል በንጽሕት ሥጋ አደረ" ይላል።[63] የአብ ቀዳማዊ ቃል የአዳም አበሳ ባልተጻፈባት ድንግል መጽሐፍ መቀረጹን እናምናለን። እንደ መስኖ ውኃ ሽው ብሎ አለፈ አንልም፤ ሥጋና ነፍሱን ከሥጋና ነፍሷ ነሳ። ቅዱስ ኪራኮስ እንዳለው "... እንደ መስኖ ውኃ በድንግል ማኅፀን ገብቶ የወጣ አይደለም፤ ነፍስን ሥጋን ነስቶ በእውነት ሰው ሆነ እንጂ፤ ሕያው ቃል እርሱ የማይመረመር አካል ያለው አንድ ባሕርይ በመሆን የምትናገር የምታውቅ ነፍስ ያለችው ሥጋን በድንግል ማኅፀን ነስቶ ሰው ሆነ።"[64] ቅድስት ኤልሳቤጥ እናትና ልጁን አስተባብራ እናቱን "የተባረክሽ፣ የማኅፀኗን ፍሬ 'ቡሩክ' እንዳለችው ሁሉ የምንከራብት

[62] ሃይ.አበ ዘኤራቅሊስ ምዕ.48:15፡ ገ.156
[63] መጽሐፈ ምስጢር፡ገ.173
[64] ሃይ.አበ ዘኪራኮስ ምዕ.91:18፡ ገ.401



ኢትዮጵያዊ የሥነ መለኮት ሊቅ እናትና ልጁን አስተባብሮ (የፈጣሪና ፍጡር ግንኙነታቸውን ሳይስት) ያወድሳቸዋል። ንዑስ ርእሳችንን በእርሱ ቃል እናሳርግ፦ "ንጽሕት ድንግል ሆይ! ይህች ዕለት (በሉቃ.2:24 የተነገረችው የመንጻት ቀን /ልደተ ስምዖን/) እንዴት የንጽሕናሽ ዕለት ሆነች? የንጽሕናን ቀን ትፈልጊ ዘንድ መች ረከስሽ? ያለሩካቤ ፀንሰሽዋልና ያለእድፍም ወልደሽዋልና የቅድስና ፍሬን ለምን በንጽሕና ቀን ወደ ቤተ መቅደስ ወሰድሽው? ከቤተ መቅደስ ይልቅ አንች ትከብሪያለሽና። ዘጸ.31:18፣ ዘሌ.11:20፣ ሉቃ.2:24፤" ይላታል አባ ጊዮርጊስ።[65] የአባ ጊዮርጊስ መነሻ፦ "ወገብረ፡ በሕገ ኦሪት፤ ከመ ይሳየጦሙ፡ ለእለ ውስተ ኦሪት - ከሕግም በታች የተወለደውን ልጁን ላከ፤ እንደ ልጆች እንሆን ዘንድ፥ ከሕግ በታች ያሉትን ይዋጅ ዘንድ" ሲል ሐዋርያው በገላ.4:4-5 ያስፈረው ክታብ ነው።

### 4.4.3 "መድኃኒቴ!"

(4.4.3.1) በሉቃ.1:47 እመቤታችን "መንፈሴም በአምላኬ በመድኃኒቴ ኃሴት ታደርጋለች - ወትትሐሠይ መንፈስየ በአምላኪየ ወመድኃኒየ" ስትል ጸሎት አድርጋለች። ይህ ቃል በግብጻውያንና በምሥራቃውያን እመቤታችን "ጥንተ አብሶ ስለ ነበረባት ከዚህ የሚያድናት መድኃኒት ሽታ ያደረገችው ጸሎት" ተደርጎ ይቀርባል። በእኛ ሊቃውንት ግን ቃሉ በኃላፊ ነው የሚተረጎመው። ባለፈው ለተደረገላት እንጂ ወደ ፊት ለሚሆነው የማዳን ሥራ አይደለም 'መድኃኒቴ' ያለችው። ሊቃውንቱ "ተዐብዮ ነፍስየ ለእግዚአብሔር - ነፍሴ እግዚአብሔርን ታከብረዋለች" ማለቷ "እግዚአብሔር አብን ነው"፤ "በአምላኪየ" ያለችው "እግዚአብሔር ወልድን ነው"፤ "መድኃኒቴ" ያለችው "መንፈስ ቅዱስን ነው" በማለት ቃሉን ለአብ፣ ለወልድ፣ ለመንፈስ ቅዱስ ሰጥተው ይተረጉሙታል። በመቀጠልም "መንፈስ ቅዱስን ስለ ምን ለብቻው ለይታ መድኃኔ አለችው? ቢሉ ጌታ ተፀንሶ ሳይወለድባት አስራ አምስት ዓመት ሙሉ ከፀብአ አጋንንት (ከአጋንንት ፈተና) 'ጠብቋት' ይኖር ነበርና። ስለዚህ መንፍስ ቅዱስን ለብቻው ለይታ 'መድኃኔ' አለችው ... 'መንፈስ ቅዱስ፡ ዐቀባ፡ እምከርሠ እማ' እንዲል። አሁን ከአብ ከወልድ ለብቻው ለይቶ

[65] መጽሐፈ ምሥጢር፡ ገ.85

አድኗት አይደለም፤ በማዳን አንድ ናቸውና እንድነታቸውን ስትናገር ነው እንጂ [መድኃኒቶቼ ከማለት ይልቅ መድኃኒቴ ያለችው]።"[66]

(4.4.3.2) የእንግሊዝኛውን ጥቅስ ካየን "And my Spirit hath 'rejoiced' in God My Savior" ሲል በትንቢት (future tense) ሳይሆን በኃላፊ (past tense) ነው የገለጸው - rejoiced! ንባቡ አስቀድሞ መጠበቋን (preserve መደረጓን) እና በዚህም ሐሴት ማድረጓን ነው የሚያሳየው። "ድኂን" ሲተረጉም "መዳን፤ ማምለጥ፤ መውጣት፤ ከተያዙ በኋላ ወይም ሳይያዙ መቅረት፤ መትረፍ፤ እንዳይያዙ መሆን፤ መጠንቀቅ፤ መጠበቅ..." ተብሎ ነው።[67] ጥቅሱ የሚያሳየው የእመቤታችን ሐሴት ማድረግ የመነጨው ስለሚመጣው ብቻ በማሰብ ሳይሆን ባለፈው ሕይወቷና በጊዜው ሁሉ ከተደረገላት የመንፈስ ቅዱስ ጥበቃ የተነሣ ነው። ይህም ገና ጥንተ አብሶ ስላልጠፋላት ለወደ ፊቱ እንዲጠፋላት ሽታ በመቃተት "ወመድኃኒየ እንዳለች ተደርጎ የሚቀርበውን ብሒል የሚቃረንና የዐቀባን ብሒል የሚያፀና ነው። እመቤታችን ቃሉን የወሰደችው "ወአንሰ እትፌሣሕ በእግዚአብሔር፤ ወእትሐሠይ በአምላኪየ ወመድኃኒየ - እኔ ግን በእግዚአብሔር እምኜ ደስ ይለኛል፤ በፈጣሪዬ በመድኃኒቴ ደስ ይለኛል" ከሚለው የዕንባቆም ጸሎት ነው።[68] መድኃኒት የሚባለው የያዘንን ሕመም የሚፈውስ ብቻ አይደለም፤ አስቀድሞ ሕማም እንዳይዘን የሚሰጥ መድኃኒት (ክትባትም) መድኃኒት ይባላል። የእመቤታችን "መድኃኒቴ" ማለት ይኸው ነው። ባለፈ ዕድሜዋ ለተደረገላት ጥበቃ ነው መድኃኒቴ ያለችው። መዳኗ:- ሎጥ ከመዓተ ሰዶም ወገሞራ፤ ዳንኤል ከአፈ አናብስት፤ ሠለስቱ ደቂቅ ከእቶነ እሳት ተጠብቀው እንደዳኑት ያለ ነው - እነርሱ ሳይነካኩ ተጠበቁ፤ እርሷም እንዲሁ - ፍቁራን የኤርትራ ኦርቶዶክሳውያን እንደ ተረኩት።

## 4.4.4 "በከርሠ አዳም ድንግል ተሐቱ - ድንግል በአዳም ወገብ ታብራ ነበር!"

[66] መጋቤ ሐዲስ ታመነ አበበ፤ የጸሎተ ማርያም ትርጓሜ፥ ገ.95
[67] አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፥ ገ.343
[68] ዳንኤልና 12ቱ ደቂቀ ነቢያት፥ ገ.333



(4.4.4.1) ከላይ ያለውን ቃል ቅዱስ ያሬድ ነው ደጋግሞ የዘመረው - በተለይ በንሐሴ ኪዳነ ምሕረት ድጓ። በእኛ አገር ያሉ የእንጽሐ ብሒል ደጋፊዎች ግን ቃሉን የመቃወም አዝማሚያ አላቸው። መጽሐፋዊና ትውፊታዊ መነሻ እንደሌለው አድርገው ያጣጥሉታል። አንዳንዶም ስድበው ለሰዳቢ ይሰጡናል።[69] ጽንሰ አሳቡን ትርጓሜ ሊቃውንትን መነሻ አድርገን እንየው።

የማክሰኞ ውዳሴ ማርያም እንድምታ "ተፈሥሒ አ! መድኃኒታ ለሔዋን" የሚለውን ንባብ ሲተረጉም "የሔዋን ደኅንነቷ ደስ ይበልሽ። ...በሔዋን ሁሉን መናገር ነው። ከሁሉ አንዱ ሰሎሞን በዓለ አእምሮ ንጉሥ ነበር። ኋላ መፍቀሬ አንስት ሆነ። ብዙ ኃጢአት ሠራ። በፍጻሜ ዘመኑ ንስሐ ቢገባ 'አይዞህ መርገም ያልወደቀባት ንጽሕት ዘር ከአዳም ባሕርይ ተከፍላ በሴት አካል ተቀርጻለች ከዚያ ሲወርድ ሲዋረድ በሴት፤... በኖኅ፤... በሴም፤... በአብርሃም፤ ... በይስሐቅ፤... በያዕቆብ፤... በይሁዳ፤... በዕሴይ፤... በዳዊት፤... በአንተ (ሰሎሞን)፤... በሮብዓም፤... ከዚያ እያይዞ እስከ ምጽአት ድረስ ያለውን ነግሮታል። ... አሁን እንዲህ ማለቱ ደም እንዲህ ሲቀዳ ይኖራል ማለት አይደለም። ጥንቱን ሰው ሲፈጠር በንጽሐ ጠባይዕ መፈጠሩን መናገር ነው" ይላል።[70] የትርጓሜው መልእክት እመቤታችን በአዳም ሰውነት ውስጥ የተለየ ባሕርይ /ዘረ-መል/ (ጂን) ሆና ታንፀባርቅ ነበር፤ ወይም ለእርሷ ጽንስ ምክንያት የሆነው አዳማዊ ተባዕታይ ዘር በልዩ ሁኔታ ተለይቶ ከትውልድ ወደ ትውልድ ይተላለፍ ነበር ለማለት አይመስልም። መልእክቱ እንድም:- በመጨረሻው የትርጓሜ ዐረፍተ ነገር እንደ ተመለከተው የእመቤታችን ተፈጥሮ (ጽንሰት) ጥንቱን አዳም ሲፈጠር (ገነት ሲገባ የተሰጠው ጸጋ ከመገፈፉ በፊት[71] ) የነበረውን ንጽሐ ባሕርይና ቅድስና

[69] ካቶሊካውያን ይህን ሐሜት ይዘው ይመስላል:- እኛን "የትስብእት ባሕርይ በመለኮት ተዋጠ፤ ተመጠጠ" የምንል የአውጣኪ ተከታዮች አድርገው አጣጥለው ሲያበቁ "የአቢሲኒያ መናፍቃን እመቤታችን 'ገና አዳም ከገነት ሳይወጣ ተፈጥራ ነበር' እያሉ ያስተምራሉ" ሲሉ በተሳሳተ አነጋገር ይገልጹናል። (Miracles of The Blessed Virgin Mary, 1928, Edited by G.G.Coulten and Eilen Power, Published by Harcourt, Brace and Company, introduction, p.40. ወይም http://www.strobertbellarmine.net/books/Heroit--MiraclesofBlessedVirginMary.pdf)
[70] ውዳሴ ማርያም ንባቡና ትርጓሜው፥ ገ.37
[71] ትብዐቶች የዐቀባን ብሂል በመርህ ደረጃ ይቀበላሉ። ነገር ግን የእመቤታችን ቅድመ ብስራት መልአክ ሕይወት አዳም ተፈጥሮ ገና ገነት ሳይገባ የቀየበትን እርባ ቀን አይነት ነው ይላሉ። አዳም ገነት ሲገባ ልጅነት አግኝቷል። ከገነት ሲወጣ ተረግሟል። እሷ በነዚህ የጊለኞቹ

ገንዘብ ያደረገ ነው ለማለት ነው። እንዲያም ሲል እመቤታችን ከአዳም ጀምሮ ባሉ አበው ጌታ ከእርሷ ተወልዶ ያድነናል በሚል ብሩህ ተስፋ ስትነገር መኖሯን ነው የሚያመለክተው፤ "እግዝእትነ ማርያም ተነግረት እምአዳም እስከ አብርሃም ወእምአብርሃም እስከ ሙሴ ወእሙሴ እስከ ዳዊት፡ ወልደ እሴይ በብዙኅ አምሳል አስተርአየት" እንዲል መቅድመ ተአምረ ማርያም ዘዘወትር።[72]

(4.4.4.2) ከላይ የሰፈረው አሳብ ትውፊት ብቻ አይደለም። ጽንሰ አሳቡ በመጽሐፍ ቅዱስም አለ - የአያትን ምግባር ለልጅ ልጅ ሰጥቶ መናገሩ። በዕብ.7፡9 "ዓሥራትን የሚያስወጣ ሌዊ እንኳ በአብርሃም እጅ ዓሥራትን ሠጥቶአል፤ መልከ ጼዴቅ በተገናኘው ጊዜ ገና በአባቱ ወገብ ነበርና [በአባቱ በአብርሃም ባሕርይ ነበርና]" ተብሎ ሰፍሯል። በተመሳሳይ በዘፍ.9፡27 "ወያርኅብ እግዚአብሔር ብሔሮ ለያፌት፤ ወይኅደር ውስተ ቤቱ ለሴም ... እግዚአብሔር ያፌትን ያስፋ፤ በሴምም ድንኳን ይደር" በሚል የሰፈረው ደረቅ ንባብ በትርጓሜው ሲብራራ "እግዚአብሔር በሴም ወገኖች ላይ ይደር፤ አንድም ጌታ ከነገደ ሴም ከተገኘች ከእመቤታችን ከንፍስዋ ነፍስ፣ ከሥጋዋ ሥጋ ነስቶ በማኅፀና አድሮ ሰው ይሁን!" ተብሏል።[73] ይህን ስናይ የውዳሴ ማርያም መተርጉማን እና ቅዱስ ያሬድ ያለምንም መነሻ "በከርሠ አዳም ድንግል ተሐቱ" እንዳላሉ መረዳት ይገባል። እነ ኤርምያስንና ዮሐንስ መጥምቅን አብነት አድርጎ "ቦ እለ ተሐርዩ እምከርሠ እሞሙ፤ ወቦ እለ ተጸሕፈ አስማቲሆሙ በሰማያት - ከእናታቸው ማኅፀን ጀምሮ የተመረጡ አሉ፤ አስቀድሞ ስማቸው በሰማይ የተጻፈም አሉ፤" ይላል ቅዱስ ያሬድ። ሐዋርያውም በሮሜ.8፡29 አስቀድሞ ያወቃቸውን የልጁን መልክ እንዲመስሉ እንደ ወሰነ፣ የወሰናቸውን እንደ ጠራ፣ የጠራቸውን እንዳጸደቀ፣ ያፀደቃቸውን እንዳከበረ ጽፏል። አክሎም በኤፌ.1፡4 "ዓለም ሳይፈጠር በፊቱ ቅዱሳንና ነውር የሌለን በፍቅር እንሆን ዘንድ በክርስቶስ መረጠን፤" ይላል። ይህም

አንቀምሮቹ አትመስለውም። አዳም ተፈጥሮ፣ ገነት ሳይገባ አርባ ቀን ሲቆይ ጸጋ ሳያገኝ፣ ርግማንም ሳይደርስበት እንደ ኖረው ሁሉ እሷም መልአኩ እስኪያበስራት እንደ'ሱ ሆና ቆይታ ከበሰራት በኋላ ልጅነትን አግኝታ፣ ከዚያ በኋላ አዳም በገነት የነበረውን አይነት ሕይወት ትራለች ይላሉ። (ወልደ አብ፤ አሳታሚ የምስበ ቅዱሳን ቀጋ ኪዳን ምሕረት አፀደ ኢዮስጥቲዎስ ገዳም፤ 2008 ዓ.ም.፡ገ.137-138።)

[72] ተአምረ ማርያም፡ገ.28

[73] መጻሕፍተ ብሉያት ክልኤቱ፡ ገ.75



የእግዚአብሔርን አስቀድሞ ዐዋቂነት የሚያሳይ ነው፤ አስቀድሞ ማወቅ፣ አስቀድሞ ለጽድቅና ኩነኔ መድቦናል ማለት - predestination - አለመሆኑ ይሠመርበትና። ታዲያ ቅዱሳኑ ሁሉ ቅዱሳን እንደሚሆኑ ጌታ አስቀድሞ ያውቃል ካልን የእመቤታችን ዓለም ሳይፈጠር በአምላክ ሕሊና ታስቦ መኖር በአባቶቻችን ሲነገር ለምንድን ነው ብርቅና ድንቅ መሆኑ?!

## 4.4.5 በጥንተ አብሶ ዙሪያ የኢትዮጵያ ቅዱስ ሲኖዶስ አቋም ምን ይሆን?

(4.4.5.1) አንጋፋው የቅዱስ ሲኖዶስ አባል እና በዓለማዊውም በመንፈሳዊውም ዕውቀት ገፍተው ከተማሩ ከቡራን አበው አንዱ የሆኑት ብፁዕ አቡነ ገብርኤል 'እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት/ የለባትም?' የሚል ብሒል በቅዱስ ሲኖዶስ ደረጃ ባለመወሰኑ ሊቃውንቱ እስካሁን ድረስ (እሳቸው ይህን ያሉ በግንቦት 1997 ዓ.ም. አሜሪካ ሳሉ ነው) በሁለት ጎራ ተከፍለው "ቅድመ ብሥራተ መልአክ ጥንተ አብሶ አለባት/ የለባትም!" እያሉ ስለሚከራከሩ ከግብጻውያን ጋር በተዛመደ መልኩ ("ነበረባት፤ በብሥራት ጊዜ ነጻች" ብሒል) ዶግማዊ ውሳኔ ሰጥቶ ለእኅት አብያተ ክርስቲያናት ማሳወቅ እንደሚገባ ገልጸዋል።[74] ደጋግሜ እንዳልኩት ለአቡነ ገብርኤል ልባዊ አክብሮት አለኝ። ነገር ግን ይህ ብልጭ ብሎ የጠፋ ጽሑፋቸው፡-

(1) ከነባሩ የዐቀባ ትውፊት አይጣጣምም።

(2) ራሳቸው የተሳተፉበት የ1988 ዓ.ም. የጳጳሳትና የሊቃውንት ጉባኤ በአማርኛ እና እንግሊዝኛ አሳትሞ ካሰራጨው መጽሐፍ ይዘት ጋር ይጣረሳል።

(3) ማዕከላዊ ተቋማችን ከእንጽሐ ይልቅ ለዐቀባ ይወግናል፤ ከ1970ዎቹ ጀምሮ ያሉ የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ልሳናት የሆኑት ትንሣኤና ማዕዶት መጽሔቶችም የዐቀባን ብሒል አስተጋብተዋል።

(4) ግብጽን ጨምሮ ሌሎች እኅት አብያተ ክርስቲያናት የእንጽሐ ("ነበረባት፤ በብሥራት ጊዜ ነጻች") ብሒላቸውን በዶግማ መልክ አውጥተው

[74] አባ ሠረቀ፡ ገ.67

አላደረሱንም። ብሒላቸውን የምናውቀው በመንፈሳዊ የሥነ ጽሑፍ ውጤቶቻቸው (Literature) ብቻ ነው።
(5) እንዲያውም እነዚህ አብያተ ክርስቲያናት የካቶሊክን ቤተ ክርስቲያን ከሚወቅሱባቸው ጉዳዮች አንዱ ሁሉንም ትውፊት ሲኖዶሳዊ ዶግማ የማድረግ አካሔድ አላቸው ብለው ነው። ለምሳሌ፦ ፍልሰታ በሁላችንም ትከበራለች። ሌሎቻችን በትውፊት ነው የምናከብራት። ካቶሊኮች ግን ፍልሰታን በሲኖዶሳዊ ዶግማ ደንግገዋታል። ስለሆነም የጥንተ አብሶን ጉዳይ በሲኖዶስ አለመደንገጋችን ከእኅት አብያተ ክርስቲያናት ምንም ዓይነት ነቀፋ ሊያመጣብን አይችልም። እነርሱን ለመምሰል ሲባል በምን ይሉኝ ደንግጎ ካልመሰልናቸው ማለት "ሳያባርሩን እንደ መሸሽ ነው" ብዬ አምናለሁ።

(4.4.5.2) አቡነ መልከ ጼዴቅ በ1984 ዓ.ም. የተከሰሱበትን፣ ሊቀ መጋቤ ብሉይ ሠይፈ በ1982 ዓ.ም. "አሰባት" ብሎ በመጻፉ በጥርጣሬ ሲታይ የኖረበትንና መጽሐፉም በሊቃውንት ጉባኤ የታገደበትን፣ የእነ ሊቀ ብርሃናት አስተርአየ ሥልጣነ ክህነት በእንጽሐ ብሒል ምክንያት በአቡነ ማትያስ ሲያዝ ሲኖዶሱ አገዳውን ከማንሣት ይልቅ በዝምታ በማለፍ ወደ ድጋፍ ያጋደለ አቋም ያንጸባረቀበትን፣ በ2004 ዓ.ም. እንዲሁ ቆሞስ አባ ሠረቀ ብርሃን ወልደ ሳሙኤል በዚሁ (በጥንተ አብሶ አሰባት ከማለት) የተነሣ ተከሰው ክሱ አቡነ ጳውሎስንም ለመነቅነቅ ተዳርሶ ከጫፍ የተመለሰበትን ሒደት እያየን የጥንተ አብሶ ጉዳይ በእርምጥም ቢሆን አቋም አልተወሰደበትም ማለት ያዳግታል። "እመቤታችን ጥንተ አብሶ ነበረባት" ያሉ ሰዎች ይህን በማለታቸው ተከሰው ሲኖዶሱ ከአንድም ሁለት ጊዜ ብሒላቸው እንዲጣራ መመሪያ ካስተላለፈ ጉዳዩ የክስ ምክንያት (cause of action) መሆን ችሏል። አስከስሷል። ካስከሰሰ የተጣሰ ድንጋጌ አለ ማለት ነው። ለማስከሰስ ድንጋጌው የግድ በሲኖዶስ መጽደቅ አይጠበቅበትም። ነገር እና በቤተ ክርስቲያን በቃልና በመጣፍ ሲነገር የኖረ ትውፊት ካለ ያ በቂ ነው። በሲኖዶስ ያልጸደቀ ብሒል እያስከሰሰም ካልሆነ ፍልሰታም እኮ እንደ ካቶሊኮች በሲኖዶሳችን ዶግማ ሆና አልተደነገገችም። ዶግማ ወጥቶ አይደለም ነሐሴ 16 ፍልሰተ ሥጋዋን የምንዘክረው። ትውፊት ነው - ቅዱስ ትውፊት። የትውፊት ገዥነት በዓለማዊ ሕግም የታወቀ ነው። በአገራችን የፍትሐ ብሔር ሕግ ልማድ (custom)፣ አሠራር (usage)፣ ወግ (moral)፣ ሥርዓት



(practice)፣ መርሕ (principle) የመሳሰሉ ቃላት በሕጉ ውስጥ እንደየአገባቡ አገልግሎት ለሚሰጡ ትውፊቶች መገለጫ ሆነው ተቀምጠዋል። አገልግሎታቸው የተጻፈው ሕግ በተግባር ካለው ትውፊት ተዋሕዶ የሠመረ የኑሮ ሥርዓት እንዲዘረጋ፣ ተዘርግቶም እንዲፀና ማስቻል ነው። በዓለም አቀፍ ደረጃም ቢሆን ዓለም አቀፋዊ የልማድ ሕግ (Customary International Law) የተባለ ያልተጻፈ ግን ሁሉም በገቢር የተቀበለው የሕግ ሥርዓት አለ። ስለዚህ እመቤታችን ጥንተ አብሶ የለባትም የሚለው በቀደምት አበው የተያዘ ብሒል በሲኖዶስ በዶግማነት ካልተደነገገ በቀር ተቀባይነት የለውም ወደሚል አስተሳሰብ እንዳንሔድ መጠንቀቅ ያሻል።

(4.4.5.3) በእኛ ዕድሜ በጽሑፍ ካልሆነ በቀር በየትኛውም ኢትዮጵያ ውስጥ ባለ ዐውደ ምሕረት ደፍሮ "እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት" ብሎ የሚያስተምር ኦርቶዶክሳዊ አላየንም፤ አልሰማንም። እንዲያውም ቀደም ሲል "ነበረባት፤ ነጽታለች" ሲሉ የነበሩ እንደ ዓሥራት ገ/ማርያም፣ መጋቤ ብሉይ ሠይፈ፣ አባ ሠረቀ እንዲሁም አቡነ ጳውሎስ የመሳሰሉ አበው ሳይቀሩ በጊዜ ሒደት አቋማቸውን እያለዘቡ ሒደዋል፤ ጽሑፎቻቸውንም ያረመበት አጋጣሚ አለ። ዓሥራት ገ/ማርያም በ1983 ዓ.ም. በ"ትምህርተ መለኮት" መጽሐፋቸው የጻፉትን የእንጽሐ ብሒል በ1991 ዓ.ም. ዳግም ኅትመት አውጥተውታል። አባ ሠረቀ ጥር 11 ቀን 2008 ዓ.ም. በቤተ ክህነት አማካይነት በወጣው በዓሉን የተመለከተ ጽሑፍ ቀደም ሲል እርሳቸውን የተቹ ሰዎች ያቀረቧቸውን ጥቅሶች ተጠቅመው ጥንተ አብሶ የለባትም ለሚለው ብሒል አድልተው ጽፈዋል።[75] መጋቤ ብሉይ ሠይፈ የ1982 ዓ.ም. አቋማቸውን በ1988 ዓ.ም. የጳጳሳትና ሊቃውንት ጉባኤ ለውጠዋል። ይህም የእንጽሐ ብሒል በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት፣ ሊቃውንት፣ ካህናት፣ ወጣቶችና ምእመናን ተቀባይነት ስለሌለው የብሒሉ አረማጆች ወደ ነባሩ የዐቀባ ብሒል ተስበው እንደሚገቡ ነው የሚያሳየው። በዚህ ከነባር ብሒል የመውጣትና የመመለስ ሒደት ውስጥ፣ እንዲሁም በብሒል መለያየት የተነሣ በሚሰነዘሩ ክርክሮች የሚሰነዘሩ ኃይለ ቃሎች ግን መጠን ያለፉ ሆነው ይሰሙኛል። እሱ ላይ ቅሬታዬን ገልጬ ልደምድም።

[75] http://eotcssd.org/dogma-ethiopian-orthodox-tewahedo-church/60-miscellaneous/478-2016-02-04-06-45-02.html

## በዐቀባ ብሒል ሥር ያሉ አመለካከቶችን የሚያነጻጽር ሠንጠረዥ

| | ካቶ ሊክ | ኢትዮጵያዊ የዐቀባ ትውፊት ዝንባሌ | ኤርትራዊ የዐቀባ ትውፊት ዝንባሌ | ሊቀ ጉባኤ አበራ በቀለ[76] |
|---|---|---|---|---|
| ኃጢአቱና መርገሙ በዘር፣ በሩካቤ ይተላለፋል | √ | X | X | √ |
| ቅድመ ተራንዮ (በዓመተ ፍዳ/ ኲነኔ) ሰው በመርገም ሥር ሆኖ ይወለድ ነበር | X | √ | √ | X |
| ነፍስ ከወላጅ ትከፈላለች | X | √ | √ | √ |
| ለእያንዳንዱ ሥጋ አዲስ ነፍስ ይፈጠራል | √ | X | X | X |
| ጥምቀተ ክርስትና ለድምሳሴ ጥንተ አብሶ | √ | X | X | √ |
| ከስቅለተ ክርስቶስ በኋላም ጥንተ አብሶ አለ | √ | X | X | √ |
| ኃጢአት በዘር ስለሚተላለፍ እመቤታችን ከተላላፊው ኃጢአትና መርገም ተጠብቃለች | √ | X | X | √ |
| ኃጢአት ጥንቱንም ስለማይወረስ እመቤታችን ከመርገም ብቻ ተጠብቃለች | X | √ | √ | X |
| ጥምቀተ ክርስትና ለዳግም ልደት | √ | √ | √ | √ |
| እመቤታችን በሕገ በሩካቤ ተወልዳለች፤ አርያማዊት ያይደለች ምድራዊት ናት | √ | √ | √ | √ |

√ = ይቀበላሉ፡፡ X = አይቀበሉም

[76] ማስታወሻ፦ የሊቀ ጉባኤ አባ አበራን አቋም በኦርቶዶክሳዊ ጥላ ስር ያለ አመለካከት አድርጌ ነው የማየው፤ ለጊዜው ስሕተት ነው እያልኩ አይደለም፤ ለማለትም አልችልም፤ ለንጽጽር ብቻ ነው ሰንጠረዡን የተጠቀምኩት!!

# ምዕራፍ አምስት

## በአንጽሖ እና በዐቀባ የእርስ በርስ ክርክር መካከል የሚሰነዘሩ ያልተስማሙኝ አባባሎች

### 5.1. በዐቀባ ብሒል ደጋፊዎች የሚሰነዘሩ የማልቀበላቸው አባባሎች

(5.1.1) ካቶሊካውያን "እመቤታችን 'የሰው ልጅ ሳትሆን አርአያማዊት ናት' ይላሉ" ስንባል አድገናል፡፡ የተሳሳተ አባባል ነው፡፡ የዐቀባን ብሒል ደጋፊ ወገኖች ይኼን አባባል የሚናገሩት ከአንጽሖ ወገን የሚሰነዘርባቸውን "ካቶሊክ" የሚል ታርጋ ለመሸሽ ነው፡፡ ሆኖም ሽሽቱ አላስፈላጊ ንግግር ለመናገር ምክንያት መሆን የለበትም፡፡

(5.1.2) እመቤታችን ጥንተ አብሶ አለባት የሚሉ የአገራችን ሊቃውንት ከምልአተ ኃጢአት (ጎልዮ፣ ነቢብ፣ ገቢር) ንጽሕት እንደ ሆነች፣ ቅድስናዋን፣ ምስጋናዋን፣ ወላዲተ አምላክነቷን፣ ከልማደ አንስት ንጽሕት መሆኗን፣ አማላጅነቷን፣ ፍልሰቷን፣ ዕርገቷን፣... ያምናሉ፤ ያስተምራሉ፡፡ ይኼ ሁሉ እየታወቀ እነዚህ ሰዎች ላይ ብዙ ጊዜ በዐቀባ ቡድኖች ተሽቀዳድሞ "ፕሮቴስታንት፣ መናፍቅ፣ ተሐድሶ፣ አርዮስ፣ ንስጥሮስ..." በማለት ገፍቶ የመጣል ዘመቻ ይካሔዳል፡፡[1] ነገሩን ከባድ የሚያደርገው ይህን ዘመቻ የራሳችን ሊቃውንት ላይ የሚያደርጉ ወገኖች ብሒሉን በአደባባይ ለሚሰብኩት አቡነ ሺኖዳ ሲሆን ጎንበስ ቀና በማለት ጉራማይሌ አቋም ያንጸባርቃሉ፡፡ ከዚያም አልፈው ያከፋልናል የሚሉትን ስም ሁሉ ለመጠቀም ሲሉ "ጥንተ አብሶ አለባት" የሚሉትን የኛዎቹን ሰዎች "ጥንተ አብሶ የለባትም" የሚሉትን የካቶሊኮች ስያሜ በግድ ያሸክሟቸዋል፡፡ አቡነ ጳውሎስና አባ ሠረቀ ብርሃን በየማኅበራዊ ሚዲያው "ካቶሊካውያን" እየተባሉ

[1] አለቃ አያሌው ታምሩ በእመቤታችን ጉዳይ እጅግ ስስ ናቸውና የአንጽሖን ብሂል ደጋፊው የጻፉትን እነ መ/ብ ሠይፈ ሥላሴንና ቀሲስ አስተርአየን "ፕሮቴስታንት ረድፈኞች" ሲሉ ይተቹዋቸዋል፡፡ (ስምረት እያሌው፣ አባቱና እምነቱ፡ገ.120፡፡) ሆኖም ለዐቀባ መቀርቀሬ እንዳለ ትችቱ የተጋነነ ፍረጃ ያለበት ይመስለኛል፡፡

ሲወረፉ ታዝበናል፡፡ መቼም "እመቤታችን ጥንተ አብሶ የለባትም" በማለት የሚታወቁት ካቶሊካውያን፣ "አለባት" ብለው በመጻፋቸው ያለአግባቡ "ካርዲናል ጳውሎስ፣ ካርዲናል ሠረቀ..." ሲባሉ የኖሩ ፓትርያርክና መነኮስ መኖራቸውን ቢሰሙ ይሳለቁብናል፡፡ አካሔዱ 'የአቡነ ጳውሎስና የአባ ሠረቀ የቀደመ ጽሑፍ የነ አቡነ ሺኖዳ ብሒል ነው ከተባለ ሰው አቡነ ሺኖዳን ስለሚወድ ሰዎቹን ለማጥላላት አይመቸንም!' ከማለት የመነጨ መሆኑ ነው፡፡ ስሕተት! ምናልባትም የቅንነት ጉድለት! በጥናታቸው ገጽ 348 "እናቱን ችል ማለት ልጁን በተሳሳተ መንገድ መረዳትን ያስከትላል - To ignore the Mother means to mis-interprete the Son" የሚሉትን አቡነ ጳውሎስ ከቀደመ የአንጽሖ ብሂላቸው በመነሳት "ፀረ ማርያም ፕሮቴስታንት" አድርጎ ለማቅረብ የሚደረገው መፋጠን እስደስቶኝም አያውቅ! በዛ!

(5.1.3) በዓለም አቀፍ ደረጃ ያሉ ብዙኃን ፕሮቴስታንቶች ጥንተ አብሶ ከቃሉ ጀምሮ በመጽሐፍ ቅዱስ ስለሌለ አንቀበለውም ባዮች ናቸው፡፡ የካቶሊኮች ፈጠራ "ተረት ተረት" ሲሉ ጽንሰ አሳቡን የዚህ የዚያ ሳይሉ በጅምላ ያጣጥሉታል፡፡ ተሐድሶዎች እንደ አንጽሖ ቡድን "ስትፀነስ ነበረባት፤ በብሥራት ጊዜ ነጻች" ሳይሆን የሚሉት "ስትጸነስ ነበረባት፤ ስትጸንስም ነበረባት፤ ከጸነሰችውም በኋላ እርሱ ብቻ ያለጥንተ አብሶ ተፀንሶ ተወለደ፤ እርሷ ግን የውርስ ኃጢአተኛ መሆኗ ቀጠለ!" ነው የሚሉት፡፡[2] በተጨማሪም አማልጂነቷን፣ የጸጋ ሰጊድና ምስጋና የሚገባት መሆኑን፣ ወላዲተ አምላክነቷን፣ ዘለዓለማዊ ድንግልናዋን፣ ከምልዓተ ኃጢአትና ከልማደ አንስት ንጽሕት መሆኗን፣ በስሟ ቤተ ክርስቲያን መታነጹን፣ በሥዕሏ ፊት ጸሎት ማድረግን በአጠቃላይ ክብረ ድንግልን አይቀበሉም፤ ይክዳሉ፡፡ ይህ ሁሉ እየታወቀ "መንጸቷ ከብሥራት መልአክ ወዲህ ነው!" ከማለት በቀር ከዚህ ፕሮቴስታንት ወለድ ተሐድሶ ውጉዝ አስተምህሮ ጋር አንዳች ቁርኝት የሌላቸውን የአንጽሖን ብሒል ደግፈው የጻፉ ኢትዮጵያውያን ሊቃውንት ጠቅልሎ የፕሮቴስታንታዊ ተሐድሶ ተላላኪ አድርጎ ማቅረብ ለሕሊና የሚከብድ ድርጊት ነው፡፡ ዐፀፋው ተጋኗል፡፡ ስያሜው ጽንፍ ወጣ፡፡ 'ሀይ' የሚልም ጠፋ፡፡

[2] ኃይለማርያም ላቀው፣ ሐውልተ ስምዕ፣ገ.175



(5.1.4) 'ሀይ' የሚል የጠፋው ብዙ ጊዜ ክርክሩ በደኅናው ቀን ተነሥቶ የሚደረግ ሳይሆን የክስ ማጀቢያና ተቀጽላ ሆኖ ስለሚመጣ ጭምር ሳይሆን አይቀርም፡፡ በ1984 ዓ.ም. አቡነ መልከ ጼዴቅ በዚህ ጉዳይ ተከሰው በሲኖዶሱ ጥሪ ሲደረግ ጥንተ አብሶ ብቸኛው የክስ ምክንያት አልነበረም፡፡ ክሱ ብቻውን የቆመ አልነበረም፡፡ በክሱ አስተዳደራዊና የመንበረ ፓትርያርክ ሥልጣን ርክክቡን ተከትሎ ግለሰባዊ መነሻዎችም የተካተቱበት ይመስላል፡፡ የአባ ሠረቀ ክስ ጫፍ የደረሰው ከማኅበረ ቅዱሳን ጋር አለመግባባታቸውን ተከትሎ ነው፡፡ እዚህም ጥንተ አብሶ ብቻውን አልቆመም፡፡ አስተዳደራዊና ግለሰባዊ (ቡድናዊ) አለመግባባቶች አጅበውታል፡፡ በጣም የሚገርመው ደግሞ በጥንተ አብሶ ከመታማትም አልፈው ተከስሰው በሲኖዶስ እስከ መጠራት የደረሱት እነ አቡነ መልከ ጼዴቅ የአቡነ ጳውሎስን ኅልፈት ተከትሎ በነበረው የዕርቅ ሒደት የተሳተፉትን መጋቤ ብሉይ ሠይፈ ሥላሴ የሐንስ "በሃይማኖት ስለማይመስሉን ከእርሳቸው ጋር ለመደራደር እንቸገራለን" በማለት ቀደም ሲል መጋቤ ብሉይ ጥንተ አብሶ አለባት ብለው መጻፋቸውን ሰበብ በማድረግ ብሒሉን ለድርድሩ ማሰናከያ ለማዋል መሞከራቸው ነው፡፡ ይኼን በሐሜት ደረጃ የሰማነውን ድርጊት ጨምሮ ከላይ ያሉት ክሶች የሚጠቁሙት ጭብጡ ራሱን ችሎ ሳይሆን በተደጋጋሚ የሌሎች ክሶች ማዳመቂያ ሆኖ መቅረቡ ለማይቋጭ ክርክር መንገድ መክፈቱን ነው፡፡ ስድቡና የጸረ ማርያምነት ፍረጃው መጋነን ርእሱን ላላስፈላጊ የእልህ መቆራቆስ ዳርጎታል፡፡

(5.1.5) የዐቀባ ብሒል ደጋፊዎች ለብሒሉ መቆርቆራቸውን ለማሳየት ሲሉ የሚጠቀሙባቸው ግለ ሰብእናን የሚነኩ ጸያፍ ቃላት ደስ አያሰኙም፡፡ በተለይ ሊቀ ብርሃናት አስተርአየ ላይ የተሰነዘሩ ከአካላዊ ተፈጥሮ እስከ ትምህርት ደረጃ የደረሱ ዘለፋዎች ንግግሩን ወደ ተራ ብሽሽቅ ከማውረድ ባለፈ ሃይማኖታዊ ፋይዳቸው አይታየኝም፡፡ በአጠቃላይ ከላይ የቀረቡ ያልተገቡ የሚመስሉኝ አካሔዶች ቢታረሙ ደስታዬ ነው፡፡

## 5.2 በአንጽሖ ብሒል ደጋፊዎች የሚሰነዘሩ የማልቀበላቸው አባባሎች

(5.2.1) የአንጽሖ ብሒል ደጋፊዎችን "ፕሮቴስታንታዊ ተሐድሶ" ለማለት የሚደፍር እንደሆነ ባይኖረኝም ስልፈ ከዐቀባ ብሒል ጋር ነው። የአንጽሖን ብሒል ጸሐፊዎች እከብራለሁ፤ "ብሒላችን በኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ጸንቶ የኖረ ነው" ማለታቸውን ግን አልቀበልም።

(5.2.2) ቀደም ሲል እንዳልኩት ለአንጽሖ ብሒል የሚሟገቱ ምሁራን ቤተ ክርስቲያን ሙሉ ለሙሉ በሚባል ደረጃ በአንድም ሆነ በሌላ መልኩ የውጭ አገር ትምህርት ያገኙ ናቸው። በተለይም የግሪክና ግብጽ ተጽዕኖ ያይልባቸዋል። ችግሩ እርሱ አይደለም። (በእኔ አተያይ) ተጽዕኖውን ከነባሩ ትውፊት ለማጣጣም ሳይጥሩ ተሽቀዳድመው ይቀበሉታል። ከዚያ በኋላ ኢትዮጵያውያን ሊቃውንት የደረሷቸው መንፈሳውያን መጻሕፍትን ከብሂላቸው ለማስማማት ይደክማሉ። ይቸኩላሉ። ጥሬ ምንባባትን ብቻ ይዞ ለመከራከር ይፋጠናሉ። ይህ ሁሉ አልሆን ሲላቸው "የሃይማኖት ጉዳይ በአዋልድ አይወሰንም" የሚል የቡሩ ሜዳ አጋጣሚ ጠቅሰው ይሸሸጋሉ። እንዲያ ከተባለ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ "ጥንተ አብሶ" የሚል ቃል የለምና የእነርሱም መከራከሪያ ከጅምሩ እንደሚሸነፍ አያውቁም፤ እነርሱ ለክርክራቸው የሚያቀርቧቸው አዋልድ መሆናቸው ትዝብት ላይ እንደሚጥላቸው አለመገንዘባቸውም ይገርማል!

(5.2.3) በነባሩ የዐቀባ ብሒል ፀንቶ ከሚኖረው የካህናትና ምእመናን ኅብረት የሚደርስባቸውን ዐጸፋ ለመቋቋም በሚያደርጉት ጥረት ትርጓሜ መጻሕፍትን ከመፈተሽ ይልቅ ተከራካሪዎቻቸውን "ካቶሊካውያን፣ ቢላግዮሳውያን፣ ያልተማሩ፣ የሚያነቡትንና የሚዘምሩትን ቃል ትርጓሜ የማይረዱ፣ በልማድ የሚመሩ፣..." የማስመሰል ከባድ ስሕተት ይፈጽማሉ። በተለይ ቀሲስ አስተርአየ ወደ ታችም፣ ወደ ጎንም፣ ወደ ላይም ያለውን የእሳቸውን አሳብ ያልተቀበለ ሁሉ ለማነወር የሚጠቀሙዋቸው ቃላት ይከብዳሉ።



(5.2.4) የአቡነ ሺኖዳ የአንጽሖ ብሒል አራማጅነት በእኛ ቤተ ክርስቲያን ተቀባይነት የለውም። ኦርቶዶክሳዊ አባትነታቸውንና ወደር-አልባ የቃልና የጽሑፍ አበርክቷቸውን እያደነቅንና እያከበርን በዚህ ረገድ ትክክል አይደሉም ብለን እናምናለን። የአገራችን የአንጽሖ ብሒል አራማጆች ግን የአቡነ ሺኖዳን ተጽዕኖ ፈጣሪነትና የኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ. ከግብጽ ኮፕቲክ ቤተ ክርስቲያን ጋር ያላትን እኅታዊ ግንኙነት ለብሒሉ ተቀባይነት ማስገኛ ለማዋል ይደክማሉ። እንኳንስ ዛሬ ከግብጽ ሞግዚትነት ነጻ በወጣንበት ዘመን በመካከለኛው ዘመንና በጎንደር ዘመነ መንግሥት በነበሩ ሃይማኖታዊ ክርክሮችም የግብጽ ጳጳሳት ሥልጣን በዋናነት በጉባኤ የተረታውን ማውገዝ ብቻ ነበር። በቡሩ ሜዳ ጉባኤ ሁለት ልደት ይፋዊ ትምህርተ ሃይማኖት ሆኖ ሲደነገግ የግብጻዊ ጳጳስ ቡራኬ አላስፈለገንም። ስለሆነም ዛሬ በራሳችን እግር በቆምንበት ጊዜ ወደ ግብጽ መፋጠናቸው ድከሙ ቢላቸው ነው።

(5.2.5) የአንጽሖ ብሒል ደጋፊ ወገኖች የሚጠቀሙዋቸው መጠን የተላለፉ ምላሾች ለተሐድሶዎች መሣሪያ ሆነው ያገለግላሉ። የዐቀባ ብሒል ደጋፊዎች ይህን የተሐድሶዎች ቅሰጣ የፍረጃ ማሳመሪያ አድርገው የአንጽሖን ብሒል ተቆርቋሪዎች ለማጣጣል ይጠቀሙበታል። ይህ የሆነው በእኔ እምነት የአንጽሖ ብሒል ደጋፊ ኢትዮጵያውያን ብሂላቸው ከዐቀባ ብሒል የሚለይበትን ለማንጠር የሚያደርጉትን ጥረት ያህል ተሐድሶዎች በስርዋጽ እያመጡ ያሉትን ብሒል አለመቃወም ነው። ተሐድሶዎች "እመቤታችን ቅድመ ጸኒስ፣ ጊዜ ጸኒስና ድኅረ ጸኒስ ከጥንተ አብሶ አልነጻችም፤ ልጇ ብቻ ነጽቶ እርሷ በውርስ ኃጢአት ቆይታ አልፋለች፤" የሚል ጸያፍ ብሒል ሲያሰራጩ በጽንዓት ከመቃወም ይልቅ የዐቀባን ብሒል በማስተሐቀር ብቻ መጠመዳቸው በቀላሉ በተሐድሶነት እንዲፈረጁ በር ከፍቷል። ብሂላቸውን ከቀሳጥያን ብሒል የማስጠበቅ ግዴታን መወጣት ላይ ክፍተት አለባቸው።

በመጨረሻም፡-

እንዲህ ዓይነት ልዩነቶች ታፍነው ከሚኖሩ ይልቅ መንፈሳዊነት ባልተለየው መነጋገር እየጠበቡና እየጠሩ ሁላችንም በአንድ ልብ በመቅደሱ እንድንቆም ምኞቴ ነው። እጸልያለሁ። ቅድስተ ቅዱሳን የምንላት እመቤት እንዲያ እንዲሆን ከተወዳጅ ልጇ እንድታማልደን። የእኔ ጸሎት የተሟላ ኢትዮጵያዊ

መነሻ አለው የምለው "መንፈስ ቅዱስ ዐቀባ እምከርሠ እሟ" ብሒል ፀንቶ እንዲኖርልኝ ነው። ጸሎቴንና ጽሑፌን የእመቤታችን ጽንሰትና ብኩርና እንበለ አበሳ መሆኑን በአራንራሂ ዜማ በሚገልጸው የአባ ጊዮርጊዝ ዘጋስጫ መጽሐፈ ሰዓታት ላሳርግ።

ለጽንሰትኪ በከርሥ፣
እንበለ አበሳ ወርኩስ፣
ለተበኩርትኪ እማገዕን፣ ቅዱስ፣
ወለበዐትኪ ቤተ መቅደስ፣
ሰላም ለኪ።

::::::::: ተፈጸመ :::::::::

# ዋቢ መጻሕፍት

(የድረ ገጾችን ባሉበት - በጽሑፉ ውስጥ - ትቼ በአካል የዳሰስኳቸውንና ጎላ ያሉትን ብቻ ነው የምዘረዝረው)


ሀ. <u>በአማርኛ የተጻፉ መጻሕፍት</u>

1. ሃይማኖተ አበው፣ አቡነ ባስልዮስ ፓትርያርክ በሆኑ 9ኛው ዓመት (1960 ዓ.ም.) የታተመ።
2. መልከ ጼዴቅ (ብፁዕ:አቡነ)፣የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን እምነትና ትምህርት፣ 1994 ዓ.ም.፣ በርክሌ፣ መድኃኔ ዓለም ቤተ ክርስቲያን፣ ካሊፎርኒያ፣ አሜሪካ።
   _ ትምህርተ ክርስትና 2ኛ መጽሐፍ፣ 1984 ዓ.ም.፣ አ.አ።
3. መሐሪ ትርፌ (ሊቀ ሊቃውንት ኂላ አቡነ ጴጥሮስ)፣ የቅዱስ ጳውሎስ መጽሐፍ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ። ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት (ከአሁን በኋላ ት/ዘ/ማ/ቤት)።
   _ መጻሕፍተ ሐዲሳት ሠለስቱ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1989 ዓ.ም.፣ አ.አ፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
4. መርስዔ ኀዘን ወልደ ቂርቆስ፣ መጻሕፍተ ሰሎሞን ወሲራክ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
   _ ትዝታዬ፡ ስለራሴ የማስታውሰው፣ 2002 ዓ.ም.፣ አስቴር ነጋ አሳታሚ ድርጅት፣ ሮኆቦት አታሚዎች።
5. መጽሐፈ ቅዳሴ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1988 ዓ.ም.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
6. መጽሐፈ ግብረ ሕማማት፣ በግእዝና በአማርኛ፣ 2005 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
7. መጽሐፍ ቅዱስ፣ የብሉይና የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት፣ 1980 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ብ/ሰ/ማ/ድ።
8. መጽሐፈ ድጓ፣ 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
9. መጻሕፍተ ብሉያት ክልኤቱ፣ እሉ እሙንቱ አሪት ዘልደት አሪት ዘጸአት፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1999 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።
10. ሞገስ ዕቁበ ጊዮርጊስ (ሊቀ መዘምራን)፣ መርሐ ጽድቅ ባሕለ ሃይማኖት፣ 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።

11. ሠረቀ ብርሃን ወልደ ሳሙኤል (አባ)፣ እውነትና ንጋት፣ 2004 ዓ.ም.፣ ሜጋ ማተሚያ ቤት።
12. ሠናየ ምክር (አባ)፣ መጽሐፈ አክሲማርስ፣ 1999 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ባሕር ዳር።
13. ሰይፈሥላሴ ዮሐንስ (መጋቤ ብሉይ)፣ መሠረተ ሃይማኖትና የካህናት ተልእኮ፣ 1982 ዓ.ም.።
14. ስምረት አያሌው (ወ/ሮ)፣ አባቴና እምነቱ፡ የአለቃ አያሌው ታምሩ የሕይወት ታሪክ፣ 2007 ዓ.ም.፣ ዕሌኒ ማተሚያ ቤት።
15. በላይ ዘገየ (ሊቀ ኅሩያን)፣ የቅኔዋ ንግሥት፣ 2006 ዓ.ም.፣ አፍሪካ አታሚዎች።
16. ብርሃኑ ጎበና (ዲያቆን)፣ ዓምደ ሃይማኖት፣ 1992 ዓ.ም.።
17. ኃይለ ማርያም ላቀው (መምህር)፣ ሐውልተ ስምዕ፣ 2004 ዓ.ም.፣ አሳታሚ ማኅበረቅዱሳን።
18. ተአምረ ማርያም፣ 1987 ዓ.ም.፣ ተስፋ ገብረ ሥላሴ ማተሚያ ድርጅት።
19. ታመነ አበበ (መጋቤ ሐዲስ)፣ የዘወትር ጸሎት ትርጓሜ፣ 2000 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ዕሌኒ ማ/ቤት።
20. ቴዎፍሎስ (ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ)፣ መዝሙረ ዳዊት፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997 ዓ.ም.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
21. አበራ በቀለ (ሊቀ ጉባኤ አባ)፣ ትምህርተ ሃይማኖትና ክርስቲያናዊ ሕይወት፣ 2008 ዓ.ም.፣ 2ኛ እትም፣ ጃጃው አታሚዎች።
22. አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ (ትርጉም በመ/ር ኅሩይ ኤርምያስ)፣ መጽሐፈ ምሥጢር፣ 2001 ዓ.ም.፣ በአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫና አባ በጸሎተ ሚካኤል አንድነት ገዳም።
23. አድማሱ ጀንበሬ (መልአከ ብርሃን)፣ መድሎተ አሚን፣ ዓመተ ምሕረቱንና ማ/ቤቱን ማወቅ አልቻልኩም።
_ ኵሉሔ ሃይማኖት፣ 1949 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
24. አያሌው ታምሩ (ሊቀ ጠበብት)፣ የኢትዮጵያ እምነት በሦስቱ ሕግጋት፣ 1953 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ብርሃንና ሰላም ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ማተሚያ ቤት።
_ ወላዲተ አምላክ በኢትዮጵያ፣ 1978 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።





_ ምልጃ፣ ዕርቅና ሰላም፣ 1992 ዓ.ም፣ ዲማ።
25. አፈወርቅ ዘውዴ (አለቃ)፣ የግእዝ ቅኔያት የሥነ ጥበብ ቅርስ-2፣ 1980 ዓ.ም.፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት።
26. እሸቱ ታደሰ (ዲያቆን)ና ደጀኔ ሽፈራው (ዲያቆን)፣ ወላዲተ አምላክ በመጽሐፍ ቅዱስ፣ 1987 ዓ.ም.።
27. ኪዳነ ወልድ ክፍሌ (አለቃ)፣ መጽሐፈ ሕዝቅኤል፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
_ መጽሐፈ ሰዋስው ወግስ፣ 1948 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት፣ አሳታሚ ደስታ ተክለወልድ።
28. ወንጌል ቅዱስ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997 ዓ.ም.፣ አ.አ.።
29. ውዳሴ ማርያምና ቅዳሴ ማርያም፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1990 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
30. ዓለማየሁ ሞገስ፣ ሁሉም ሁሉን ይወቅ፣ 1987 ዓ.ም.።
31. ዓሥራት ገብረ ማርያም፣ትምህርተ መለኮት፣ 1983 ዓ.ም. እና 1991 ዓ.ም. (2ኛ እትም)።
32. ዘለዓለም እሰይ (መልአከ ገነት)፣ የጸሎተ ሃይማኖት ትርጓሜ። 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ አልፋ አታሚዎች።
33. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተክርስቲያን እምነት፣ ሥርዓተ አምልኮና የውጭ ግንኙነት፣ 1988 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
34. የመጽሐፍ ቅዱስ መዝገበ ቃላት (የኢትዮጵያ መጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር)፣ 6ኛ እትም፣ 1992 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ባናዊ ማተሚያ ቤት።
35. የኢፌዲሪ የወንጀል ሕግ፣ 1996 ዓ.ም.፣ ብ/ሰ/ማ/ድ።
36. የፌደራል ታራሚዎች አያያዝ ደንብ ቍጥር 138/1999፣ ብ/ሰ/ማ/ድ።
37. ዳንኤልና 12ቱ ደቂቅ ነቢያት፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1998 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
38. ድርሳነ ዘዮሐንስ አፈወርቅ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1987 ዓ.ም.፣ ተስፋ ገብረ ሥላሴ ማተሚያ ቤት።
39. ጌራወርቅ ጥበቡ (መጋቤ ምሥጢር)፣ መጽሐፈ ኢሳይያስ፣ ንባቡና ትርጓሜው፣ 1997 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ክ/ማ/ቤት።
40. ግርማ ርእዮቱ (ሊቀ ጉባኤ፡ አባ)፣ ታአዶክስ፣ 2003 ዓ.ም.።

41. ጎርጎርዮስ (ብፁዕ አቡነ፣ሊቀ ጳጳስ ዘሸዋ)፣ የቤተክርስቲያን ታሪክ በዓለም መድረክ፣ 1978 ዓ.ም.፣ አ.አ.፣ ት/ዘ/ማ/ቤት።

ለ. መጽሔቶች

1. ሠይፈ ሥላሴ ዮሐንስ (መጋቤ ብሉይ)፣ 1971 ዓ.ም.፣ "ምልዕተ ጸጋ ማርያም"፣ ትንሣኤ፣ ቊጥር 23።
2. ብርሃኑ አድማስ (ዲያቆን)፣ 2001 ዓ.ም.፣ "ሠርግን ከዐርባ ጋር ያዛመደው ምንድን ነው?"፣ ሐመር፣ 16ኛ ዓመት፣ ቊጥር 5፣ ገ.27-28።
3. ዳንኤል ዓለሙ (መምህር)፣ 1985 ዓ.ም.፣ "ንጽሕት በድንግልና"፣ ማዕዶት፣ መስከረም፣ ቁ.38።

ሐ. የእንግሊዝኛ ማጣቀሻዎች

1. Aba Paulos, Filsata: The Feast of the Assumption of the Virgin Mary and the Mariological tradition of the Ethiopian Orthodox Tewahido Church, 1988, unpublished, Princeton Theological Seminary
2. Encyclopedia Aethiopica, Volume 3, 2007.
3. Tsehai Wada; Abortion Law in Ethiopia: Mizan Law Review: vol. 2. No.1, Jan 2008: p. 8
4. H.H.Pope Shenouda III, "What is Man?", 2nd print, June, 2004, Egyptian Printing.

አንድ ሰው ታሪክንና ሃይማኖትን በአንድ መንገድ መረዳት ይችላል የሚል እምነት የለኝም፡፡ አተረጓጎሙ ትልቅ ጥንቃቄ የሚጠይቅና ይልቁንም በሚጠናበት ዘመን ባለው ማኅበራዊ መቼት እንዳይዛባ መጠንቀቅ ትልቁ ኃላፊነት መሆኑ እንደ ተጠበቀ ሆኖ በአዘጋገቡ ያጋጠመውን ችግር በየጊዜው በሚደረጉ ምርምሮችና በተገኙት ተጨባጭ ማስረጃዎች መሠረት ማስተካከል ይችላል፡፡ በአንጻሩ እውነተኛው ሃይማኖት ከእግዚአብሔር የተገለጠ በመሆኑ መሠረታዊ አስተምህሮው ላይ ሊደረግ የሚችል መሻሻልና ለውጥ ፈጽሞ አይስማማውም፡፡ ሆኖም በታሪክ ሒደት የቃላት ውክልናና የመልእክት አተረጓጎም እየተለወጠ ሲሔድ ያንን ተከትሎ የሃይማኖታዊ አስተምህሮ ለውጥ እንዳይመጣ ነቅቶ ተግቶ መጠበቅና ማስተማር የሃይማኖት መምህራን ቀዳሚ ተግባር ነው፡፡ ነገር ግን በዘመናት ውስጥ ሰዎች ለታሪክ ሊደረግ የሚገባውን ለሃይማኖት፤ ለሃይማኖት ሊደረግ የሚገባውን ደግሞ ለታሪክ እያገለባበጡ ታሪካዊ እውነት ለመሰላቸው አምነው ሲሞቱለት ሃይማኖቱን ደግሞ በመረዳታቸው መጠን ብቻ ሲተቹትና በደረሱበት እሳቤ መጠን እንደ ገና ሠርተው ሊያሳምኑበት ሲሞክሩ ማየቱ የተለመደ ነገር ከሆነ የሰነባበተ ይመስላል፡፡

በእኛ ሀገርም በእነዚህ በሁለቱም ዘውጎች ላይ በተደጋጋሚ የተከሰቱ ችግሮች እንዳሉ ለመረዳት አይቸግርም፡፡ ለማረጋገጥ የፈለገ ሰው ደግሞ ይህን መጽሐፍ ማንበብ ሊበቃው ይችላል፡፡ በእኛ ሀገር ታሪካዊ አዘጋገቡም ሆነ አተረጓጎሙ እንደ ሃይማኖት ከሚያወዛግቡ ኩነቶች ውስጥ የደቂቀ እስጢፋኖስ ነገር ሊጠቀስ ይችላል፡፡ ሃይማኖታዊ ጉዳዮች ሆነው በዘመናችን ሰዎች ዕውቀት ልክ ሊሠሩና ሊለወጡ ከሚታማባቸው ሃይማኖታዊ ጉዳዮች መካከል ደግሞ ከጥንተ አብሶ አንጻር እመቤታችንን አስመልክቶ የሚካሔደው ተዋሥኦ ሊጠቀስ የሚችል ይመስለኛል፡፡ የዚህ መጽሐፍ "ወልታ ጽድቅ" አዘጋጅ (በብዕር ስሙ በአማን ነጸረ) ደግሞ ከይዘት አንጻር የሚራራቁ የሚመስሉ ነገር ግን ከላይ ከጠቀስኩት እሳቤና ሁለቱም እመቤታችንን ማዕከል ከማድረጋቸውም አንጻር የሚገናኙትን እነዚህን ሁለት ጉዳዮች እንደ ብልህ ገበሬ አንድ ላይ ጠምዶ አቅርቦልናል፡፡ ምንም እንኳ ሁለቱም ጉዳዮች በየራሳቸው ገና ብዙ ሊጠኑ፣ ሊጻፍባቸውና ሊብራሩ የሚችሉ ቢሆኑም በእኔ ንባብ መሠረት ከሆነ ለዘመኑ ትውልድ በጥሩና በተሻለ መንገድ ሲቀርቡ "ወልታ ጽድቅ" የመጀመሪያ መጽሐፍ ይመስለኛል፡፡ በእኔ እምነት በአማን በእነዚህ ሁለት እጅግ አስፈላጊ ጉዳዮች ላይ ከአቀራረቡ ጀምሮ አዳዲስ ነገሮችን ይዞ ብቅ ብሏል፡፡ ስለዚህም በጉዳዩ ላይ ማወቅ፣ ማጥናት፣ መመራመር፣ መሞገት፣ መረዳትና መጻፍ ብቻ ሳይሆን መታዘብ የሚፈልግ እንኳ ቢሆን ወልታ ጽድቅን እንዲያነብብ በልበ ሙሉነት እጠቁመዋለሁ፡፡ ታሪካዊ ግንዛቤን እንደ እምነት ፤ እምነትን እንደ ዐለማዊ ዕውቀት ይዞ ነገር ለተገላበጠበትም ወደ ፍጹሙ መድኃኒትና ድኅነት የምታደርሰው የሥቃይ ማስታገሻ (anti pain) ልትሆንለት የምትችል ምርጥ ቅመማ ናት፤ ወልታ ጽድቅ፡፡

ብርሃኑ አድማስ (ዲ/ን፤ በሥነ ድርሣን ሁለተኛ ዲግሪ)

ኅትመት ፋር ኢስት ትሬዲንግ ኃላ.የተ.የግ.ማኅበር
011 156 53 52

ዋጋ 70 ብር